# ፍትሐ ነገሥት
# ንባቡና ትርጓሜው



ብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ጳውሎስ
ፓትርያርክ ርዕሰ ሊቃነ ጳጳሳት ዘኢትዮጵያ
ወዕጨጌ ዘመንበረ ተክለሃይማኖት በሆኑ
በ፭ኛው ዓመት ለ፭ኛ ጊዜ ታተመ ።

**አሳታሚ**
ትንሣኤ የመጻሕፍት ማሳተሚያ ድርጅት
አዲስ አበባ ፲፱፻፺ ዓ·ም



ብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ጳውሎስ ፓትርያርክ ርእሰ ሊቃነጳጳሳት ዘኢትዮጵያ
ወእጨጌ ዘመንበረ ተክለሃይማኖት

መግቢያ፡—

ፍትሐ ነገሥት የሚው ቃል "ፍትሕ እና ነገሥት" በሚሉት ሁለት ቃላት የተሰናሰለ ወይም የተያያዘ ቃል ነው ። ትርጓሜውም ፍርድ ፤ ውሳኔን መስጠት፣ ሕግና ሥርዓትን ማስፈን ማለት ሲሆን ነገሥታቱ ክርስቲያኖች ከመሆናቸው ጋር ሥጋዊውንም ሆነ መንፈሳዊውን ፍትሕ ይመለከቱ ስለነበር በነገሥታቱ ስም "ፍትሐ ነገሥት" ተብሎ ተሰይሞአል ። ኢትዮጵያ አገራችን በጽሑፍ ከአሉዋት ጥንታውያን የሕግ መጻሕፍት መካከል ታላቁና የታወቀው ፍትሐ ነገሥት የተባለው መጽሐፍ ነው ።

ፍትሐ ነገሥት ከዓረብኛ ወደ ግእዝ የተተረጐመውና በሥራ ላይ የዋለው በንጉሠ ነገሥቱ አፄ ዘርዐያቆብ (ከ1444 እስከ 1468) ዓ.ም እንደሆነ ይታወቃል ። ከዚህም ጋር ይህ የሕግና የሥርዓት መጽሐፍ በመላ ኢትዮጵያ ተዳርሶ ሊቃውንቱ እየተማሩትና እያስተማሩት በሕግ ሸንጐ ላይ ሊውል ችሎአል ። ሊቃውንቱ ለአያሌ ዘመናት በብራና ብቻ በእጅ እየጻፉ ፤ በጉባዔ እየተረጐሙ ትምህርቱ ከአንዱ ወደ አንዱ በቃል እየተላለፈ በኢትዮጵያም የሕግ ቀዋሚ የፍርድ መጽሐፍ ሆኖ አገልግሎአል ። በተለይ ይህን መጽሐፍ ለሚያውቁ የሕግ ሊቃውንት ሁሉ ከፍተኛ የሕግ አዋቂነት የመዓርግ ስም ይሰጣቸው ነበር ። የፍትሐ ነገሥት መጽሐፍ በሀገራችን ሥርወ ሕግ ሁኖ ብዙ ዘመን የተሠራበት ከመሆኑ ጋር አሁንም የሕግ ምንጭነቱን እንደያዘ ይገኛል ።

በመሠረቱ ፍትሐ ነገሥት ፍትሕ መንፈሳዊና ፍትሕ ሥጋዊ ፤ ተብሎ በሁለት ዐበይት ክፍሎች የተከፈለ ነው ። በ1948 ዓ.ም የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ተረቆ በአዋጅ በሥራ ላይ ከመዋሉ በፊት በኢትዮጵያችን ይሠራበት የነበረው ሕግ ፍትሐ ነገሥት እንደነበር ግልጽ ነው ። መንፈሳዊ ሕግነቱም አሁንም በሥራ ላይ እንደዋለ ነው። በመሆኑም

1ኛ/ በ1956 ዓ.ም በግዕዝ ብቻ

2ኛ/ በ1958 ዓ.ም ንባብና ትርጓሜው

3ኛ/ በ1961 ዓ.ም በእንግሊዝኛ

4ኛ/ መጽሐፈ ሕግጋት ዐበይት በሚል ስያሜ በ1962 ዓ.ም በግእዝና በአማርኛ ታትሞ በሥራ ላይ ውሎአል ። ሆኖም የመጽሐፉ አገልግሎት እጅግ በጣም አስፈላጊ በመሆኑና ቀደም ሲል የታተመው ተሠራጭቶ በማለቁና የምእመናኑም ፍላጐትና ጥያቄ በርካታ በመሆኑ ብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ጳውሎስ፣ ፓትርያርክ ፤ ርዕሰ ሊቃነ ጳጳሳት ዘኢትዮጵያ ወእጨጌ ዘመንበረ ተክለ ሃይማኖት በሆኑ በ፲ኛው ዓመት እነሆ በግእዝና በአማርኛ ለ5ኛ ጊዜ አሳትመን ማቅረባችንን ስናበስር መንፈሳዊ ደስታ ይሰመናል ።

"ወስብሐት ለእግዚአብሔር"

ማሳተሚያ ድርጅቱ

fteha/04

# ማ ው ጫ

ገጽ

## እንቀጽ ፡ ቀዳማዊ ።



## ክፍል ፡ ዳግማዊ ።

በእንተ ፡ ግብራት ፡ ዓለማውያት ፡ ዘምግብና ፡



## መጀመሪያ ፡ አንቀጽ ።



## ሁለተኛ ፡ ክፍል ።

ስለ ፡ ዓለማውያን ፡ ሥራና ፡ አስተዳደር ፡

በስመ ፡ አብ ፡ ወወልድ ፡ ወመንፈስ ቅዱስ ፡ አሐዱ ፡ አምላክ ፡ ንዌጥን ፡ በረድኤተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወሥነ ፡ ሠርሖቱ ፡ በጽሒፈ ፡ መቅድመ ፡ ጉባኤ ፡ ዘአስተጋብእዎ ፡ ሊቃውንት ፡ ጸሎቶሙ ፡ ወበረከቶሙ ፡ ወሀብተ ፡ ረድኤቶሙ ፡ የሀሉ ፡ ምስለ ፡ ኵሎሙ ፡ ክርስቲያን ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፡ አሜን ።

በአብ ፡ በወልድ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ስም ፡ ፩ ፡ አምላክ ፡ ሊቃውንት ፡ የሰበሰቡትን ፡ የዚህን ፡ መጽሐፍ ፡ መቅድም ፡ መጻፍን ፡ በእግዚአብሔር ፡ አጋዥነትና ፡ በማቅናቱ ፡ መበጀት ፡ እንጀምራለን ። ጸሎታቸውና ፡ በረከታቸው ፡ የረድኤታቸውም ፡ ሀብት ፡ ከክርስቲያኖች ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ይኑር ፡ አሜን ።





ወእምድኅረ ፡ ኀልቀ ፡ ዓመተ ፡ ሰማዕታት ፡ ሰበ ፡ ረሰይዎ ፡ ንጉሠ ፡ ፫፻፲ቱ ፡ ወ፰ቱ ፡ ርቱዓነ ፡ ሃይማኖት ፡ ለቈስጠንጢኖስ ፡ ውእቱሂ ፡ ይቤሎሙ ፡ እንስ ፡ ኢይፈቅድ ፡ መንግሥተ ፡ እስመ ፡ ፍኖተ ፡ ክርስቶስ ፡ ወፍኖተ ፡ ዓለም ፡ ካልእ ፡ ውእቱ ። ወፍኖቱስ ፡ ለክርስቶስ ፡ ወትእዛዙ ፡ ጥይቅት ፡ "ትቤ ፡ አፍቅሩ ፡ ጸላእተክሙ ፡ ወሠናየ ፡ ግበሩ ፡ ለእለ ፡ ይትዔገሉክሙ" ዘንተ ፡ ወዘይመስሎ ። እስመ ፡ ዛቲ ፡ ትእዛዝ ፡ ሕገ ፡ ትሩፋት ፡ ይእቲ ፡ ዳግሚት ፡ ትኤዝዝ ፡ ከመ ፡ ይትዓገሡ ፡ ወከመ ፡ ይፁሩ ፡ ወይሥረዩ ፡ ወያናሕስዩ ፡ ወያሠንዩ ፡ ለውሉደ ፡ ቢጽ ፡ ወያስተዓርይዎሙ ፡ በነፍስሙ ። እሮ ፡ ይትከሀለኒ ፡ ከመ ፡ እዕርዕ ፡ ዘንተ ፡ ትእዛዘ ፡ ወከመ ፡ እእዝዝ ፡ ኵነኔ ፡ ወፈድየ ፡ ዕዳ ፡ በጊዜሁ ፡ ዘእንበለ ፡ ምሕረት ፡ ወተበቅሎ ፡ ለግፉዕ ፡ እምነ ፡ ገፋዒሁ ። እስመ ፡ ኵሉ ፡ ዘፍጹም ፡ ይደሉ ፡ በግብር ፡ ከመ ፡ ይሥዐሮ ፡ ለዘየሐጽጽ ፡ ወበእንተዝ ፡ ሠዐረቶ ፡ ሕገ ፡ እግዚእነ ፡ ለዘይቀድም ፡ እምኔሃ ። ለዛቲስ ፡ ኢይደሉ ፡ ተሥዕሮታ ፡ እስመ ፡ አልቦ ፡ ዘይከብር ፡ እምኔሃ ። ለሊሃ ፡ ሕገ ፡ ፍጻሜ ፡ ወማኅለቅት ። እስመ ፡ አልቦ ፡ ዘይከብር ፡ እምፍኖተ ፡ ምሒር ፡ ወእሠንዮ ፡ ወጸዊረ ፡ ትዕግሥት ።

የሰማዕታት ፡ ዘመን ፡ ከተፈጸመ ፡ በኋላ ፡ ሃይማኖታቸው ፡ የቀና ፡ ፫፻፲፰ ፡ ሊቃውንት ፡ ቆስጠንጢኖስን ፡ ንጉሥ ፡ ባደረጉት ፡ ጊዜ ፡ እርሱ ፡ እኔ ፡ መንግሥትን ፡ አልሻም ፡ አላቸው ። የክርስቶስ ፡ መንገድና ፡ የዓለም ፡ መንገድ ፡ ልዩ ፡ ነውና ። የክርስቶስ ፡ መንገድና ፡ የተረጋገጠች ፡ ትእዛዙ ፡ ግን ፡ ጠላቶቻችሁን ፡ ውደዱ ፡ ለሚቀሙዋችሁም ፡ በጎ ፡ አድርጉ ፡ (ማቴ ፡ ፭ ፡ ፵፩-፵፬ ። ሉቃ ፡ ፮ ፡ ፳፯-፴፭ ።) ይህንና ፡ የሚመስለውን ፡ ትላለችና ። ይህች ፡ ትእዛዝ ፡ የትሩፋት ፡ ሕግ ፡ ናትና ። ሁለተኛም ፡ እንዲታገሡ ፡ እንዲሸከሙ ፡ ይቅር ፡ እንዲሉ ፡ እንዲያቃልሉ ፡ ለባልንጀሮቻቸውም ፡ ልጆች ፡ መልካም ፡ እንዲያደርጉ ፡ ከሰውነታቸውም ፡ ጋር ፡ እንዲያስተካክሏቸው ፡ (ሉቃ ፡ ፫ ፡ ፲፩ ።) ታዝዛለች ። ይህን ፡ ትእዛዝ ፡ እተው ፡ ዘንድ ፡ ፍርድንና ፡ ያለ ፡ ምሕረት ፡ በጊዜው ፡ ዕዳ ፡ መክፈልን ፡ እዝዝ ፡ ዘንድ ፡ ለተበደለውም ፡ ከበዳዩ ፡ መበቀልን ፡ እዝዝ ፡ ዘንድ ፡ እንዴት ፡ ይቻለኛል ። በሥራ ፡ ፍጹም ፡ የሆነው ፡ ሁሉ ፡ ጐደሎውን ፡ ሊሽረው ፡ ይገባልና ። ስለዚህም ፡ የጌታችን ፡ ሕግ ፡ ከእርስዋ ፡ የሚቀድመውን ፡ ሻረችው ። እርስዋ ፡ ግን ፡ መሻር ፡ አይገባትም ። ከእርስዋ ፡ የሚበልጥ ፡ የለምና ፡ እሷ ፡ የፍጹምነትና ፡ የመጨረሻ ፡ ሕግ ፡ ናት ፡ ከርኅርኄና ፡ መልካም ፡ ከማድረግ ፡ ትዕግሥትንም ፡ ከመያዝ ፡ የበለጠ ፡ ሕግ ፡ የለምና ።

እሜሃ ፡ ሰበ ፡ ሰምዑ ፡ ተሠጥዎተ ፡ ቃሉ ፡ ለቈስጠንጢኖስ ፡ ፫፻፲ቱ ፡ ወ፰ቱ ፡ ሊቃናት ፡ ጸለዩ ፡ ጸሎተ ፡ ኀበ ፡ እግዚእነ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ሎቱ ፡ ስብሐት ፡ እንዘ ፡ ይብሉ ፡ እግዚኦ ፡ አልቦ ፡ ጥንት ፡ ለቅድምናከ ፡ ወለድኅርናከ ፡ አልቦ ፡ ፍጻሜ ፡ እስመ ፡ አንተ ፡ ልዑል ፡ እምነ ፡ መልዕልት ፡ ወአልቦ ፡ መሠረት ፡ ለዕመቅከ ፡ ወአልቦ ፡ ኑኅ ፡ ወግድም ፡ ለመለኮትከ ፡ መንግሥትከኒ ፡ መንግ

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ የቈስጠንጢኖስን ፡ የቃሉን ፡ መልስ ፡ ስምተው ፡ ፫፻፲፰ቱ ፡ ሊቃውንት ፡ ክብር ፡ ይግባውና ፡ ወደ ፡ ጌታችን ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ እንዲህ ፡ እያሉ ፡ ጸሎትን ፡ ጸለዩ ። "አቤቱ ፡ ለቀዳሚነትህ ፡ ጥንት ፡ ለኋለኛነትህም ፡ ፍጻሜ ፡ የለውም ፡ አንተ ፡ ከከፍተኞች ፡ በላይ ፡ ከፍተኛ ፡ ነህና ፡ ለጥልቅነትህ ፡ መሠረት ፡ የለውምና ፡ ለግዛትህም ፡ ወርድ ፡ ቁመት ፡ የለውምና ።

### መቅድም

ሐዋርያት ፡ በ፴ትእዛዝ ፡ እምቀኖናት ፡ ዘኍልቆሙ ፡ ፹ወ፩ ፡ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ዘአሕጸጽነ ፡ ንሕነ ፡ ምንተኒ ፡ እምነ ፡ ግብር ፡ ፍትሐ ፡ አንትሙ ፡ በዘይደሉ ፡ እበመ ፡ ብነ ፡ ለኵልነ ፡ መንፈሰ ፡ እግዚአብሔር ። ወብሂሎቶሙ ፡ በውስተ ፡ ቀኖናት ፡ ዘ፴ወ፩ ፡ ትእዛዝ ፡ እምኔሃ ፡ ወለእመ ፡ ተርፈ ፡ እምኔነ ፡ ምንትኒ ፡ ያዘክር ፡ ኤጲስቆጶስ ። ወዓዲ ፡ ሀሎ ፡ በውስተ ፡ ቀኖና ፡ ዘ፵ወ፮ ፡ እምኔሃ ፡ ወለእመ ፡ ተርፈ ፡ እምኔነ ፡ ምንትኒ ፡ አፍቁራን ፡ ለዝንቱሂ ፡ ይከሥቶ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለዘኮነ ፡ ድልወ ፡ ወትትመራሕ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በዘይደሉ ፡ ኀበ ፡ መርሶ ፡ ወዛኅን ።

ወዓዲ ፡ ይቤሉ ፡ ለኤጲስቆጶሳት ፡ በዲድስቅልያ ፡ ፩ቱ ፡ እስመ ፡ ለክሙኒ ፡ ይቤለክሙ ፡ እግዚእነ ፡ "ዘአሰርክሙ ፡ በምድር ፡ ይኩን ፡ እሱረ ፡ በሰማያት ፡ ወዘፈታሕክሙ ፡ በምድር ፡ ይኩን ፡ ፍቱሐ ፡ በሰማያት" ። ወፍትሐ ፡ በሥልጣን ፡ ከመ ፡ እምላክ ።

ወለእመኒ ፡ ፈትሐ ፡ በእንተ ፡ ንስሓሆሙ ፡ ለኃጥአን ፡ በአዝማን ፡ ነዋኅ ፡ አበውሐ ፡ ለሊቃውንት ፡ አቅልሎታ ፡ ወአጽንዖታ ፡ በእምጣነ ፡ ይሬእይዎ ፡ ለተውላጠ ፡ ግብሮሙ ። ወጥንትሰ ፡ ዘይገብሩ ፡ ቦቱ ፡ በዝንቱ ፡ ፍካሬ ፡ ኮለንታሁ ፡ ቃለ ፡ እግዚእነ ፡ ውእቱ ፡ ሎቱ ፡ ስብሐት ፡ ዘይቤሎሙ ፡ ለአርዳኢሁ ፡ "ሑሩ ፡ ወመሀሩ ፡ ኵሎ ፡ አሕዛበ ፡ ወአጥምቅዎሙ ፡ በስመ ፡ አብ ፡ ወወልድ ፡ ወመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ወመሀርዎሙ ፡ ይዕቀቡ ፡ ኵሎ ፡ ዘአዘዝኩክሙ ፡ ወአነ ፡ እሄሉ ፡ ምስሌክሙ ፡ እስከ ፡ ኅልቀተ ፡ ዓለም" ። ወጥዩቅ ፡ ውእቱ ፡ ከመ ፡ እሙንቱ ፡ ኢይሄልዉ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ፡ ወዕዉቅ ፡ እንከ ፡ ከመ ፡ ለሊሁ ፡ አመረ ፡ በዝንቱ ፡ ቃል ፡ በእንተ ፡ እለ ፡ ይመጽኡ ፡ ድኅሬሆሙ ፡ ወይሠየሙ ፡ ለምሀሮ ፡ ህየንቴሆሙ ። ወያስተጸንዕ ፡ ዘንተ ፡ በብሂሎቱ ፡ ሎሙ ፡ ወዘእብሎ ፡ ለክሙ ፡ እብል ፡ ለኵሉ ። ወበእንተ ፡ ዝንቱ ፡ ኮነት ፡ ውክፍት ፡ ቀኖና ፡ ማኅበር ፡ ቅድበት ፡ ወሊቃውንት ፡ ቅዱሳን ፡ ማእምራን ፡ ዘከመ ፡ አቡሊድስ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ዘሮሜ ፡ ወባስልዮስ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ዘቂሳርያ ፡ ወእለ ፡ ይመስልዎሙ ፡ እምሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ ዘእለ ፡ እስክንድርያ ።

መዕበስ ፡ ኮነ ፡ ፈቂድ ፡ ኀበ ፡ ሰቢክ ፡ ወፈንዎተ ፡ ሐዋርያት ፡ ውእቱ ፡ አስተሐምሞ ፡ ቡብከት ፡ ባሕቲቱ ። በከመ ፡ ይቤ ፡ ጳውሎስ ፡ ሐዋርያ ። ወበብከትስ ፡ ሕጹር ፡ በእንተ ፡ ሃይማኖት ፡ ወትእዛዘ ፡ ሕይወትሰ ፡ ትሄሉ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ። ኅደጉ ፡ ሰባክያን ፡ ፈሊጠ ፡ ምግባራት ፡

### መቅድም

ቍጥራቸው ፡ ፹፩ ፡ ከሆኑት ፡ ቀኖናት ፡ ውስጥ ፡ በ፴ኛው ትእዛዝ ፡ እንዲህ ፡ እንዳሉ ፡ እኛ ፡ ከሥራ ፡ ማናቸውንም ፡ የአጐደልነ ፡ ብንሆን ፡ እናንተ ፡ በሚገባ ፡ አሟሉት ። ለሁላችንም ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ አለንና ። በቀኖናት ፡ ውስጥ ፡ በ፴፩ኛው ፡ ትእዛዝ ፡ ከእኛ ፡ የቀረ ፡ አንዳች ፡ ነገር ፡ ቢኖር ፡ ኤጲስቆጶሱ ፡ ያሳስብ ፡ ማለታቸውም ፡ ይህንኑ ፡ ያስረዳል ። ዳግመኛም ፡ በቀኖናው ፡ ውስጥ ፡ በ፵፮ኛው ፡ ላይ ፡ ወንድሞች ፡ ሆይ ፡ ከእኛ ፡ የቀረ ፡ ምንም ፡ ቢኖር ፡ እግዚአብሔር ፡ ለተገባው ፡ ሰው ፡ ይገልጠው ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንም ፡ ጸጥታ ፡ ወዳለው ፡ ወደብ ፡ ትመራ ፡ የሚል ፡ አለ ።

ዳግመኛም ፡ ለኤጲስቆጶሳት ፡ በዲድስቅልያ ፡ በ፩ኛው ፡ ክፍል ፡ እናንተንም ፡ እኮ ፡ ጌታችን ፡ በምድር ፡ ያሠራችሁት ፡ በሰማይ ፡ የታሠረ ፡ ይሁን ፡ በምድር ፡ የፈታችሁትም ፡ በሰማይ ፡ የተፈታ ፡ ይሁን ፡ እንደ ፡ እምላክም ፡ በሥልጣን ፡ ፍረዱ ፡ ብሏችኋል ፡ አሉ ። (ማቴ ፡ ፲፰ ፡ ፲፰) ።

በለ ፡ ኃጥአን ፡ በንስሐ ፡ መመለስ ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ቢፈርዱ ፡ የሥራቸውን ፡ ለውጥ ፡ በሚያዩዋት ፡ መጠን ፡ ማጽናናትንና ፡ ማቅለልን ፡ ለሊቃውንት ፡ ፈቅደዋል ። ይህን ፡ ትርጓሜ ፡ የሚያደርጉበትም ፡ ጥንተ ፡ ነገር ፡ ምስጋና ፡ ይግባውና ፡ ሁለንተናው ፡ የጌታችን ፡ ቃል ፡ ነው ። ሂዱ ፡ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡ አስተምሩ ፡ በአብ ፡ በወልድ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ስም ፡ አጥምቋቸው ፡ ያዘዝኋችሁንም ሁሉ ፡ እንዲጠብቁ ፡ አስተምሩአቸው ፡ እኔም ፡ እስከ ፡ ዓለም ፡ ፍጻሜ ፡ ድረስ ፡ ከእናንተ ፡ ጋር ፡ እኖራለሁ ፡ ያላቸው ፡ ቃል ፡ ነው ። (ማቴ ፡ ፳፰ ፡ ፲፱-፳) ። እነርሱ ፡ እስከ ፡ ዓለም ፡ ፍጻሜ ፡ ድረስ ፡ እንዳይኖሩ ፡ የተረዳ ፡ ነው ። በዚህ ፡ ቃል ፡ ከእነርሱ ፡ በኋላ ፡ ስለሚመጡትና ፡ በማስተማርም ፡ በእነርሱ ፡ ፈንታ ፡ ስለሚሾሙት ፡ የተናገረ ፡ መሆኑን ፡ እርሱ ፡ እንዳስረዳ ፡ የታወቀ ፡ ነው ። ለእናንተ ፡ የምለውን ፡ ለሁሉ ፡ እላለሁ ፡ (ማር ፡ ፲፫ ፡ ፴፯) በማለቱ ፡ ይህን ፡ ያጸናል ። ስለዚህም ፡ የተቀደሰችው ፡ ማኅበርና ፡ ቅዱሳን ፡ ማእምራን ፡ የሆኑ ፡ የሊቃውንቱ ፡ ቀኖና ፡ ተቀባይነትን ፡ ያገኘች ፡ ሆነች ። እኒሁም ፡ እንደ ፡ ሮሜ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ እንደ ፡ አቡሊዲስና ፡ እንደ ፡ ቂሳርያው ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ እንደ ፡ ባስልዮስ ፡ ከእስክንድርያ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳትም ፡ እነርሱን ፡ እንደሚመስሉት ፡ ያሉት ፡ ናቸው ።

ፈቃድ ፡ ወንጌልን ፡ ለመስበክና ፡ ሐዋርያትን ፡ ለመላክ ፡ ከሆነስ ፡ ለስብከት ፡ መትጋት ፡ ብቻ ፡ ነው ። ጳውሎስ ስለ ፡ ሃይማኖት ፡ የሚደረገው ፡ ስብከት ፡ አጭር ፡ ነው ፡ የሕይወት ፡ ትእዛዝ ፡ ግን ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ይኖራል ፡ እንዳለ ። (ዕብ ፡ ፲፩ ፡ ፴፱) ፡ ሰባክያን ፡ በየሀገሩ ፡ የፍርድ ፡

ዘሥርዓት ፡ በውስተ ፡ እህጉር ፡ ለሊቃውንት ።

እስመቦ ፡ እለ ፡ ይጼውዑ ፡ ሰብአ ፡ ኀበ ፡ ኀዲገ ፡ ጥሪት ፡ ፍጹመ ፡ ኢሠርዑ ፡ ሎሙ ፡ ቀኖናተ ፡ ፍሉጣተ ፡ በእንተ ፡ ፍትሐ ፡ ልቃሕያት ፡ ወተሳትፎታት ፡ ወለእለ ፡ ይስሕቡ ፡ ኀበ ፡ ኀዲገ ፡ አውስቦ ፡ ኢሠርዑ ፡ ሎሙ ፡ ፍትሐ ፡ ዚአሁ ። ወለእለ ፡ ይከልኡ ፡ አፍቅሮተ ፡ ዓለም ፡ ወዘሀሎ ፡ ውስቴቱ ፡ ኢሐገጉ ፡ ሎሙ ፡ ሥርዓተ ፡ ተናግዶ ፡ ወረባኅ ።

ወዓዲ ፡ በቀዊሞሙ ፡ ሠሪዐ ፡ ምግባራት ፡ ሥጋውያት ፡ እለ ፡ በከዊነ ፡ እንተ ፡ መፍትው ፡ ይፍትሑ ፡ ባቲ ፡ መኳንንት ፡ ላዕለ ፡ ሰብእ ፡ በዘተነግረ ፡ በሕግ ፡ ቀዳማዊ ፡ ዘውእቱ ፡ ኦሪት ፡ በከመ ፡ ተሠርዐ ፡ በእንቀጸ ፡ ዚአሁ ። ወበእንተዝ ፡ ይቤ ፡ ጴጥሮስ ፡ ሐዋርያ ፡ በ፲ወ፪ ፡ ትእዛዝ ፡ እም፴ወ፩ ፡ ኦአኃው ፡ መጻሕፍት ፡ ይሜህራክሙ ፡ በእንተ ፡ ዘተርፉ ፡ ትእዛዛት ፡ ወንሕነኒ ፡ ንነግረክሙ ፡ ዘተአዘዝነ ፡ ቦቱ ።

ወረሰዩ ፡ ጸሐቆሙ ፡ ኀበ ፡ ሕገ ፡ ፍጻሜ ፡ ወኀበ ፡ ፈጽሞተ ፡ ገሥፆተ ፡ ምግባራት ፡ ዘውስጥ ፡ መንፈሳዊት ፡ ዘይደልዎ ፡ ለለባዊ ፡ ከመ ፡ የአኃዝ ፡ ባቲ ፡ ነፍሶ ፡ ዘኢይደልዎሙ ፡ ለመኳንንት ፡ ይፍትሑ ፡ ባቲ ፡ ዘከመ ፡ ገሥፆተ ፡ ሐሊናት ፡ ወጠባይዓት ፡ ወመጻእያት ፡ ዘውስጥ ፡ ወአኮ ፡ እንተ ፡ ትትገበር ፡ በመለያልይ ፡ ዘከዊነ ። እስመ ፡ ለዝንቱ ፡ ተማሣዕ ፡ ደኃራዊ ፡ ይትረከብ ፡ ቦቱ ፡ ፍጻሜ ፡ ሰብእ ፡ ዘተማረረ ፡ በነፍስ ፡ ወሥጋ ፡ በገቢረ ፡ ምግባራቲሁ ፡ ነፍሳዊት ፡ ወሥጋዊት ፡ እስመ ፡ ነፍስ ፡ ይእቲ ፡ እንተ ፡ ታንሰሐስሖ ፡ ለሥጋ ፡ ወእምከመ ፡ ተገሠፀ ፡ ኣንሰሐሳሒ ፡ ወኮነ ፡ ፍጹመ ፡ ይትጌሠጽ ፡ ምግባራቲሁ ፡ እለ ፡ ይትገበሩ ፡ በዘያንሰሐስሕ ፡ ዘውእቱ ፡ ሥጋ ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ከመ ፡ ንዋየ ፡ መስቆ ፡ ለነፍስ ።

ወናሁ ፡ ተሠርዐ ፡ በተፍጻሚተ ፡ ዝንቱ ፡ መጽሐፍ ፡ ዘይደሉ ፡ ለሊቃውንት ፡ ከመ ፡ ይወስኩ ፡ ዲቤሁ ፡ ወያንትጉ ፡ እምኔሁ ፡ ወእልቦ ፡ ዘኢኮነ ፡ ሎሙ ፡ ብዉሐ ፡ ውስተ ፡ ዝንቱ ። ወተዘከረ ፡ በመትሎሁ ፡ ውስተ ፡ አሐዱ ፡ ምዕራፍ ፤ ከመ ፡ ይደሉ ፡ ገቢረ ፡ ቀኖናተ ፡ ቃለ ፡ ማኅበር ፡ ዘኒቅያ ፡ በብሂሎቶሙ ። ወለእመ ፡ ተዐደወ ፡ ፩ሂ ፡ ዘእቅደምነ ፡ ወብህልናሁ ፡ እኮ ፡ ኪያነ ፡ ዘይትቃወም ፡ አላ ፡ ይትቃወሞ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ውእቱ ፡ ለይሕትት ፡ ዝንቱ ፡ መጻሕፍተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወያስተሐይጽ ፡ መጻሕፍተ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፤ አሚሃ ፡ ይሌቡ ፡ ከመ ፡ እግዚአብሔር ፡ አዘዘነ ፡ በዝንቱ ፡ ኵሉ ።

ወይትዐወቅ ፡ እምቀኖናሆሙ ፡ ከመ ፡ ኵሉ ፡ ዘተ



መጽሐፍን ፡ ለይቶ ፡ መጻፍን ፡ ለሊቃውንት ፡ ተዉ ።

ሰውን ፡ ፈጽሞ ፡ ገንዘብን ፡ ወደመተው ፡ የሚጠሩበት ፡ ጊዜ ፡ ነበረና ፡ ስለ ፡ ብድርና ፡ ስለ ፡ ሽርክና ፡ ለሚፈርደው ፡ ፍርድ ፡ የተለዩ ፡ ሕጎችን ፡ አልሠሩላቸውም ። ጋብቻን ፡ ወደመተው ፡ ለሚያስቡትም ፡ ሰዎች ፡ የዚህን ፡ ፍርድ ፡ አልሠሩላቸውም ። ዓለምንና ፡ በውስጡ ፡ ያለውን ፡ መውደድን ፡ ለሚከለክሉትም ፡ የንግድንና ፡ የትርፍን ፡ ፍርድ ፡ አልደነገጉላቸውም ።

ዳግመኛም ፡ ዳኞች ፡ በሰዎች ፡ ላይ ፡ የሚፈርዱት ፡ ሥጋዊ ፡ ፍርድ ፡ በቀድሞ ፡ ሕግ ፡ በኦሪት ፡ በተነገረውና ፡ በአንቀጹ ፡ በተወሰነው ፡ ይበቃል ፡ ብለው ፡ ለተገለጡት ፡ ሥራዎች ፡ ሕግ ፡ መሥራትን ፡ ተዉ ። ስለዚህም ፡ ሐዋርያው ፡ ጴጥሮስ ፡ ከ፴፩ዱ ፡ ውስጥ ፡ በ፲፪ኛው ፡ ትእዛዝ ፡ "ወንድሞች ፡ ሆይ ፡ ከእኛ ፡ የቀረውን ፡ መጻሕፍት ፡ ያስተምሩአችኋል ፤ እኛም ፡ የታዘዝነውን ፡ እንነግራችኋለን" ፡ አለ ።

ትጋታቸውን ፡ ወደ ፡ ፍጹምነት ፡ ሕግ ፡ ወደ ፡ ወንጌልና ፡ ነፍስ ፡ በሕዋሳት ፡ ውስጥ ፡ የምትሠራቸውን ፡ ሥራዎች ፡ ወደ ፡ መገሠጽ ፡ አደረጉ ። ፀዋቂ ፡ ሰው ፡ መኳንንት ፡ ሊፈርዱባት ፡ የማይቻላቸውን ፡ ነፍሱን ፡ ወስኖ ፡ ለመያዝ ፡ የሚበቃበትን ፡ ይኸውም ፡ በሕዋሳተ ፡ አፍአ ፡ የሚሠሩ ፡ ሥራዎችን ፡ ያይደለ ፡ በሕዋሳተ ፡ ውስጥ ፡ የሚሠሩ ፡ ሥራዎችን ፡ ወስኖ ፡ መያዝ ፡ ነው ። በዚህ ፡ በኋለኛው ፡ ተግሣጽ ፡ ነፍሳዊና ፡ ሥጋዊ ፡ ሥራዎችን ፡ በመሥራት ፡ ከሥጋና ፡ ከነፍስ ፡ የተሠራው ፡ የሰው ፡ ፍጹምነት ፡ ይገኝበታልና ። ሥጋን ፡ የምታንቀሳቅሰው ፡ ነፍስ ፡ ናትና ፤ አንቀሳቃሹ ፡ (ነፍስ) ፡ ከተገሠጸ ፡ ፍጹምም ፡ ከሆነ ፡ በሚንቀሳቀሰው ፡ የሚሠሩት ፡ ሥራዎች ፡ ይገሠጻሉ ፤ ይኸውም ፡ ሥጋ ፡ ነው ። እርሱ ፡ (ሥጋ) ፡ ለነፍስ ፡ እንደ ፡ መሆን ፡ ነውና ።

እነሆ ፡ በዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ መጨረሻ ፡ ላይ ፡ ለሊቃውንት ፡ የሚገባው ፡ ነገር ፡ ተጽፎአል ፤ በእርሱ ፡ ላይ ፡ እንዲጨምሩ ፡ ከእርሱም ፡ እንዲቀንሱ ፡ በዚህ ፡ ውስጥ ፡ ያልተፈቀደላቸው ፡ ነገር ፡ የለም ። በሚቀጥለው ፡ በምዕራፍ ፡ ፩ ፡ ውስጥም ፡ ቀኖናትን ፡ ማድረግ ፡ እንዲገባ ፡ ተነገረ ። የኒቅያ ፡ ማኅበር ፡ እንዲህ ፡ አሉ ። አስቀድመን ፡ የተናገርነውን ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ አንኳ ፡ ቢያፈርስ ፡ እኛን ፡ የሚቃወም ፡ አይደለም ፤ እርሱ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ይቃወማል ፡ እንጂ ፤ ይህ ፡ ሰው ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መጻሕፍት ፡ ይመርምር ፤ የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ መጻሕፍትንም ፡ ይመልከት ። ያንጊዜ ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዳዘዘን ፡ ይረዳል ።" አሉ ።

አምላክ ፡ በአጻፋቸው ፡ መጻሕፍትና ፡ ሐዋርያት ፡

ንግረ ፡ ባቲ ፡ ኢኮነ ፡ ፍሉጠ ፡ ወከሙተ ፡ ወዘይትዐወቅ ፡ ውስተ ፡ መጻሕፍት ፡ እምላካውያት ፡ ወቀኖናት ፡ ሐዋርያውያት ። ወእመ ፡ አኮሰ ፡ እምኮነ ፡ ዘተነግረ በቀኖና ሆሙ ፡ ለማኅበር ፡ ደጊሞተ ፡ ነገር ፡ ዘኢይትፈቀድ ፡ ውእቱ ። ወባሕቱ ፡ ተነግረ ፡ እምቀዲሙ ፡ ድሙረ ፡ ዘእንበለ ፡ ፍልጠት ፡ ወፈለጥዎ ፡ ድኅረ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ዘይትአነዝ ፡ ወይትሜጠን ፡ በከመ ፡ አቅደምነ ፡ ነገረ ። ወዝንቱ ፡ ውእቱ ፡ ግብሩ ፡ ለዝንቱ ፡ መጽሐፍ ፡ ወእምሳሊሁ እምውስተ ፡ ዘተደንገረ ፡ በዘመን ፡ ፀ ፡ ዘይመስል ፡ ለኀበ ፡ ዘቀደሞ ፡ ወንሰእል ፡ እምኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምሕረተ ፡ ወተሰናስዎ ፡ ወረድኤተ ።

እእምር ፡ ከመ ፡ ዝንቱ ፡ መጽሐፍ ፡ ይነግር ፡ መቅድመ ፡ ወክልኤተ ፡ ኅብረታተ ፡ ወመቅድምሂ ፡ ይዜኑ ፡ በእንተ ፡ ክልኤቱ ፡ ክፍላት ። ቀዳማዊሰ ፡ ነዋ ፡ ቀደመ ። ዳግማዊኒ ፡ ሀሎ ፡ በዘክሮተ ፡ መጻሕፍት ፡ ወቀኖናት ፡ ዘአስተጋብአ ፡ ዝንቱ ፡ መጽሐፍ ፡ ወከሚተ ፡ ትእምርታቲሆሙ ። ለመጻሕፍትሰ ፡ እምላካውያት ፡ ትእምርተ ፡ ፊደለ ፡ ወንጌል ፡ ፳ ፡ ወለግብረ ፡ ሐዋርያት ፡ ወሐዋርያ ፡ ትእምርቶሙ ፡ ስመ ፡ እንባርዮን ፡ ቃል ። ወለመልእክታተ ፡ ጳውሎስኒ ፡ ትእምርቶሙ ፡ በስመ ፡ አህጉር ፡ ወበስመ ፡ ብእሲ ፡ ዘጸሐፈ ፡ ሎቱ ፡ መልእክተ ፡ እው ፡ በስመ ፡ ካልእ ፡ እምአስማት ። ለዕብራውያን ፡ ዕብ ፡ ወለጢሞቴዎስ ፡ ጢሞ ። ወለመጻሕፍተ ፡ አረትኒ ፡ በ፬ ፡ ፊደላት ፡ እሙንቱ ፡ ወፊደለ ፡ ትእምርተ ፡ አረት ፡ ቀዳማዊ ፡ ትአ ፡ ወዳግማዊ ፡ ትቤ ፡ ወሣልስ ፡ ትጋ ፡ ወራብዕ ፡ ትዳ ፡ ወኃምስ ፡ ትሔ ፡ ወበዝ ፡ ኍልቈ ፡ መጻሕፍት ።

ለመጻሕፍተ ፡ ቀኖናትሰ ፡ ቀዳሚሆሙ ፡ ቀኖና ፡ ዘሠርዕዋ ፡ ሐዋርያት ፡ ወእሙንቱ ፡ እንዘ ፡ ጉቡአን ፡ በጽርሐ ፡ ጽዮን ፡ እምድኅረ ፡ ዕርገት ፡ ወርደተ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ ወእምቅድመ ፡ ይዘረዉ ፡ በእንተ ፡ ስብከት ። ወጸመዉ ፡ መስካውያን ፡ ወንስጥርሳውያን ፡ በእንተ ፡ ተርጕሞቱ ፡ እምልሳነ ፡ ጽርእ ፡ ኀበ ፡ ዓረቢ ። ወውእቱ ፡ ሀሎ ፡ ኀበ ፡ ያዕቆባውያን ፡ ወሶርያውያን ፡ ወውእቱ ፡ ጽሑፍ ። ወኍልቊሰ ፡ በኀበ ፡ መስካውያን ፡ ፹ ፡ ቀኖናት ፡ ወትእምርተ ፡ ፊደሉኒ ፡ ዓይን ፡ ውእቱ ።

ወዳግማዊ ፡ ቀኖና ፡ ዘአስተናበርዎ ፡ ካዕበ ፡ ሐዋርያት ፡ ወፈነውዎ ፡ በእደ ፡ ቀሌምንጦስ ፡ ረድእ ፡ ጴጥ



በሥራዋቸው ፡ ቀኖናት ፡ የታወቀውና ፡ በእርስዋ ፡ የተነገረው ፡ ሁሉ ፡ የተለየ ፡ የተገለጠ ፡ እንዲሆን ፡ ከቀኖናቸው ፡ የተነሣ ፡ ይታወቃል ፡ ይህስ ፡ ባይሆን ፡ ኖሮ ፡ በማኅበሩ ፡ ቀኖና ፡ የተነገረው ፡ የማይወደድ ፡ ነገርን ፡ መደጋገም ፡ በሆነ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ መጀመሪያውኑ ፡ ያለ ፡ መለየት ፡ በአንድነት ፡ ተነገረ ። አስቀድመን ፡ እንደተናገርን ፡ የሚመጠን ፡ የሚያዝ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ በኋላ ፡ ለዩት ። የዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ ሥራውና ፡ ልማዱ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ በኋላ ፡ ዘመን ፡ ከተነገረው ፡ ውስጥ ፡ የቀደመውን ፡ የሚመስል ፡ አለበት ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ይቅርታንና ፡ ስምምነትን ፡ እርዳታንም ፡ እንለምናለን ።

ይህ ፡ መጽሐፍ ፡ መቅድምንና ፡ ሁለቱን ፡ ዓይነቶች ፡ (ሥጋዊና ፡ መንፈሳዊ ፡) እንደሚናገር ፡ ዕወቅ ። መቅድሙም ፡ ስለ ፡ ሁለቱ ፡ ክፍሎች ፡ ይናገራል ። መጀመሪያው ፡ እነሆ ፡ አስቀድሞ ፡ ተነገረ ። ሁለተኛውም ፡ መጻሕፍትንና ፡ ይህ ፡ መጽሐፍ ፡ የሰበሰባቸውን ፡ ቀኖናት ፡ በመጥቀስ ፡ ምልክቶቻቸውንም ፡ በመግለጥ ፡ ተነገረ ።

የእምላክ ፡ መጻሕፍት ፡ ግን ፡ የወንጌል ፡ ፊደል ፡ ምልክት ፡ ፳ ፡ ነው ። የግብረ ፡ ሐዋርያትና ፡ የሐዋርያ ፡ ምልክታቸው ፡ መጽሐፉን ፡ ጽፈው ፡ ያኖሩት ፡ ሰዎች ፡ ስም ፡ ነው ። የጳውሎስ ፡ መልእክታትም ፡ ምልክታቸው ፡ በአገሮቹ ፡ ስምና ፡ መልእክቱን ፡ በጻፈለት ፡ ሰው ፡ ስም ፡ ነው ። ወይም ፡ ከስሞቹ ፡ በሌላ ፡ ስም ፡ ነው ። ከዕብራውያን ፡ ሲጠቅስ ፡ ዕብ ፡ ይላል ። ከጢሞቴዎስ ፡ ሲጠቅስ ፡ ጢሞ ፡ ይላል ። የአረት ፡ መጻሕፍትም ፡ ምልክታቸው ፡ በሁለት ፡ ፊደሎች ፡ ተወስኗል ። የመጀመሪያው ፡ አረት ፡ ምልክት ፡ ትአ ፡ ነው ። የሁለተኛው ፡ ምልክት ፡ ትቤ ፡ የሶስተኛው ፡ ምልክት ፡ ትጋ ፡ የአራተኛው ፡ ምልክት ፡ ትዳ ፡ የአምስተኛው ፡ ምልክት ፡ ትሔ ፡ ይላል ። ሆሄ ፡ የመጻሕፍት ፡ መቁጠሪያ ፡ ነው ።

የቀኖና ፡ መጻሕፍት ፡ መጀመሪያቸው ፡ ሐዋርያት ፡ የሠሩዋት ፡ ናት ። እነርሱ ፡ ከዕርገትና ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ከወረደ ፡ በኋላ ፡ ለስብከት ፡ ከመበተናቸውም ፡ አስቀድሞ ፡ በጽርሐ ፡ ጽዮን ፡ ተሰብስበው ፡ ሳሉ ፡ የሠሩዋት ፡ ናት ። ንስጥሮሳውያንና ፡ መስካውያን ፡ ይህን ፡ ከግሪክ ፡ ወደ ፡ ዐረቢኛ ፡ ለመተርጐም ፡ ደከሙ ። እርሱም ፡ በያዕቆባውያንና ፡ በሶርያውያን ፡ ዘንድ ፡ አሁን ፡ አለ ፡ እርሱም ፡ ተጽፎአል ። በመስካውያን ፡ ዘንድ ፡ ቊጥሩ ፡ ፹ ፡ ቀኖና ፡ ነው ። የፊደሉም ፡ ምልክት ፡ ዓይን ፡ ነው ።

ሁለተኛው ፡ ቀኖና ፡ ሐዋርያት ፡ ዳግመኛ ፡ ያዘጋጁትና ፡ የሊቀ ፡ ሐዋርያቱ ፡ የጴጥሮስ ፡ ደቀ ፡ መዝሙር ፡

ሮስ ፡ ሊቀ ፡ ሐዋርያት ፡ ኀበ ፡ ኵሎሙ ፡ አርድእት ፡ ወኀበ ፡ ኵሎሙ ፡ መሃይምናን ። ወተርጐምዎ ፡ ኀበ ፡ ዓረቢ ፡ መለካውያን ፡ ወንስጥሮሳውያን ፡ ውስተ ፡ አሐቲ ፡ መጽሐፍ ። ወኍላቌሃ ፡ በኀበ ፡ መለካውያን ፡ ፹ወ፫ቱ ። ወከማሁ ፡ ውእቱ ፡ በኀበ ፡ ያዕቆባውያን ፡ ወሶርያውያን ። ወኍልቍሰ ፡ በኀበ ፡ ንስጥሮሳውያን ፡ በከመ ፡ ይነግር ፡ መጽሐፈ ፡ ኵሎሙ ፡ ክርስቲያን ፡ ዘአስተጋብአ ፡ ወልደ ፡ ጠይብ ፡ ንስጥሮሳዊ ፡ ፹ወ፪ቱ ። ወትእምርቱሰ ፡ ፬ ፡ ፊደላት ፡ ፪ቱ ፡ እምስመ ፡ ሐዋርያት ፡ ወሣልስ ፡ እምስመ ፡ ረድእ ፡ ዘተፈነወ ፡ በእደዊሁ ። ትብህለ ፡ ከመ ፡ አባ ፡ ሚካኤል ፡ ዘሀገረ ፡ ድምያጥ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ አሎንተ ፡ ሕፀረ ፡ ቀኖናተ ፡ አስተጋብአ ፡ ዘውእቶሙ ፡ ፫ቱ ፡ መጻሕፍት ፡ እምነተሉ ፡ ዘተጽሕፉ ፡ እምኔሆሙ ፡ ለለ ፡ አሐዱ ፡ በበኍልቆሙ ፡ ወኢኮነ ፡ አሐዱ ፡ ዘተከሥተ ፡ እምካልእ ፡ ውእቱ ፡ ባሕቲቱ ፡ ከሠቶሙ ፡ ወራብእኒ ፡ ይመርሕ ፡ ስሙ ፡ ዘከመ ፡ ቀዳማዊ ፡ ውእቱ ፡ ወትእምርቱኒ ፡ ረስጦአ ፡ ዘውእቱ ፡ ቀሌምንጦስ ፡ ቀዳማዊ ።

ወግብጻውያንስ ፡ አውፅኡ ፡ በኍልቌ ፡ አሌፍ ፡ ፩ ፡ ቤት ፡ ፪ ፡ ወከመዝ ፡ እስከ ፡ ፲ ፡ ወበኀበ ፡ ካፍስ ፡ ፳ ፡ ላሜድ ፡ ፴ ፡ ወከመዝ ፡ እስከ ፡ ተፍጻሜቱ ። ወአውፅኡ ፡ ውእቶሙ ፡ ዘንተ ፡ ኀበ ፡ ፪ቱ ፡ መጻሕፍት ፡ አለ ፡ ይነግሩ ፡ ለለ ፡ አሐዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ዘይበዝኅ ፡ እምዘሀሎ ፡ ውስተ ፡ ካልኡ ፡ ወኍልቌ ፡ አሐዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ፸ወ፩ቱ ፡ ቀኖና ፡ ወትእምርቱ ፡ ረስጠብ ፡ ዘውእቱ ፡ ቀሌምንጦስ ፡ ዳግም ። ወኍልቌ ፡ ካልእኒ ፡ ፶ወ፮ቱ ፡ ወትእምርቱኒ ፡ ረስጠጅ ፡ ዘውእቱ ፡ ቀሌምንጦስ ፡ ሣልስ ።

እሎንኬ ፡ መጻሕፍት ፡ ፫ቲሆን ፡ የኀብሩ ፡ በነገር ፡ ወፍሉጣት ፡ አማንቱ ፡ በኍልቌ ፡ አከፋል ፡ ኢይዌስክ ፡ አሐዱ ፡ ላዕለ ፡ ካልኡ ፡ ዘእንበለ ፡ በኀዳጥ ።

ወሣልስ ፡ መጽሐፍ ፡ ዘዐዉቅ ፡ በኀበ ፡ ግብጻውያን ፡ ዲድስቅልያ ፡ ዘውእቱ ፡ ትምህርት ፡ ብሂል ፡ ወይነግር ፡ ከመ ፡ አሙንቱ ፡ ተጋብኡ ፡ በእንተ ፡ አንብሮቱ ፡ ውስተ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ፲ወ፪ቱ ፡ ሐዋርያት ፡ ወጳውሎስ ፡ ኅሩይ ፡ ወያዕቆብ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ዘኢየሩሳሌም ። ወጽሕቁ ፡ በእንተ ፡ አውፅአቱ ፡ ግብጻውያን ፡ ወአልቦ ፡ ውስቴቱ ፡ ምንትኒ ፡ ዘየሐጽጽ ፡ እምቀኖናት ። ወመብዝኅቶ ፡ ረሰዩ ፡ ስምዐ ፡ ውስቴቱ ፡ በውስተ ፡ መካናት ፡ እምወንጌል ፡ ወእምብሉይ ፡ ወኍላቌሁ ፡ ፵ወ፫ቱ ፡ አን



በሆነ ፡ በቀሌምንጦስ ፡ እጅ ፡ ወደ ፡ ምእመናን ፡ ሁሉ ፡ የላኩት ፡ መጽሐፍ ፡ ነው ። መለካውያንና ፡ ንስጥሮሳውያን ፡ አንድ ፡ መጽሐፍ ፡ አድርገው ፡ ወደ ዐረብኛ ተረጐሙት ። ቍጥሩም ፡ በመለካውያን ፡ ዘንድ ፡ ፹፫ ፡ ነው ። በያዕቆባውያንና ፡ በሶርያውያንም ፡ ዘንድ ፡ ቍጥሩ ፡ እንደዚሁ ፡ ነው ። በንስጥሮሳውያን ፡ ዘንድ ፡ ያለው ፡ ቍጥሩ ፡ ግን ፡ ንስጥሮሳዊ ፡ ወልደ ፡ ጠይብ ፡ የሰበሰበው ፡ የክርስቲያኖች ፡ ሁሉ ፡ መጽሐፍ ፡ እንደ ሚናገረው ፡ ፹፪ ፡ ነው ። ምልክቱም ፡ አራት ፡ ፊደላት ፡ ናቸው ። ሁለቱ ፡ ከሐዋርያት ፡ ስም ፡ ሦስተኛውም ፡ በእጁ ፡ ከተላከበት ፡ ደቀ ፡ መዝሙር ፡ ስም ፡ ላይ ፡ የተጠቀሰ ፡ ነው ። የድምያጥ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ አባ ፡ ሚካኤል ፡ እነዚህን ፡ ቀኖናት ፡ አሳጥሮ ፡ እንደ ፡ ሰበሰባቸው ፡ ተነገረ ። እነርሱም ፡ እያንዳንዳቸው ፡ በየቍጥራቸው ፡ ከተጻፉት ፡ ወገን ፡ የሆኑ ፡ ሦስት ፡ መጻሕፍት ፡ ናቸው ። አንድ ፡ እንኳ ፡ በሌላ ፡ የተገለጠ ፡ አይደለም ። እርሱ ፡ ብቻ ፡ ገለጣቸው ፡ እንጂ ። አራተኛውም ፡ መጀመሪያ ፡ እንደሆነ ፡ ስሙ ፡ ያስረዳል ። ምልክቱም ፡ ረስጦአ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ የመጀመሪያው ፡ ቀሌምንጦስ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ግብጻውያን ፡ ግን ፡ አሌፍን ፡ ፩ ፡ ቤትን ፡ ፪ ፡ ብለው ፡ ቈጠሩ ፡ በዚህም ፡ ሁኔታ ፡ እስከ ፡ ፲ ፡ ቈጠሩ ። ካፍን ፡ ፳ ፡ ላሜድን ፡ ፴ ፡ አደረጉት ። በዚህ ፡ ዓይነት ፡ እስከ ፡ መጨረሻው ፡ ቈጠሩ ። እያንዳንዱ ፡ ባንዱ ፡ ውስጥ ፡ ካለው ፡ የሚበልጥ ፡ የሚናገሩ ፡ ሁለት ፡ መጻሕፍት ፡ አድርገው ፡ አወጣጡት ። ከእነርሱም ፡ ያንዱ ፡ ቍጥር ፡ ፸፩ ፡ ቀኖና ፡ ነው ። ምልክቱም ፡ ረስጠብ ፡ ይላል ። ይኸውም ፡ ሁለተኛው ፡ ቀሌምንጦስ ፡ ማለት ፡ ነው ። የሁለተኛውም ፡ ቍጥር ፡ ፶፮ ፡ ነው ። ምልክቱም ፡ ረስጠጅ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ ሦስተኛው ፡ ቀሌምንጦስ ፡ ማለት ፡ ነው ።

እነዚህም ፡ ሦስቱ ፡ መጻሕፍት ፡ በነገር ፡ ይተባበራሉ ። በአከፋፈል ፡ ቍጥር ፡ ግን ፡ የተለያዩ ፡ ናቸው ። አንዱ ፡ በሁለተኛው ፡ ላይ ፡ ከጥቂት ፡ በቀር ፡ አይጨምርም ።

ሦስተኛውም ፡ መጽሐፍ ፡ በግብፃውያን ፡ ዘንድ ፡ ዲድስቅልያ ፡ በመባል ፡ የታወቀ ፡ ነው ። ትርጓሜውም ፡ ትምህርት ፡ ማለት ፡ ነው ። እርሱን ፡ ጽፎ ፡ ለማኖር ፡ ፲፪ቱ ፡ ሐዋርያትና ፡ የተመረጠው ፡ ጳውሎስ ፡ የኢየሩሳሌም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ያዕቆብም ፡ በኢየሩሳሌም ፡ እንደ ተሰበሰቡ ፡ ይናገራል ። ግብጻውያን ፡ እርሱን ፡ ተርጕሞ ፡ ለማውጣት ፡ ተጉ ። ከቀኖናት ፡ ምንም ፡ የሚያንስበት ፡ የለውም ። ከውስጡም ፡ በየአንቀጹ ፡ ላይ ፡ አብዛኛውን ፡ ከወንጌልና ፡ ከብሉይ ፡ ምስክር ፡ አደረጉለት ።

ቀጽ ፡ ወትእምርቱ ፡ ድስቅ ፡ ዝ ፡ ውእቱ ፡ ዲድስቅልያ ።

ወራብዕኒ ፡ መልእክተ ፡ ጴጥሮስ ፡ ኀበ ፡ ቀሌምንጦስ ፡
ወትእምርቱ ፡ ጴጥ ፡ ዝ ፡ ውእቱ ፡ ጴጥሮስ ።

ወሐምስ ፡ ቀኖና ፡ ጉባኤ ፡ ቀዳሚሆሙ ፡ ለጉባኤያት ፡
እለ ፡ ተጋብኡ ፡ እምድኅረ ፡ ሐዋርያት ፡ በሀገረ ፡ ዕንቆራ ፡
ዘእምአህጉረ ፡ ገላትያ ። ወኍልቆሙ ፡ ፲ወ፪ ፡ ኤጲስ
ቆጶሳት ፡ ወተጋብኡ ፡ በእንተ ፡ ምክንያት ፡ ዘወድቀ ፡
እመ ፡ ዘመነ ፡ ፍርሃት ፡ በዘዘዚአሁ ፡ ክህደት ፡ ወኍልቍ ፡
በመጽሐፈ ፡ ቅብጥ ፡ ፳ወ፭ ፡ ቀኖና ። ወትእምርታሂ ፡
ስመ ፡ ዚአሃ ።

ወሳድስ ፡ ቀኖና ፡ ማኅበር ፡ ዳግማዊ ፡ ዘተጋብኡ ፡
በቅርጣግና ። ወውእቱ ፡ ሀልው ፡ ኀበ ፡ ቂሳርያ ። ወኍል
ቆሙ ፡ ፶ ኤጲስቆጶሳት ። ወሥርዑ ፡ ፲ወ፬ተ ፡ ቀኖናተ ፡
በእንተ ፡ ስብሳብ ፡ ወካህናት ። ወትእምርቱ ፡ ቀጠግ ፡
ዝውእቱ ፡ ቅርጣግና ።

ወሳብዕ ፡ ቀኖና ፡ ጉባኤ ፡ ሣልስ ፡ ዘግንግራ ። ወኍ
ልቆሙ ፡ ፲ወ፫ቱ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ዘተጋብኡ ፡ በእንተ ፡
እውግዞቶሙ ፡ ለእለ ፡ የሐርሙ ፡ በሊዐ ፡ ሥጋ ፡ ወአው
ስቦ ። ወሥርዑ ፡ ዘንተ ፡ በእንተዝ ፡ ወዘይመስሎ ፡ ፳ ፡
ቀኖናተ ። ወትእምርቱ ፡ ግንር ፡ ዝውእቱ ፡ ግንግራ ።

ወሳምን ፡ ቀኖና ፡ ጉባኤ ፡ ራብዕ ። ወኍልቆሙ ፡
፲ወ፫ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ዘተጋብኡ ፡ በእንጾኪያ ፡ በእንተ ፡
ክህደተ ፡ ጳውሎስ ፡ ሳሚሳጢ ፡ ሶበ ፡ ይቤ ፡ እስመ ፡ ክር
ስቶስ ፡ ሰብእ ፡ ዕሩቅ ። ወመተርዎ ፡ ወሥርዑ ፡ ፳ወ፭ተ ፡
ቀኖናተ ፡ በእንተ ፡ ክህነት ። ወትእምርቱ ፡ ጾክ ፡ ዝው
እቱ ፡ እንጾኪያ ።

ወታስዕ ፡ ቀኖና ፡ ጉባኤ ፡ ኃምስ ፡ ወውእቱ ፡ ቀዳሚ
ሆሙ ፡ ለጉባኤያት ፡ ዐበይት ፡ ዘተጋብኡ ፡ በኒቅያ ፡ በ፫፻
፳ወ፭ቱ ፡ ዓመት ፡ እምሥጋዌ ፡ ወበ፲ወ፱ ፡ ዓመተ ፡ መን
ግሥቱ ፡ ለቈስጠንጢኖስ ፡ ዘየዐቢ ፡ ቀዳሚሆሙ ፡ ለነገ
ሥተ ፡ ክርስቲያን ። ወኍልቆሙ ፡ ፫፻፲ወ፰ቱ ፡ ኤጲስ
ቆጳሳት ። ወተብህለ ፡ ከመ ፡ እሉ ፡ ተኀርዩ ፡ እምኛ፻ወ
፫፻ወ፵ ፡ ኤጲስቆጳሳት ፡ ዘተጋብኡ ፡ በምክንያተ ፡ ክሕ
ደቱ ፡ ለአርዮስ ፡ ሶበ ፡ ይቤ ፡ እስመ ፡ ወልድ ፡ ፍጡር ፡
ውእቱ ፡ ወተዋሥአ ፡ እለእክንድሮስ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡
ዘእለ ፡ እስክንድርያ ፡ ወሞዖ ። ወነበሩ ፡ ምስሌሁ ፡ ማኅ



ቍጥሩም ፡ ፴፫ ፡ አንቀጽ ፡ ነው ። ምልክቱም ፡ ድስቅ ፡
ነው ። ይኸውም ፡ ዲድስቅልያ ፡ ማለት ፡ ነው ።
አራተኛውም ፡ ጴጥሮስ ፡ ወደ ፡ ቀሌምንጦስ ፡ የላ
ከው ፡ መልእክት ፡ ነው ። ምልክቱም ፡ ጴጥ ፡ ነው ።
ይኸውም ፡ ጴጥሮስ ፡ ማለት ፡ ነው ።
አምስተኛውም ፡ የጉባኤ ፡ ቀኖና ፡ ከሐዋርያት ፡
በኋላ ፡ የገላትያ ፡ አገሮች ፡ ክፍል ፡ በሆነች ፡ በዕንቆራ ፡
ከተማ ፡ የተሰበሰቡት ፡ ሊቃውንት ፡ የጸፉት ፡ የጉባኤ
ዎች ፡ ተቀዳሚያቸው ፡ ነው ፡ ቍጥራቸውም ፡ ፲፪ ፡ ኢጲ
ስቆጶሳት ፡ ነው ። በልዩ ፡ ልዩ ፡ ክሕደት ፡ ምክንያት ፡
ፍርሃት ፡ በበዛበት ፡ ዘመን ፡ ተሰበሰቡ ። ቍጥርዋ ፡ በግ
ብጽ ፡ መጽሐፍ ፡ ፳፭ ፡ ቀኖና ፡ ነው ። ምልክቷም ፡ ስሟ ፡
ነው ።
ስድስተኛውም ፡ በቅርጣግና ፡ የተሰበሰቡት ፡ የ፪ኛው
ማኅበር ፡ ቀኖና ፡ ነው ። ይኸውም ፡ በቂሳርያ ፡ የሚገኝ ፡
ከተማ ፡ ነው ። ቍጥራቸውም ፡ ፶ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ነው ።
ስለ ፡ ጋብቻና ፡ ስለ ፡ ካህናት ፡ ፲፬ ፡ ቀኖናት ፡ ጻፉ ፡ ምል
ክቱም ፡ ቀጠግ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ ቅርጣግና ፡ ማለት ፡
ነው ።
ሰባተኛውም ፡ በግንግራ ፡ የተደረገ ፡ የሦስተኛው ፡
ጉባኤ ፡ ቀኖና ፡ ነው ። ቍጥራቸውም ፡ ፲፫ ፡ ኤጲስቆጶ
ሳት ፡ ነው ። እነርሱም ፡ ሥጋ ፡ መብላትንና ፡ ጋብቻን ፡
የሚከለክሉትን ፡ አውግዞ ፡ ለመለየት ፡ የተሰበሰቡ ፡
ናቸው ። ስለዚህ ፡ ይህንና ፡ የሚመስለውንም ፡ ፳ ፡ ቀኖ
ናት ፡ ጻፉ ። ምልክቱም ፡ ግንር ፡ ነው ። ይኸውም ፡ ግን
ግራ ፡ ማለት ፡ ነው ።
ስምንተኛው ፡ የአራተኛው ፡ ጉባኤ ፡ ቀኖና ፡
ነው ። ቍጥራቸው ፡ ፲፫ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ነው ። እነ
ርሱ ፡ በጳውሎስ ፡ ሳሚሳጢ ፡ ክሕደት ፡ ምክንያት ፡ ክርስ
ቶስ ፡ ዕሩቅ ፡ ብእሲ ፡ ነው ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ በአንጾኪያ ፡
የተሰበሰቡት ፡ ናቸው ። አውግዘውም ፡ ለዩት ፡ ስለ ፡
ክህነት ፡ ፳፭ ፡ ቀኖናት ፡ ጻፉ ፡ ምልክቱም ፡ ጾክ ፡ ነው ፡
ይኸውም ፡ አንጾኪያ ፡ ማለት ፡ ነው ።
ዘጠነኛውም ፡ የአምስተኛው ፡ ጉባኤ ፡ ቀኖና ፡ ነው ።
እርሱም ፡ የታላላቅ ፡ ጉባኤያት ፡ ተቀዳሚያቸው ፡ ነው ።
ይኸውም ፡ ከክርስቶስ ፡ ልደት ፡ በኋላ ፡ በ፫፻፳፭ ፡ ዓመት
ለክርስቲያን ፡ ነገሥታት ፡ መጀመሪያቸው ፡ የሆነ ፡
ታላቁ ፡ ቈስጠንጢኖስ ፡ በነገሠ ፡ በ፲፱ኛው ፡ ዓመት ፡
በኒቅያ ፡ ስብሰባ ፡ የተደረገበት ፡ ነው ። ቍጥራቸው ፡
፫፻፲፰ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ነው ። እሊህ ፡ ከሁለት ፡ ሺህ ፡
፫፻፵ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ውስጥ ፡ እንዲ ፡ ተመረጡ ፡ ተነገረ ፡
አርዮስ ፡ ወልድ ፡ ፍጡር ፡ ነው ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ በእርሱ ፡
ክሕደት ፡ ምክንያት ፡ የተሰበሰቡ ፡ ናቸው ። የእስክንደ

[illegible]ር ፡ ሰመትሮቲ ፡ ወሰደቲ ፡ ወጸሐፉ ፡ መጽሐፈ ፡ እንተ ፡ [illegible]ት ፡ ውስቴታ ፡ ሃይማኖት ፡ ርትዕት ። ወሠርዑ ፡ እምድኅረ ፡ ፍትሕ ፡ ቀኖናተ ፡ ብዙኀተ ፡ ጥቀ ። ወበዛቲ ፡ መጽሐፍ ፡ ሀለዉ ፡ ፪ቱ ፡ ክፍል ። ለ፩ ፡ እምኔሆሙ ፡ ኍልቁ ፡ ፷ ፡ ቀኖና ፤ ወእምድኅሬሁሰ ፡ ቃላት ፡ ብዙኃት ፡ ዘአልቦን ፡ ኍልቈ ። ወውእቱ ፡ ዘይሰነዐዉ ፡ ላዕ[illegible] ። ወትእምርቲሁ ፡ ኒቅ ፡ ዝ ፡ ውእቱ ፡ ኒቅያ ።

ወካልኡኒ ፡ ብዙኅ ፡ ረባኅ ፡ ቦቱ ። ወጽሕቀ ፡ ለአዕል[illegible]ቱ ፡ መለካውያን ፡ ወንስጥሮሳውያን ። ወውእቱ ፡ ንቡር ፡ በኀበ ፡ ያዕቆባውያን ፡ ወሶርያውያን ። ወኍልቈ ፡ ዚአሁ ፡ በውስተ ፡ መጽሐፈ ፡ መለካውያን ፡ ፻ወ፬ቱ ፡ ቀኖና ። ወዘይተልዋሆን ፡ ቃላት ፡ ዘአልቦን ፡ ኍልቈ ። ወመጽሐፍሰ ፡ ዘሀሎ ፡ ኀበ ፡ መለካውያን ፡ ቦቱ ፡ ተውሳክ ፡ ለባሕቲቶሙ ፡ ወትእምርቲ ፡ ኒቅያ ።

ዓሥርኒ ፡ ቀኖና ፡ ጉባኤ ፡ ሳድስ ፡ ዘሎዶቅያ ፡ ወኍልቆሙ ፡ ፲ወ፱ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ዘተጋብኡ ፡ በእንተ ፡ [illegible]ኒ ፡ ወዘይመስልዎ ፡ እምስብእ ፡ ፈጠራ ፡ ዕልዋነ ፡ ሃይማኖት ። ወሠርዑ ፡ ፳ወ፱ተ ፡ ቀኖና ፡ በእንተ ፡ ክህነት ፡ መተዐምዶ ፡ ወአውስቦ ፡ ወዘይመስሉ ። ወይእቲ ፡ ብዝኀተ ፡ ረባኅ ። ወትእምርታ ፡ ዶቅ ፡ ዝ ፡ ውእቱ ፡ ሎዶቅያ።

፲ወ፩ዱ ፡ ቀኖና ፡ ዘጉባኤ ፡ ሳብዕ ፡ ወኍልቆሙ ፡ ፲ወ፱ ፡ ኤጲስቆጳሳት ፡ ዘተጋብኡ ፡ በሰርድቅያ ፡ ፩ ፡ ዘሀገረ ፡ ሮም ፡ ወፍልስጢን ፡ በእንተ ፡ አርዮሳውያን ፡ እለ ፡ ተንሥኡ ፡ ላዕለ ፡ አትናቴዎስ ፤ ዘውእቱ ፡ ዓሥር ፡ ወታሕ[illegible] ፡ እምሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ ዘእለ ፡ እስክንድርያ ፡ ወላዕለ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ዘእንጸኪያ ፤ ወላዕለ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ዘቍ[illegible]ንጥንያ ። ወሰደድዎሙ ፡ ወሜጥዎሙ ፡ እሉ ፡ ኀበ ፡ መናብርቲሆሙ ፤ ወሠርዑ ፡ ፳ወ፩ደ ፡ ቀኖና ፡ በእንተ ፡ መዓርገ ፡ ኤጲስቆጶሳት ። ወትእምርቱ ፡ ሰድቅ ፡ ዝውእቱ ፡ ሰርድቅያ ።

፲ወ፪ቱ ፡ ቀኖናተ ፡ እቡሊድስ ፡ ሊቀጳጳሳት ፡ ዘሮሜ ፡ ወኍልቆሙ ፡ ፴ወ፰ ፡ ቀኖና ። ወጽሕቀ ፡ በእንተ ፡ እዕልዎቱ ፡ ግብጻውያን ። ወውእቱ ፡ ይጼጕ ፡ ረባኅ ፡ ፈድፋደ ፡ [illegible]ናሁ ፡ ጸሐፈ ፡ እምኔሁ ፡ አባ ፡ ገብርኤል ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ [illegible]ለ ፡ እለክንድርያ ፡ በውስተ ፡ ቀኖና ፡ ዘአስተጋብአ ፡ [illegible]ያ ። ወትእምርተ ፡ ስሙ ፡ በደሰ ፡ ዝ ፡ ውእቱ ፡ እቡሊድስ ።

ርያው ፡ ሊቀ/፡ ጳጳሳት ፡ እለ ፡ እስክንድሮስ ፡ ተከራክሮ ፡ ረታው ፡ እርሱን ፡ በማውገዝና ፡ በመለየት ፡ ማኅበር ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ተባበሩ ። የቀናች ፡ ሃይማኖት ፡ ያለችበትን ፡ መጽሐፍ ፡ ጻፉ ። ከፍርድ ፡ በኋላም ፡ እጅግ ፡ የበዙ ፡ ቀኖናትን ፡ ጻፉ ። በዚህች ፡ መጽሐፍም ፡ ሁለት ፡ ክፍሎች ፡ አሉ ። ከነርሱ ፡ የአንዱ ፡ ቍጥር ፡ ፷ ፡ ቀኖና ፡ ነው ። ከእርሱ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ ስፍር ፡ ቍጥር ፡ የሌላቸው ፡ ብዙ ፡ ቃላቶች ፡ አሉ ። እነሱም ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የሚስማሙ ፡ ናቸው ። ምልክቱም ፡ ኒቅ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ ኒቅያ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ሁለተኛውም ፡ ብዙ ፡ ጥቅም ፡ አለበት ። መለካውያንና ፡ ንስጥሮሳውያን ፡ እርሱን ፡ ለመተርጐም ፡ ተጉ ። እርሱም ፡ በያዕቆባውያንና ፡ በሶርያውያን ፡ ዘንድ ፡ ይገኛል ። ቍጥሩም ፡ በመለካውያን ፡ መጽሐፍ ፡ ፻፬ ፡ ቀኖና ፡ ነው ። የሚከተሏቸውም ፡ ቃላት ፡ ቍጥር ፡ የላቸውም ። በመለካውያን ፡ ዘንድ ፡ ያለው ፡ መጽሐፍ ፡ ግን ፡ ለብቻው ፡ ትርፍ ፡ አለው ። ምልክቱም ፡ ኒቅያ ፡ ነው ።

አሥረኛውም ፡ በሎዶቅያ ፡ የተደረገው ፡ የስድስተኛው ፡ ጉባኤ ፡ ቀኖና ፡ ነው ። ስለማኒና ፡ ሃይማኖትን ፡ ከለወጡ ፡ የልብ ፡ ወለድ ፡ ሰዎች ፡ ወገን ፡ ስለ ፡ ሚመስሉት ፡ የተሰበሰቡት ፡ ኤጲስቆጳሳት ፡ ቍጥራቸው ፡ ፲፱ ፡ ነው ። ስለ ፡ ክህነት ፡ ስለ ፡ አገልግሎት ፡ ስለ ፡ ጋብቻና ፡ ስለሚመስለውም ፡ ፳፱ ፡ ቀኖና ፡ ጻፉ ፡ ይህችውም ፡ ብዙ ፡ ጥቅም ፡ አለባት ። ምልክቷም ፡ ዶቅ ፡ ይላል ። ይኸውም ፡ ሎዶቅያ ፡ ማለት ፡ ነው ።

አሥራ ፡ አንደኛው ፡ የሰባተኛው ፡ ጉባኤ ፡ ቀኖና ፡ ነው ። ቍጥራቸውም ፡ ፲፱ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ነው ። እነርሱም ፡ ከእስክንድርያ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ ፲፱ኛኛው ፡ በሆነው ፡ በአትናቴዎስና ፡ በእንጾኪያው ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፤ በቍስጥንጥንያው ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ላይ ፡ ስለተነሡት ፡ አርዮሳውያን ፡ የፍልስጢንና ፡ የሮም ፡ አንድ ፡ ክፍል ፡ በሆነች ፡ በሰርድቅያ ፡ የተሰበሰቡ ፡ ናቸው ። እነዚህን ፡ የተነሡትን ፡ አሳረፋዋቸው ። እሊህን ፡ ግን ፡ ወደ ፡ መንበራቸው ፡ መለሷቸው ። ስለ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ መዓርግ ፡ ፳፩ ፡ ቀኖና ፡ ጻፉ ። ምልክቱም ፡ ሰድቅ ፡ ይላል ። ይኸውም ፡ ሰርድቅያ ፡ ማለት ፡ ነው ።

አሥራ ፡ ሁለተኛው ፡ የሮሜ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ የእቡሊዲስ ፡ ቀኖና ፡ ነው ። ቍጥራቸውም ፡ ፴፰ ፡ ቀኖና ፡ ነው ። ስለትርጓሜ ፡ ግብጻውያን ፡ ተጉ ። እርሱም ፡ ብዙ ፡ ጥቅም ፡ ይሰጣል ። የእስክንድርያ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ አባ ፡ ገብርኤል ፡ እርሰዋን ፡ በሰበሰበበት ፡ ቀኖና ፡ ውስጥ ፡ እነሆ ፡ ከእርሱ ፡ ጻፈ ። የስሙም ፡ ምልክት ፡ በደሰ ፡ ይላል ። ይኸውም ፡ እቡሊዲስ ፡ ማለት ፡ ነው ።

፲ወ፫ቱ ፡ ቀኖና ፡ ዘቅዱስ ፡ ባስልዮስ ፡ ዐቢይ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ዘቂሳርያ ፡ በእንተ ፡ ክህናት ፡ ወተሀምዶ ፡ ወእውስቦ ፡ ወዘይመስሎ ፡ ወውእቱ ፡ ቅዉም ፡ በኀበ ፡ ግብጻውያን ፡ ወመለካውያን ፡ ወኍልቆ ፡ ፲ወ፮ቱ ፡ ወሀሎ ፡ ውስቴቱ ፡ ረባሕ ፡ ብዙኅ ፡ ወትእምርቱ ፡ በስ ፡ ዝ ፡ ውእቱ ባስልዮስ ። ወናሁ ፡ ተነግረ ፡ ንስቲት ፡ እምዝድላቲሁ ፡ ውስተ ፡ አንቀጸ ፡ መንኮሳት ፡ ወትእምርቱ ፡ በስ ።

፲ወ፬ቱ ፡ ቀኖናት ፡ ዘአሙራት ፡ በቀኖናተ ፡ ነገሥት ፡ ዘውስቴታ ፡ ሥርዓታት ፡ ዓለማውያት ። ወተብህለ ፡ ከመ ፡ ይእቲ ፡ ፬ ፡ መጻሕፍት ፡ ዘአስተጋብአዎሙ ፡ ለነገሥት ፡ እምቃላት ፡ ብዙኃት ፡ በማኅበረ ፡ ኒቅያ ፡ ወተጽሕፈት ፡ በዓውደ ፡ ቈስጠንጢኖስ ፡ ንጉሥ ። ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ዘአሙር ፡ በአብጥሊስ ። ወኍልቁኒ ፡ ፵ ፡ አንቀጽ ። ወመለካውያን ፡ አስተጋብእዎ ። ወውእቱ ፡ መጽሐፍ ፡ ሠናይ ፡ ፈድፋደ ። ወትእምርቱ ፡ ጠስ ፡ ዘውእቱ ፡ ተጥላሳት ።

ወለካልእኒ ፡ ኍልቁ ፡ በውስተ ፡ ፪ሆን ፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናት ፡ ዘግብጽ ፡ ወመለካውያን ፡ ፻ወ፴ ፡ አንቀጽ ወውእቱ ፡ ሀሎ ፡ ኀበ ፡ ንስጡር ። ወናሁ ፡ ጸሐፈ ፡ እምኔሁ ፡ አባ ፡ ገብርኤል ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ዘእለ ፡ እስክንድርያ ፡ በፍጻሜ ፡ መጽሐፉ ። ወትእምርቱ ፡ መክ ፡ ዘውእቱ ፡ ነገሥት ፡ ዳግም ።

ወሣልስ ፡ ዘጽሕቁ ፡ በእዕልዎቱ ፡ መለካውያን ። ወኍልቁ ፡ ፹ወ፯ቱ ፡ አንቀጽ ፡ ወትእምርቱ ፡ መጅ ፡ ዝ ፡ ውእቱ ፡ ነገሥት ፡ ሣልስ ፡ ወእሉ ፡ ፪ቱ ፡ መጻሕፍት ፡ እለ ፡ የኀብሩ ፡ እምኔሆሙ ፡ ንስቲት ። ወዘተጽሕፈ ፡ እምኔሁ ፡ ኅዳጥ ፡ ውእቱ ።

ወራብዕኒ ፡ ኍልቁ ፡ ፴ወ፰ቱ ፡ ክፍል ፡ ወቀዳማዊ ፡ እምኔሁ ፡ ተጽሕፈ ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡ ፻ወ፷ ፡ ወካልእኒ ፡ ፻፹ወ፩ ። ወመብዝኅቱ ፡ እምፍትሐ ፡ አረት ፡ ወ፬ ፡ እምኔሁ ፡ ዘኢየኀብር ፡ ምስለ ፡ ሐዲስ ፡ ሕግ ። ወዘተጽሕፈ ፡ እምኔሁ ፡ ንስቲት ። ወትእምርቱ ፡ መግ ፡ ዘውእቱ ፡ ነገሥት ፡ ራብዕ ። ወዘይበዝኅ ፡ እመጻሕፍተ ፡ ቀኖና ፡ ይትፈለጥ ፡ ኍልቈ ፡ ፩ዱ ፡ ምስለ ፡ ኍልቈ ፡ ካልኡ ፡

ወአልቦ ፡ ካልእ ፡ ዘይነግር ፡ እመጻሕፍት ፡ ወቀኖናት ፡ እንተ ፡ አቅደምነ ፡ ዘክሮቶን ፡ ዘእንበለ ፡ ዜናዊ ፡ ዘውእቱ ፡ ድዮናስዮስ ። ወትእምርቱ ፡ ድ ፡ ወለጎርጎርዮስ ትእምርቱ ፡ ግር ፡ ወለዮሐንስ ፡ አፈወርቅ ፡ ትእምርቱ ፡

መቅድም

አሥራ ፡ ሦስተኛው ፡ የቂሳርያ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ታላቁ ፡ ቅዱስ ፡ ባስልዮስ ፡ ስለ ፡ ክህነት ፡ ስለ ፡ ምንኵስና ፡ ስለ ፡ ጋብቻና ፡ ስለ ፡ ሚመስለው ፡ የጻፈው ፡ ቀኖና ፡ ነው ። ይኸውም ፡ በግብጻውያንና ፡ በመለካውያን ፡ ዘንድ ፡ ይገኛል ። ቍጥሩም ፡ ፲፮ ፡ ነው ። በውስጡም ፡ ብዙ ፡ ጥቅም ፡ አለበት ። ምልክቱም ፡ በስ ፡ ይላል ። ይኸውም ፡ ባስልዮስ ፡ ማለት ፡ ነው ።

አሥራ ፡ አራተኛው ፡ በውስጢ ፡ ዓለማውያን ፡ ሥርዓቶች ፡ ያሉባት ፡ በነገሥታት ፡ ሕጎች ፡ የታወቁ ፡ ቀኖናት ፡ ናቸው ። በኒቅያ ፡ ማኅበር ፡ ከብዙዎቹ ፡ ቃላት ፡ ለይተው ፡ ለነገሥታት ፡ የሰበሰቡዋቸውና ፡ በንጉሡ ፡ በቈንጠንጢኖስ ፡ አደባባይ ፡ የተጻፉ ፡ ፬ ፡ መጻሕፍት ፡ እንደሆኑ ፡ ተነገረ ። ከእርስዋ ፡ አንዱ ፡ አብጥሊስ ፡ በመባል ፡ የታወቀ ፡ ነው ። ቍጥሩም ፡ ፵ ፡ አንቀጽ ፡ ነው ። መለካውያንም ፡ ሰበሰቡት ። ይህም ፡ መጽሐፍ ፡ እጅግ ፡ ጥሩ ፡ ነው ። ምልክቱም ፡ ጠስ ፡ ይላል ። ይኸውም ፡ ተጥላሳት ፡ ማለት ፡ ነው ።

የሁለተኛውም ፡ ቍጥሩ ፡ በግብጽና ፡ በመለካውያን ፡ በሁለቱም ፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናት ፡ ፻፴ ፡ አንቀጽ ፡ ነው ። እርሱም ፡ በንስጥሮሳውያን ፡ ዘንድ ፡ አለ ። እነሆ ፡ የእስክንድርያው ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ አባ ፡ ገብርኤል ፡ በመጽሐፉ ፡ መጨረሻ ፡ ከእርሱ ፡ ጻፈ ። ምልክቱም ፡ መክ ፡ ይላል ። ይኸውም ፡ ሁለተኛው ፡ የነገሥታት ፡ ሕግ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ሦስተኛው ፡ መለካውያን ፡ ለመተርጐም ፡ የደከሙበት ፡ ነው ። ቍጥሩ ፡ ፹፯ ፡ አንቀጽ ፡ ነው ። ምልክቱም ፡ መጅ ፡ ይላል ። ይኸውም ፡ ሦስተኛው ፡ የነገሥታት ፡ ሕግ ፡ ማለት ፡ ነው ። እሊህ ፡ ሁለቱ ፡ መጻሕፍት ፡ የሚተባበሩት ፡ በትንሹ ፡ ነው ። ከእርሱ ፡ የተጻፈውም ፡

አራተኛውም ፡ ቍጥሩ ፡ ፴፰ ፡ ክፍል ፡ ነው ። ከእርሱም ፡ የመጀመሪያው ፡ ፻፷ ፡ አንቀጽ ፡ ሁለተኛውም ፡ ፻፹፩ ፡ አንቀጽ ፡ እንደሆነ ፡ ተጻፈ ። አብዛኛው ፡ ከኦሪት ፡ ፍርድ ፡ ነው ። ከእርሱም ፡ ውስጥ ፡ ከሐዲስ ፡ ኪዳን ፡ ሕግ ፡ ጋር ፡ የማይተባበር ፡ አለበት ። ከእርሱ ፡ የተጻፈውም ፡ ትንሽ ፡ ነው ። ምልክቱም ፡ መግ ፡ ይላል ። ይኸውም ፡ አራተኛው ፡ የነገሥታት ፡ ሕግ ፡ ማለት ፡ ነው ። የሚበዛው ፡ የሕግ ፡ መጻሕፍት ፡ የአንዱ ፡ ቍጥር ፡ ከሁለተኛው ፡ ጋር ፡ ይለያያል ።

አስቀድመን ፡ ከተናገርናቸው ፡ ሕጎችና ፡ መጻሕፍት ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ የለም ፡ ይኸውም ፡ ስባኪው ፡ ድዮናስዮስ ፡ ከተናገረው ፡ በቀር ፡ ነው ። ምልክቱም ፡ ድ ፡ ይላል ። የጎርጎርዮስም ፡ ምልክቱ ፡ ግር ፡ ይላል ። የዮሐ

ሐ። ወለክርስቶዶሎስ ፡ ዘውእቱ ፡ ገብረ ፡ ክርስቶስ ፡ እም ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ ዘእለ ፡ እስክንድርያ ፡ ትእምርቱ ፡ ክር ስጣ ። ወለጢሞቴዎስ ፡ ትእምርቱ ፡ ጢሞ ።

ወዙሉ ፡ ዘተነግረ ፡ እምቀኖናት ፡ እንዘ ፡ ይፈልጠ ፡ ለካልኡ ፡ ይመውዕዎ ፡ እለ ፡ ይበዝኁ ። ወእለ ፡ ዘልማድ ፡ ዘይደሉ ፡ ለጊዜ ፡ ዘይሰነዐው ፡ ወየኀብር ፡ ምስለ ፡ ልብ ። ዝንቱስ ፡ ቃል ፡ ይከውን ፡ እምቃለ ፡ ፍካሬ ። ወግድፈተ ፡ ቃልስ ፡ ይከውን ፡ እምኢተጠናቅቆ ። ወይደልዎ ፡ ለዘያነብብ ፡ በእዝልፎ ፡ ከመ ፡ ያርትዕ ፡ እምዘተግህደ ፡ በኀቤሁ ።

ተፈጸመ ፡ መቅድም ።



ንስ ፡ አፈወርቅም ፡ ምልክቱ ፡ ሐ ፡ ይላል ። ከእስክንድርያ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ ወገን ፡ የክርቶዶሎስ ፡ ይኸውም ፡ የክርስቶስ ፡ አገልጋይ ፡ ማለት ፡ ነው ። ምልክቱም ፡ ክር ስጣ ፡ ይላል ። የጢሞቴዎስም ፡ ምልክቱ ፡ ጢሞ ፡ ይላል ። ከቀኖናት ፡ ውስጥ ፡ የተነገረው ፡ ሁሉ ፡ ሌላውን ፡ ሲለውጠው ፡ ሲገኝ ፡ የሚበዙት ፡ ያቸንፉታል ። ከጊዜው ጋር ፡ የሚስማሙና ፡ ለልቡና ፡ የሚመጥኑ ፡ የሀገር ፡ ልማዶችም ፡ ያቸንፉታል ። ይኸውም ፡ ቃል ፡ ከትርጓሜ ፡ ቃል ፡ የተገኘው ፡ ነው ። የቃል ፡ ግድፈት ፡ ግን ፡ ከለመጠንቀቅ ፡ የተነሣ ፡ ይሆናል ፡ ዘወትር ፡ ለሚያነብ ፡ ሰው ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ የተገለጠውን ፡ ማቅናት ፡ ይገባዋል ።

መቅድሙ ፡ ተፈጸመ ።

ኍልቈ ፡ አናቅጽ ፡ ዘቀዳማዊ ።

ወኵሉ ፡ ዘቀዳማዊ ፡ ይከውን ፡ ፳ወ፪ቱ ፡ እንቀጽ ፡ በእንተ ፡ ካህናት ፡ ወሕገገ ፡ ቅኔ ፡ ወስብሐት ፡ ለእግዚ አብሔር ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፡ አሜን ።

## ክፍል ቀዳማዊ ።

እንቀጽ ፡ ቀዳማዊ ፡ በእንተ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ወበእ ንተ ፡ ኵሉ ፡ ዘይደሉ ፡ ላቲ ።

፪ ፡ በእንተ ፡ ጥንተ ፡ መጻሕፍት ፡ ውኩፋት ።

፫ ፡ በእንተ ፡ ጥምቀተ ፡ ክርስትና ፡ ወእለ ፡ ይበውኡ ፡ ውስተ ፡ ሃይማኖት ።

፬ ፡ በእንተ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ።

፭ ፡ በእንተ ፡ ኤጲስቆጶሳት ።

፮ ፡ በእንተ ፡ ቀሳውስት ።

፯ ፡ በእንተ ፡ ዲያቆናት ።

፰ ፡ በእንተ ፡ እለ ፡ ተርፉ ፡ ላእካነ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን።

፱ ፡ በእንተ ፡ ካህናት ።

፲ ፡ በእንተ ፡ መነኰሳት ፡ ወመነኰሳይያት ።

፲ወ፩ ፡ በእንተ ፡ ተግሣጽ ፡ ወትእዛዘ ፡ ሕዝብ ።

፲ወ፪ ፡ በእንተ ፡ ቅዳሴ ።

፲ወ፫ ፡ በእንተ ፡ ቍርባን ።

፲ወ፬ ፡ በእንተ ፡ ጸሎት ።

፲ወ፭ ፡ በእንተ ፡ ጾም ።

፲ወ፮ ፡ በእንተ ፡ ምጽዋት ።

፲ወ፯ ፡ በእንተ ፡ ዘይሠየም ፡ ለከፊለ ፡ ምጽዋት ።

፲ወ፰ ፡ በእንተ ፡ ዓሥራት ፡ ወበኵራት ፡ ወብጽዓታት ፡ ወጕልታት ።

፲ወ፱ ፡ በእንተ ፡ እሑዳት ፡ ወበዓላት ።

፳ ፡ በእንተ ፡ ሰማዕታት ፡ ወተእማንያን ፡ ወከሀድያን ።

፳ወ፩ ፡ በእንተ ፡ ድዉያን ።

፳ወ፪ ፡ በእንተ ፡ ሙታን ።

ተፈጸመ ፡ ክፍል ፡ ቀዳማዊ ።

የመጀመሪያው ፡ አንቀጽ ፡ ቍጥር ።

መጀመሪያው ፡ ክፍል ፡ ስለ ፡ ካህናትና ፡ ስለ ፡ አገል ግሎት ፡ ሕጎች ፡ የሚናገር ፡ ፳፪ ፡ አንቀጽ ፡ ነው ። ለእግዚ አብሔር ፡ ምስጋና ፡ ይግባው ፡ ለዘላለሙ ፡ አሜን ።

## መጀመሪያ ፡ ክፍል ።

አንቀጽ ፡ ፩ ፡ ስለ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ስለእርሷ ፡ ስለሚ ገባው ፡ ሁሉ ።

አንቀጽ ፡ ፪ ፡ ሊቀበሏቸው ፡ ስለሚገቡ ፡ ጥንታውያን ፡ መጻሕፍት ።

አንቀጽ ፡ ፫ ፡ ስለ ፡ ክርስትና ፡ ጥምቀትና ፡ ወደ ፡ ሃይማ ኖት ፡ ስለሚገቡ ፡ ሰዎች ።

አንቀጽ ፡ ፬ ፡ ስለ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ።

አንቀጽ ፡ ፭ ፡ ስለ ፡ ኤጲስቆጶሳት ።

አንቀጽ ፡ ፮ ፡ ስለ ፡ ቀሳውስት ።

አንቀጽ ፡ ፯ ፡ ስለ ፡ ዲያቆናት ።

አንቀጽ ፡ ፰ ፡ ስለቀሩት ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ አገልጋ ዮች ።

አንቀጽ ፡ ፱ ፡ ስለ ፡ ካህናት ፡ ሁሉ ።

አንቀጽ ፡ ፲ ፡ ስለ ፡ መነኰሳትና ፡ ስለ ፡ መነኰሳይያት ።

አንቀጽ ፡ ፲፩ ፡ ስለ ፡ ሕዝብ ፡ ትእዛዝና ፡ ተግሣጽ ።

አንቀጽ ፡ ፲፪ ፡ ስለ ፡ ቅዳሴ ።

አንቀጽ ፡ ፲፫ ፡ ስለ ፡ ቍርባን ።

አንቀጽ ፡ ፲፬ ፡ ስለ ፡ ጸሎት ።

አንቀጽ ፡ ፲፭ ፡ ስለ ፡ ጾም ።

አንቀጽ ፡ ፲፮ ፡ ስለ ፡ ምጽዋት ።

አንቀጽ ፡ ፲፯ ፡ ምጽዋትን ፡ ለማደል ፡ ስለሚሾም ።

አንቀጽ ፡ ፲፰ ፡ ስለ ፡ አሥራትና ፡ ስለ ፡ በኵራት ፡ ስለ ፡ ስእለት ፡ ስለ ፡ ጕልቶች ።

አንቀጽ ፡ ፲፱ ፡ ስለ ፡ እሑዶችና ፡ ስለ ፡ በዓላት ።

አንቀጽ ፡ ፳ ፡ ስለ ፡ ሰማዕታት ፡ ስለ ፡ እማንያንና ፡ ስለ ፡ ከሐድያን ።

አንቀጽ ፡ ፳፩ ፡ ስለ ፡ ድዉያን ።

አንቀጽ ፡ ፳፪ ፡ ስለ ፡ ሙታን ።

መጀመሪያው ፡ ክፍል ፡ ተፈጸመ ።

ኍልቈ ፡ አናቅጽ ፡ ዘዳግማዊ ።

ክፍል ፡ ዳግማዊ ፡ በእንተ ፡ ግብራት ፡ ዓላማውያት ፡ ዘምግባና ።

ምግባናሰ ፡ ዘሰብእ ፡ ባሕቲቱ ፡ በሐሳበ ፡ ሰብእና ሁ ፡ መግእዝ ፡ ውእቱ ፡ ዘከመ ፡ መባልዕት ፡ ወአልባስ ፡ ወአብያት ፡ ወአውስቦ ፡ ወሕርመተ ፡ ዕቁባት ።

ወምግባናሰ ፡ ዘበሥርዓታ ፡ ናሁ ፡ አቅደምነ ፡ መብዝኅታ ፡ በአንቀጸ ፡ ተግሣፆሙ ፡ ለሕዝባውያን ፡ ከመ ፡ ይንበር ፡ ብእሲ ፡ ምስለ ፡ ብእሲቱ ፡ ወወልዱ ፡ ወገብሩ ። ወምግባናሰ ፡ ሀገራዊት ፡ ዘከመ ፡ ተናግዶ ፡ ወተፋትሖ ፡ ወኵነኔ ፡ ፍትሕ ፡ ዘበእንተ ፡ አበሳት ፡ ውእቱ ፡ ወኍልቆሙ ፡ ፳ወ፱ቱ ፡ አንቀጽ ፡ ለፍጻሜ ፡ ፶ወ፩ዱ ፡ አንቀጽ ።

፳ወ፫ ፡ በእንተ ፡ መባልዕት ፡ ወአልባስ ፡ ወአብያት ፡ ወተግባራት ።
፳ወ፬ ፡ በእንተ ፡ ሕዩ ፡ ወውሂበ ፡ ንዋይ ፡ ዘአቅሞ ፡ ሰብ ሳብ ፡ ወአውስቦ ።
፳ወ፭ ፡ በእንተ ፡ ሕርመተ ፡ ዕቁባት ።
፳ወ፮ ፡ በእንተ ፡ ሀብት ።
፳ወ፯ ፡ በእንተ ፡ ልቃሕ ፡ ወተሐብዮ ፡ ወአኀዝ ፡ ወአመግቦ ።
፳ወ፰ ፡ በእንተ ፡ ሕስት ፡ ከመ ፡ ልብስ ፡ ወእንስሳ ፡ ወካል እኒሆሙ ።
፳ወ፱ ፡ በእንተ ፡ ምዕቅብና ፡ ንዋይ ፡ ወዘይመስሎ ።

፴ ፡ በእንተ ፡ ምግብና ።
፴ወ፩ ፡ በእንተ ፡ ግብርናት ፡ ወግእዛን ፡ ወእግአዘ ፡ ገብር ።

፴ወ፪ ፡ በእንተ ፡ ሐፃኒ ፡ ዘከመ ፡ ሕቅፈተ ፡ ሕፃን ፡ በኵሉ ፡ ግብሩ ።
፴ወ፫ ፡ በእንተ ፡ ሤጥ ፡ ወተሣይጦ ፡ ወመትሎሆሙ ።

፴ወ፬ ፡ በእንተ ፡ ተሳትፎ ፡ ንዋይ ፡ ወዘይመስሎ ፡ ለዝ ንቱ ፡ ግብር ።
፴ወ፭ ፡ በእንተ ፡ አገብሮ ፡ ወመዓት ።
፴ወ፮ ፡ በእንተ ፡ ተዓስቦ ፡ ቤት ፡ ወውሂበ ፡ ንዋይ ፡ ለም ድር ፡ ዘከመ ፡ ገመታ ።
፴ወ፯ ፡ በእንተ ፡ ሐኒጸ ፡ ሕንፃ ፡ ወዘይተልዎ ።
፴ወ፰ ፡ በእንተ ፡ ልቃሕ ።
፴ወ፱ ፡ በእንተ ፡ ተአምኖ ፡ ኀባውእ ።
፵ ፡ በእንተ ፡ ረኪብ ፡ ዘተገድፈ ፡ እምእንስሳ ፡ ወዘይመ ስሎ ።

የሁለተኛው ፡ አንቀጽ ፡ ቍጥር ።

ሁለተኛው ፡ ክፍል ፡ ዓለማውያን ፡ ስለሆኑ ፡ የአስተዳ ደር ፡ ሥርዓቶች ።

የአስተዳደር ፡ ሹመት ፡ ግን ፡ እካለ ፡ መጠን ፡ ያደረሰና ፡ ጠባዩ ፡ ያማረ ፡ እንደ ፡ መሆኑ ፡ መጠን ፡ የሰው ፡ ብቻ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ እንደ ፡ መብል ፡ እንደ ፡ ልብስ ፡ እንደ ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ ጋብቻ ፡ ያለውና ፡ ከዕቁባት ፡ እንደ ፡ መከ ልከል ፡ ያለውን ፡ ነው ። በየሥርዓቷ ፡ የሆነውን ፡ አስተ ዳደር ፡ ግን ፡ አብዛኛዋን ፡ እነሆ ፡ በሕዝባውያን ፡ ተግ ሣጽ ፡ አንቀጽ ፡ አስቀደምነ ። ወንድ ፡ ከሚስቱና ፡ ከልጁ ከሎሌውም ፡ ጋር ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ። ሀገራዊት ፡ አስተዳ ደር ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ንግድ ፡ እንደ ፡ ፍትሐ ፡ ብሔር ፡ እንደ ፡ ወንጀል ፡ ፍርድ ፡ ያለው ፡ ነው ። ቍጥራቸውም ፡ ፳፱ ፡ አንቀጽ ፡ ነው ። በመጨረሻም ፡ ድምሩ ፡ ፶፩ ፡ አን ቀጽ ፡ ነው ።

አንቀጽ ፡ ፳፫ ፡ ስለ ፡ መብል ፡ ስለ ፡ ልብስ ፡ ስለ ፡ ቤትና ፡ ስለ ፡ ተግባረ ፡ እድ ።
አንቀጽ ፡ ፳፬ ፡ ስለ ፡ ማጨት ፡ ጋብቻን ፡ ለማጽናት ፡ ገንዘብ ፡ ስለመስጠትና ፡ ስለ ፡ ጋብቻ ።
አንቀጽ ፡ ፳፭ ፡ ከዕቁባት ፡ ስለ ፡ መከልከል ።
አንቀጽ ፡ ፳፮ ፡ ስለ ፡ ስጦታ ።
አንቀጽ ፡ ፳፯ ፡ ስለ ፡ ብድር ፡ ስለ ፡ ዋስትና ፡ ስለ ፡ መያዣ ለአስተዳዳሪነት ፡ ስለመሾም ።
አንቀጽ ፡ ፳፰ ፡ እንደ ፡ ልብስና ፡ እንደ ፡ እንስሳ ፡ ያሉት ንና ፡ ሌሎችንም ፡ ስለ ፡ መዋስ ።
አንቀጽ ፡ ፳፱ ፡ ገንዘብን ፡ በአደራ ፡ ስለማስጠበቅና ፡ ስለሚመስለውም ።
አንቀጽ ፡ ፴ ፡ በአስተዳዳሪነት ፡ ስለመሾም ።
አንቀጽ ፡ ፴፩ ፡ ስለ ፡ ባርነት ፡ ስለ ፡ ነፃነት ፡ ባሪያንም ፡ ነፃ ፡ ስለ ፡ ማውጣት ።
አንቀጽ ፡ ፴፪ ፡ ስለ ፡ ሞግዚት ፡ ሕፃንን ፡ በሥራው ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ መከባከብ ።
አንቀጽ ፡ ፴፫ ፡ ስለ ፡ መሸጥና ፡ ስለመግዛት ፡ እነርሱንም ስለሚከተለው ።
አንቀጽ ፡ ፴፬ ፡ ስለ ፡ ሽርክና ፡ ይህንንም ፡ ሥራ ፡ ስለሚ መስለው ።
አንቀጽ ፡ ፴፭ ፡ ስለ ፡ ማስገደድና ፡ ስለቍጣ ።
አንቀጽ ፡ ፴፮ ፡ ቤትን ፡ ስለ ፡ ማከራየት ፡ እንደ ፡ ግምቷ ፡ ስለ ፡ ምድር ፡ ገንዘብን ፡ ስለመስጠት ።
አንቀጽ ፡ ፴፯ ፡ ስለ ፡ ቤት ፡ ሥራና ፡ ስለሚመስለውም ።
አንቀጽ ፡ ፴፰ ፡ ስለ ፡ ብድር ።
አንቀጽ ፡ ፴፱ ፡ ኃጢአትን ፡ ስለ ፡ ማመን ።
አንቀጽ ፡ ፵ ፡ ከእንስሳው ፡ ወገን ፡ የጠፋውን ፡ ስለማግ ኘትና ፡ ስለሚመስለውም ።

ኍልቊ፡ አናቅጽ፡ ዘዳግማዊ።

፺ወ፩፡ በአንተ፡ ጽሒፈ፡ ትእዛዝ፡ በንዋይ።

፺ወ፪፡ በአንተ፡ ርስት።
፺ወ፫፡ በአንተ፡ ፈታሒ፡ ወዘምስሌሁ።
፺ወ፬፡ በአንተ፡ ነገሥት።
፺ወ፭፡ በአንተ፡ ብሉይ፡ ወሐዲስ።
፺ወ፮፡ በአንተ፡ ኵነኔ፡ ከሓድያን።
፺ወ፯፡ በአንተ፡ ቀታልያን።
፺ወ፰፡ በአንተ፡ ተማሣፀ፡ ዝሙት።
፺ወ፱፡ በአንተ፡ ኵነኔ፡ ሰረቅት።
፻፡ በአንተ፡ ኍልቈ፡ ኃጣውእ።
፻ወ፩፡ በአንተ፡ ዘዘዚአሁ፡ ኍልቈ፡ ምግባራት።

ተፈጸመ፡ አንቀጽ፡ ፻ወ፩ዱ።

የሁለተኛው፡ አንቀጽ፡ ቍጥር።

አንቀጽ፡ ፺፩፡ በገንዘብ፡ ላይ፡ ለማዘዝ፡ ኑዛዜ፡ ስለ፡ መጻፍ።
አንቀጽ፡ ፺፪፡ ስለ፡ ርስት።
አንቀጽ፡ ፺፫፡ ስለ፡ ዳኛና፡ ስለ፡ ረዳቶቹ።
አንቀጽ፡ ፺፬፡ ስለ፡ ነገሥታት።
አንቀጽ፡ ፺፭፡ ስለ፡ ብሉይና፡ ስለ፡ ሐዲስ።
አንቀጽ፡ ፺፮፡ ስለ፡ ከሀድያን፡ ቅጣት።
አንቀጽ፡ ፺፯፡ ስለ፡ ነፍሰ፡ ገዳዮች።
አንቀጽ፡ ፺፰፡ ስለ፡ ዝሙት፡ ቅጣት።
አንቀጽ፡ ፺፱፡ ስለ፡ ሌቦች፡ ቅጣት።
አንቀጽ፡ ፻፡ ስለ፡ ኃጢአት፡ ቍጥር።
አንቀጽ፡ ፻፩፡ ስለ፡ ልዩ፡ ልዩ፡ ሥራዎች፡ ቍጥር።

የ፻፩ዱ፡ አንቀጽ፡ እርእስት፡ ተፈጸመ።



በስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዋሕድ ፡ በመለኮት ፡ ዘይሴለስ ፡ በአካላት ፡ ወኩነታት ፡

## አንቀጽ ቀዳማዊ

### በእንተ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ወዘይደሉ ፡ ላቲ ።

፩ ጅ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንሰ ፡ ቤተ ፡ ጸሎት ፡ ይእቲ ፡

፪ በስ ፡ ፺ወ፬ ፡ ወኢይሕንጹ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ዘእንበለ ፡ በትእዛዘ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ወለእመ ፡ ተሀበለ ፡ ፩ዱሂ ፡ ወገብረ ፡ ካልእ ፡ እምዝንቱ ፡ ኢይቅረብ ፡ ቍርባን ፡ በውስቴታ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ፡ ወለእመ ፡ ተሀበለ ፡ ካህን ፡ ዘንተ ፡ ወቀረበ በውስቴታ ፡ ቍርባን ፡ ይትመተር ።

፫ ወከዊን ፡ ሕንፃሃ ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ወሥርዓታ ፡ ህሎ ፡ በውስተ ፡ ክፍል ፡ ዘ፲ወ፰ቱ ፡ ወበ፴ ፡ እምዲድስቅልያ ። ወትኩን ፡ ብርሀተ ፡ በብዙኅ ፡ መኃትው ፡ በአምሳለ ፡ ሰማይ ፡ ወፈድፋደሰ ፡ ጊዜ ፡ ያነብቡ ፡ ክፍላተ ፡ መጻሕፍት ፡ ቅዱሳት ፡ ዘውእቶሙ ፡ ጳውሎስ ፡ ወሐዋርያ ፡ ወግብር ፡ ወወንጌል ፡ መንግሥትስ ፡ ትኩን ፡ ብርሀተ ፡ ጥቀ ።

፬ ጼዋ ፡ ወያኀትዉ ፡ በሰምዕ ፡ ወቀንዲል ፡ ጊዜ ፡ ይቄድስ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ታቦታተ ፡ ምሥዋዕ ፡ ወየሀልዉ ፡ ምስሌሁ ፡ ጊዜ ፡ ቅዳሴሃ ፡ ፯ቱ ፡ ቀሳውስት ፡ ወይኅትዎ ፡ ኪያሃ ፡ በሜሮን ፡ ዘውእቱ ፡ ቅብዐ ፡ ትፍሥሕት ፡ እስመ ፡ ማኅተመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ውእቱ ፡ ይደሉ ፡ ከመ ፡ ይቀድሱ ፡ በውስቴታ ።

፭ ወያንብቡ ፡ ዲበ ፡ምሥዋዕ ፡ ወንጌለ ፡ ዮሐንስ ፡ አምላካዊ ፡ ወኢይቀድሱ ፡ በላዕሌሁ ፡ ቀዳሚ ፡ ዘእንበለ ፡ ይትጋብኡ ፡ ቀሳውስት ፡ ወሊቃውንት ፡ ወኵሎሙ ፡ ዲያቆናት ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ዝንቱ ፡ ክብረ ፡ ወፍሥሐ ።

፮ ወለእመ ፡ ተሰብረ ፡ ምሥዋዕ ፡ አው ፡ ፈለሰ ፡ ይቀድሱ ፡ ዳግመ ፡ ወይኩን ፡ ታቦት ፡ በዘይፈልስ ፡ እመካን ፡ ውስተ ፡ መካን ፡ ከመ ፡ እብነ ፡ ደቂቀ ፡ እስራኤል ፡ ዘፈለሰ ፡ እመካን ፡ ውስተ ፡

በመለኮት ፡ አንድ ፡ በአካላትና ፡ በሁኔታዎች ፡ ፫ ፡ በሆነ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ።

## አንቀጽ፡ ፩ ።

### ስለ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንና ፡ ለእርስዋ ፡ ስለሚገባው ።

፩ ጅ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ግን ፡ የጸሎት ፡ ቤት ፡ ናት ።(ማቴ ፡ ፳፩ ፡ ፲፫ ። ማር ፡ ፲፩ ፡ ፲፯ ) ።

፪ በስ ፡ ፺፬ ። ያለ ፡ ኤጲስቆጶሱ ፡ ትእዛዝ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡ አይሥሩ ። አንድ ፡ ሰው ፡ ስንኳ ፡ ደፍሮ ፡ ከዚህ ፡ ውጪ ፡ ቢሠራ ፡ በውስጥዋ ፡ እስከ ፡ ዘላለም ፡ ቍርባን ፡ አይቅረብ ። ቄሱም ፡ ይህን ፡ ተላልፎ ፡ በውስጥዋ ፡ ቍርባንን ፡ ቢቈርብ ፡ ይሻር ።

፫ የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ አሠራር ፡ ሁኔታና ፡ ሥርዓትዋ ፡ በዲድስቅልያ ፡ በ፲፰ኛውና ፡ በ፴ኛው ፡ ክፍል ፡ ይገኛል ። በሰማይ ፡ አምሳል ፡ በብዙ ፡ መብራቶች ፡ የበራች ፡ ትሁን ። ይልቁንም ፡ የቅዱሳት ፡ መጻሕፍትን ፡ ክፍሎች ፡ በሚያነብቡት ፡ ጊዜ ፡ እነርሱም ፡ ጳውሎስና ፡ ሐዋርያ ፡ የሐዋርያት ፡ ሥራ ፡ ናቸው ፡ ወንጌል ፡ መንግሥት ፡ በሚያነቡበት ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ በጣም ፡ የበራች ፡ ትሁን ።

፬ ጴጥ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ የመሠውያውን ፡ ታቦት ፡ በሚባርክበት ፡ ጊዜ ፡ በሰምና ፡ በዘይት ፡ ያብሩ ። በምትባረክበትም ፡ ጊዜ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ሰባት ፡ ቀሳውስት ፡ ይኑሩ ። የደስታ ፡ ቅባት ፡ በሆነ ፡ በሜሮን ፡ ይትቡዋት ፡ የእግዚአብሔር ፡ ማኅተም ፡ ነውና ። በውስጥዋም ፡ ይቀድሱ ፡ ዘንድ ፡ ይገባል ።

፭ በመሠውያው ፡ (በመንበሩ ፡) ላይ ፡ እምላካዊ ፡ የሆነ ፡ የዮሐንስ ፡ ወንጌልን ፡ ያንብቡ ። ቀሳውስትና ፡ አለቃቸው ፡ ዲያቆናቱም ፡ ሁሉ ፡ ሳይሰበሰቡ ፡ አስቀድመው ፡ በላዩ ፡ አይቀድሱ ፡ ይህ ፡ ደስታና ፡ ክብር ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ።

፮ መሠውያው ፡ ቢሰበር ፡ ወይም ፡ ቢፈልስ ፡ (ቢማረክ ፡ ) ዳግመኛ ፡ ይቀድሱት ፡ ታቦቱ ፡ ከቦታ ፡ ወደ ፡ ቦታ ፡ ይዛወር ፡ እንደነበረው ፡ እንደ ፡ እስራኤል ፡ ልጆች ፡ ታቦት ፡ ከቦታ ፡ ወደ ፡

መካን ።
፯ በስ ፡ ፺ወ፯ ፡ በደስ ፡ ፳ወ፱ ፡ ወመሬተ ፡ ምሥዋ
ዕኒ ፡ ዘይኲስትርዎ ፡ እምኔሁ ፡ ይግድፍዎ ፡
ውስተ ፡ ባሕር ፡ ዘይውኅዝ ፤
፰ ረስጣ ፡ ፳ወ፰ ፡ ወዙሉ ፡ ዘኮነ ፡ እምቤተ ፡ ክርስ
ቲያን ፡ እምንዋይ ፡ ዘተቀደሰ ፡ እመኒ ፡ ንዋየ ፡
ወርቅ ፡ ወብሩር ፡ ኢይደልዎ ፡ ለብእሲ ፡ ከመ ፡
ይትገበር ፡ በሙ ፡ ውስተ ፡ ቤቱ ፡ እስመ ፡
ዝንቱ ፡ ዐሊወ ፡ ሕግ ፡ ውእቱ ፡ ወለእመ ፡ ገብረ ፡
ዘንተ ፡ ይሰደድ ፡ እምድኅረ ፡ ተኰነነ ፡ እምቤተ
ክርስቲያን ።
፱ ረስጣ ፡ ፳ወ፱ ፡ ወዘውፁኦን ፡ እምሃይማኖት ፡
ዳግመ ፡ ሰእመ ፡ ጸንዑ ፡ ዲበ ፡ ምእመናን ፡ ወከ
ልእዎሙ ፡ እምሐዊር ፡ ኀበ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡
ይቀድስ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ውስተ ፡ ቤቱ ። ወለእ
መሰ ፡ ኢተክህለ ፡ ዝንቱ ፡ ከመ ፡ ይትጋብኡ ፡
በበይናቲሆሙ ፡ ውስተ ፡ ፩ዱ ፡ ቤት ፡ አው ፡
ውስተ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ይዘምር ፡ ኵሉ ፡
ለለ፩ዱ ፡ በኀበ ፡ ሀለወ ፡ ውእቱ ፡ ባሕቲቱ ፡ ወያ
ንብብ ፡ ወይጸሊ ።
፲ ዶቅ ፡ ፺ወ፰ ፡ ወኢያዕርጉ ፡ ቍርባነ ፡ ውስተ ፡
አብያቲሆሙ ፡ ለኤጲስ-ቆጶሳት ፡ ወኢኀበ ፡
፩ሂ ፡ እምቤተ ፡ ምእመናን ፡ ዘእንበለ ፡ ኀበ ፡
ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ዘተቀደሰት ፡ ግንር ፡ ፯ ፡
ወእመቦ ፡ ዘተዐደወ ፡ ላዕለ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲ
ያን ፡ ወገብረ ፡ ውስተ ፡ ቤቱ ፡ ግብረ ፡ ቤተ ፡
ክርስቲያን ፡ እንተ ፡ ኢትትገበር ፡ ዘእንበለ ፡
በኀቤሃ ፡ ውጉዘ ፡ ለይኩን ።
፲፩ በደስ ፡ ዘ፳ወ፱ ፡ ወኢይንበር ፡ ፩ሂ ፡ ውስተ ፡
መካነ ፡ ምሥዋዕ ፡ ዘእንበለ ፡ ለጸሎት ፡ ባሕ
ቲታ ፡ ወሰስጊድ ፡ በቅድመ ፡ ምሥዋዕ ። ዘ፲
ወ፱ ፡ ወኢይደልዎ ፡ ለአሐዱሂ ፡ እምእመናን ፡
ለእመ ፡ ኢኮነ ፡ ካህነ ፡ ከመ ፡ ይባእ ፡ ኀበ ፡ ምሥ
ዋዕ ፡ ከመ ፡ ይትመጠው ፡ ቍርባነ ።
፲፪ ዶቅ ፡ ዘ፳ወ፰ ፡ ኢይደሉ ፡ ከመ ፡ ይጸውዑ ፡
ለረፌቅ ፡ ወለምሳሕ ፡ ውስተ ፡ አብያተ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ወታቦታቲሁ ፡ ቅዱሳት ፤ ቆሮንቶስ ፡
ዘ፲ወ፩ ፡ ወኢታስተሐቅሩ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡
ለእግዚአብሔር ፡ ወኢታስተኀፍርዎሙ ፡ ለእለ ፡
እልቦሙ ፡ ምንትኒ ፡ እመብልዕ ፡ ወስቴ ፡ በበ
ሊያትክሙ ፡ ወሰትዮትክሙ ፡ በውስተ ፡ ቤተ ፡

ቦታ ፡ የሚዘዋወር ፡ ይሁን ።
፯ በስ ፡ ፺፯ ። በደስ ፡ ፳፱ ። ከእርሱ ፡ የሚጠርጉ
ትን ፡ የመሠውያውን ፡ አመድ ፡ በፈሳሽ ፡
ባሕር ፡ ውስጥ ፡ ይጣሉት ።
፰ ረስጣ ፡ ፳፰ ። ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ከተባረከ ፡
ዕቃ ፡ ወገን ፡ የሆነውን ፡ ሁሉ ፤ የወርቅና ፡
የብር ፡ ዕቃም ፡ ቢሆን ፡ ሰው ፡ በቤቱ ፡ ውስጥ ፡
ሊሠራባቸው ፡ አይገባውም ። ይህ ፡ ሕግን ፡
ማፍረስ ፡ ነውና ። ይህን ፡ ያደረገ ፡ እንደሆነም ፡
ከተፈረደበት ፡ በኋላ ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡
ይለይ ።
፱ ረስጣ ፡ ፳፱ ፤ ከሃይማኖት ፡ የወጡ ፡ ሰዎች ፤
ዳግመኛም ፡ በምእመናን ፡ ላይ ፡ ቢነሣሡባቸው ፡
ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንም ፡ ከመሄድ ፡ ቢከለክ
ሏቸው ፡ ኤጲስቆጶሱ ፡ በቤቱ ፡ ይቀድስ ። በአ
ንድ ፡ ቤት ፡ ወይም ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ይሰ
በሰቡ ፡ ዘንድ ፡ ባይቻል ፡ ግን ፡ እያንዳንዱ ፡
ብቻውን ፡ በያለበት ፡ ቦታ ፡ ያመስግን ፡ ያን
ብብ ፡ ይጸልይ ።
፲ ዶቅ ፡ ፺፰ ፡ በተቀደሰች ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡
ውስጥ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ በኤጲስቆጶሳት ፡ ቤት ፡
ወይም ፡ በምእመናን ፡ በ፩ዱ ፡ ቤት ፡ ቍርባንን ፡
አያሳርጉ ። ግንር ፡ ፯ ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡
ላይ ፡ የተደፋፈረና ፡ በእርስዋ ፡ ዘንድ ፡ካል
ሆነ ፡ በቀር ፡ ሊደረግ ፡ የማይገባውን ፡ የቤተ ፡
ክርስቲያንን ፡ ሥራ ፡ የሠራ ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡
የተወገዘ ፡ (የተለየ ፡) ይሁን ።
፲፩ በደስ ፡ ፳፱ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ስንኳ ፡ በመሠው
ያው ፡ ቦታ ፡ ውስጥ ፡ ለጸሎትና ፡ በመሠውያው ፡
ፊት ፡ ለመስገድ ፡ ብቻ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ አይ
ቀመጥ ። ፲፱ ፡ ከምእመናንም ፡ ወገን ፡ ለአንዱ ፡
እንኳ ፡ ካህን ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ ወደ ፡ መሠው
ያው ፡ (መቅደስ ፡) ሊገባና ፡ ቍርባንን ፡ ሊቀ
በል ፡ አይገባውም ።
፲፪ ዶቅ ፡ ፳፰ ፡ በቤተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ውስጥና ፡
በተቀደሱት ፡ ታቦቶች ፡ አጠገብ ፡ ግብዣ ፡ ለማ
ድረግ ፡ መጥራት ፡ አይገባም ። ቆሮንቶስ ፡ ፲፪ ፡
(፩ቆሮ ፡ ፲፩ ፡ ፳-፳፪) ። የእግዚአብሔርን ፡ ቤተ ፡
ክርስቲያን ፡ አታቃሉ ፡ አንዱ ፡ የተራበ ፡ ሌላውም
የሰከረ ፡ ሲሆን ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ውስጥ ፡ በመ
ብላታችሁና ፡ በመጠጣታችሁ ፡ ከመብልና ፡ ከመ

ክርስቲያን ፡ እንዘ ፡ እሑዱ ፡ ርኊብ ፡ ወካልኡ ፡
ስኩር ።
፲፫ ዶቅ ፡ ዘ፵ወ፱ ፡ ኢይደልዎን ፡ ለአንስት ፡ በዊአ፡
ነበ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ወኢይጸልያ ፡ ውስቴቱ ።
፳ ፡ ወእደክውኖሙ ፡ ለሠየጥ ፡ ወለመጠል
ባን ፡ ተማይጦ ፡ በውስተ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ።
፲፬ ድስቅ ፡ ዘ፲ወ፪ ፡ ይሰቀብዎሙ ፡ ለአናቅጸ ፡ ቤተ፡
ክርስቲያን ፡ ከመ ፡ ኢይባእ ፡ ኀቤሃ ፡ እደው ፡
እለ ፡ ኢኮኑ ፡ ምእመናነ ፡ እው ፡ ምእመናን ፡
ውጉዛን ፡ እምስታፌ ፡ ምሥጢር ፡ ቅድስት ።

ጠዋ ፡ ወገን ፡ ምንም ፡ የሌላቸውን ፡ አታሳፍሩ
ዋቸው ።
፲፫ ዶቅ ፡ ፵፱ ። ሴቶች ፡ ከመቅደስ ፡ ውስጥ ፡ ገብ
ተው ፡ መጸለይ ፡ አይገባቸውም ። ፳ ። ለሻጮ
ችና ፡ ለለዋጮችም ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡
ውስጥ ፡ መገበያየት ፡ አይገባቸውም ።
፲፬ ድስቅ ፡ ፲፪ ። ምእመናን ፡ ያልሆኑ ፡ ሰዎች ፡
ወይም ፡ ሥጋውንና ፡ ደሙን ፡ ከመቀበል ፡ የተ
ወገዙ ፡ ምእመናን ፡ ወደ ፡ እርስዋ ፡ እንዳይገቡ ፡
የቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡ በሮች ፡ ይጠብቋቸው ።

---

## አንቀጽ ፡ ዳግም ፡

በእንተ ፡ መጻሕፍት ፡ አምላካውያት ፡ ዘእሙንቱ ፡
ተወክፎቶን ፡ ኀበ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ቅድ
ስት ፡ ዘኵልቆሙ ፡ ፹ወ፩ ።

፲፭ ረስጣ ፡ ፫ወ፩ ፡ ረስጠብ ፡ ፶ወ፮ ፡ መጻሕፍት ፡
እንተ ፡ ተወክፍዎን ፡ ምእመናን ፡ ውስተ ፡
ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ መጻሕፍተ ፡ ብሉይ ፡ አሪት ፡
፳፰ቱ ፡ ብሔር ። መጽሐፈ ፡ ኢያሱ ፡ ወልደ ፡ ነዌ፡
፩ ። መጽሐፈ ፡ መሳፍንት ፡ ፩ ። መጽሐፈ ፡ ሩት፡
፩ ። መጽሐፈ ፡ ዮዲት ፡ ፩ ። መጽሐፈ ፡ ነገሥት፡
አርባዕቱ ፡ ቀዳማዊ ፡ ወዳግማዊ ፡ ፩ ፡ መጽሐፍ፡
ሣልስ ፡ ወራብዕ ፡ ፩ ፡ መጽሐፍ ፡ ዐ፪ ፡ ሕሁ
ፃን ። ፪ ፡ መጻሕፍት ፡ ዘእዝራ ፡ ጸሐፊ ፡ አስ
ቴር ፡ ፩ ፡ መጽሐፍ ። ጦቢያ ፡ ፩ ፡ መጽሐፍ ።
ነገረ ፡ መቃብያን ፡ ፪ ፡ መጻሕፍት ። ኢዮብ ፡ ፩ ፡
መጽሐፍ ። መዝሙረ ፡ ዳዊት ፡ ፩ጼ ፡ መጽሐፍ፡
ጥበበ ፡ ሰሎሞን ፡ ፭ቱ ፡ መጻሕፍት ፡ ምሳሌ ፡
ያት ፡ ቆሐልት ፡ መኃልየ ፡ መኃልይ ፡ ጥበብ ፡
ጥበበ ፡ በጕር ።
፲፮ መጻሕፍተ ፡ ነቢያት ፡ ነ፮ቱ ፡ ዐበይትስ ፡ ፬ቱ ፡
ወእሙንቱ ፡ ኢሳይያስ ፡ ወኤርምያስ ፡ ወሕዝቅ
ኤል ፡ ወዳንኤል ። ንኡሳንሂ ፡ ፲ወ፪ቱ ፡ ሆሴዕ ፡
አሞጽ ፡ ሚክያስ ፡ ኢዩኤል ፡ አብድዩ ፡ ዮናስ ፡
ናሆም ፡ እንባቆም ፡ ሶፎንያስ ፡ ሐጌ ፡ ዘካርያስ ፡
ሚልክያስ ።
፲፯ ወሙፅእ ፡ እምእሉ ፡ ጥበበ ፡ ኢያሱ ፡ ወልደ ፡
ሲራክ ፡ ለትምህርተ ፡ ሕፃናት ፡ ወካዕበ ፡
መጽሐፈ ፡ ዮሴፍ ፡ ወልደ ፡ ኮርዮን ፡ ወውእቱ ፡
መጽሐፈ ፡ መቃብያን ።

## አንቀጽ ፪ ።

በቅድስት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሲቀበሏቸው ፡
የታዘዙ ፡ ቍጥራቸው ፡ ፹፩ ፡ የሆኑ ፡ ስለ ፡ አም
ላካውያት ፡ መጻሕፍት ።

፲፭ ረስጣ ፡ ፹፩ ፡ ረስጠብ ፡ ፶፮ ፡ ምእመናን ፡
በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ የተቀበሏቸው ፡ መጻሕ
ፍት ፡ ፰ቱ ፡ ብሔረ ፡ ኦሪት ፡ የነዌ ፡ ልጅ ፡ የኢ
ያሱ ፡ መጽሐፍ ፡ ፩ ፡ የመሳፍንት ፡ መጽሐፍ ፡
፩ ፡ የሩት ፡ መጽሐፍ ፡ ፩ ፡ የዮዲት ፡ መጽሐፍ ፡
፩ ፡ የነገሥት ፡ መጽሐፍ ፡ መጀመሪያውና ፡ ሁለ
ተኛው ፡ ፩ ፡ መጽሐፍ ፡ ሦስተኛውና ፡ አራተ
ኛው ፡ ፩ ፡ መጽሐፍ ፡ ሁለቱ ፡ ሕሁፃን ፡ የጸሐፊው ፡
የዕዝራ ፡ ፪ቱ ፡ መጻሕፍት ፡ አስቴር ፡ ፩ ፡ መጽ
ሐፍ ፡ ጦቢያ ፡ ፩ ፡ መጽሐፍ ፡ መቃብያን ፡ ፪ ፡
መጻሕፍት ፡ ኢዮብ ፡ ፩ ፡ መጽሐፍ ፡ የዳዊት ፡
መዝሙር ፡ ፩ ፡ መጽሐፍ ፡ የሰሎሞን ፡ ጥበብ ፡
፭ ፡ መጻሕፍት ፡ ምሳሌ ፡ ቆሀልት ፡ መኃልየ ፡
መኃልይ ፡ ጥበብ ፡ የባጎር ፡ ጥበብ ።

፲፮ የነቢያት ፡ መጻሕፍት ፡ ፲፮ ፡ ታላላቆቹ ፡ አራት ፡
እነዚህም ፡ ኢሳይያስ ፡ ኤርምያስ ፡ ሕዝቅኤል ፡
ዳንኤል ፡ ናቸው ። ታናናሾቹም ፡ ዓሥራ ፡
ሁለት ፡ እነዚሁም ፡ ሆሴዕ ፡ አሞጽ ፡ ሚክያስ ፡
ኢዩኤል ፡ አብድዩ ፡ ዮናስ ፡ ናሆም ፡ እንባቆም ፡
ሶፎንያስ ፡ ሐጌ ፡ ዘካርያስ ፡ ሚልክያስ ፡ ናቸው።
፲፯ የሲራክ ፡ ልጅ ፡ የኢያሱ ፡ ጥበብ ፡ ለሕፃናት ፡
ትምህርት ፡ ከእሊህ ፡ የተውጣጣ ፡ ነው ። ዳግ
መኛም ፡ የኮርዮን ፡ ልጅ ፡ የዮሴፍ ፡ መጽሐፍ ፡
( ዜና ፡ አይሁድ ፡ ) እለ ፡ እርሱም ፡ የመቃብያን፡
መጽሐፍ ፡ ነው ።

፲፰ መጻሕፍተ ፡ ሐዲስ ፡ ፳፯ቱ ፡ ወንጌላውያን ፡ ሰባክ
ያን ፡ ማቴዎስ ፡ ወማርቆስ ፡ ሉቃስ ፡ ወዮሐ
ንስ ። ፩ዱ ፡ መጽሐፈ ፡ አብርክሲስ ፡ መጽሐፈ ፡
ሐዋርያት ፡ ፯ቱ ፡ መልእክታት ፡ ወእምኔሆሙ ፡
ዘጴጥሮስ ፡ ፪ቱ ፡ ወዘዮሐንስ ፡ ወንጌላዊ ፡ ፫ቱ ፡
መልእክታት ። መልእክተ ፡ ያዕቆብ ፡ ፩ዱ ።
መልእክተ ፡ ይሁዳ ፡ ፩ዱ ። መጽሐፈ ፡ ጳው
ሎስ ፡ ፲ወ፬ቱ ፡ መልእክታት ። መጽሐፈ ፡ አቡ
ቀለምሲስ ፡ ዘዮሐንስ ፡ ወንጌላዊ ፡ ፩ዱ ።

፲፱ እሉንቱ ፡ ሕገጋት ፡ እንተ ፡ አዘዝናክሙ ፡ ባቲ ።
ረስጣ ፡ ፶ወ፰ ፡ ረስጠብ ፡ ፵ወ፩ ። እመቦ ፡ ብእሲ
ዘንሥአ ፡ እመጻሕፍተ ፡ ሐሰት ፡ እንተ ፡ አንበ
ርዋ ፡ ክሐድያን ፡ ወአብአ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ ክር
ስቲያን ፡ እግዚአብሔር ፡ ቅዱስ ፡ ከመ ፡ ይእቲ ፡
መጽሐፈ ፡ እግዚአብሔር ፡ ንጽሕት ፡ በእንተ ፡
ሙስና ፡ ሕዝብ ፡ ይሰደድ ።



፲፰ የሐዲስ ፡ መጻሕፍት ፡ ፳፯ቱ ፡ ወንጌሎች ፡ ሰባክ
ያን ፡ የሆኑ ፡ ማቴዎስ ፡ ማርቆስ ፡ ሉቃስና ፡
ዮሐንስ ፡ የሐዋርያት ፡ ሥራ ፡ ፩ ፡ የሐዋርያት ፡
መጽሐፍ ፡ ፯ ፡ መልእክታት ፡ ከእነርሱም ፡ የጴ
ጥሮስ ፡ ፪ ፡ የወንጌላዊ ፡ ዮሐንስ ፡ ፫ መልእክ
ታት ፡ የያዕቆብ ፡ መልእክት ፡ ፩ ፡ የይሁዳ ፡
መልእክት ፡ ፩ ። የጳውሎስ ፡ መጽሐፍ ፡ ፲፬ ፡
መልእክታት ፡ የወንጌላዊው ፡ የዮሐንስ ፡
ራእይ ፡ ፩ ፡ መጽሐፍ ።

፲፱ እንድትጸኑባቸው ፡ ያዘዝናችሁ ፡ መጻሕፍት ፡
እነዚህ ፡ ናቸው ። ረስጣ ፡ ፶፰ ። ረስጠብ ፡ ፵፩ ።
ከሐድያን ፡ ከአስቀመጧቸው ፡ የሐሰት ፡ መጻ
ፍት ፡ የወሰደና ፡ ንጽሕት ፡ የሆነች ፡ የእግዚአ
ሔር ፡ መጽሐፍ ፡ እንደሆነች ፡ አድርጎ ፡ ሕዝ
ብን ፡ ለማሳሳት ፡ ወደ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፡
ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ያገባ ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡ ይለይ።

---

## አንቀጽ ፡ ሣልስ ፡

### በእንተ ፡ ጥምቀት ፡ ወእለ ፡ ይበውኡ ፡ ኀበ ፡ አሚን ፡

፳ ጥምቀትሰ ፡ ሥሩዕ ፡ ላዕለ ፡ እደው ፡ ወአንስት ፡
ንኡሰሙ ፡ ወዐቢዮሙ ፡ በእንተ ፡ ዘይቤ ፡ እግዚ
እን ፡ ሎቱ ፡ ስብሐት ። ጅ ፡ "ዘኢተወልደ ፡
እማይ ፡ ወእመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ኢይሬእያ ፡ ለመ
ንግሥተ ፡ እግዚአብሔር" ። ወበእንተ ፡ ዘይቤ
ሎሙ ፡ ለአርዳኢሁ ፡ "ሑሩ ፡ ወመሀሩ ፡ ኵሎ ፡
አሕዛበ ፡ ወአጥምቅዎሙ ፡ በስመ ፡ አብ ፡ ወወ
ልድ ፡ ወመንፈስ ፡ ቅዱስ" ። ወቀኖናት ፡ ሥሩ
ዓት ፡ በእንተ ፡ ዝንቱ ።

፳፩ ድስቅ ፡ ፳ወ፩ ፡ ኢያጥምቅ ፡ ዘእንበለ ፡ ኤጲስ
ቆጶስ ፡ አው ፡ ቀሲስ ፡ ወዲያቆናትሰ ፡ ይትለ
አኩ ፡ ምስሌሆሙ ።

፳፪ ጴጥ ፡ ፬ ፡ ወኢይከውኖ ፡ ለ፩ዱሂ ፡ ከመ ፡ ያጥ
ምቅ ፡ በሕልያን ፡ ወኢይሢጥ ፡ ሀብተ ፡ መን
ፈስ ፡ ቅዱስ ፡ በሤጥ ።

፳፫ ድስቅ ፡ ፳ ፡ ወአንስትኒ ፡ ኢያጥምቃ ፡ መነሂ ።

፳፬ ረስጣ ፡ ፵ወ፬ ፡ ወለእመቦ ፡ ብእሲ ፡ ዘተወክፈ ፡
ጥምቀተ ፡ እምዓላውያን ፡ ኢኮነ ፡ ውእቱ ፡
ምእመነ ።

፳፭ ድስቅ ፡ ፴ወ፬ ፡ ዘኒቅያ ፡ ፳ወ፬ ፡ ኢይትወከፉ ፡

## አንቀጽ ሣልስ ።

### ስለ ፡ ጥምቀትና ፡ ወደ ፡ ሃይማኖት ፡ ስለ ሚገቡ ፡ ሰዎች ።

፳ ጥምቀትስ ፡ ለወንዶችም ፡ ለሴቶችም ፡ ለትል
ቆችም ፡ ለትንሾችም ፡ የታዘዘ ፡ ነው ። ጅ ፡
ክብር ፡ ምስጋና ፡ ይግባውና ፡ ጌታችን ፡ በወ
ንጌል ፡ ከውሀና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ያልተወ
ለደ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ አያያ
ትም ፡ ስላለ ። (ዮሐ ፡ ፫ ፡ ፭) ። ለደቀመዛሙር
ቱም ፡ ሂዱና ፡ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡ አስተምሩ ፡
በአብ ፡ በወልድ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ስም ፡
አጥምቋቸው ፡ ስላላቸው ። (ማቴ ፡ ፳፰ ፡ ፲፱) ።
በነዚህም ፡ ሥርዓቶች ፡ ተሠርተዋል ።

፳፩ ድስቅ ፡ ፳፩ ። ከኤጲስቆጶስ ፡ ወይም ፡ ከቄስ ፡
በቀር ፡ ማንም ፡ አያጥምቅ ። ዲያቆናት ፡ ግን ፡
ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ ያገልግሉ ።

፳፪ ጴጥ ፡ ፬ ። ማንም ፡ ሰው ፡ በጉቦ ፡ ሊያጠምቅ ፡
አይገባውም ። የመንፈስ ፡ ቅዱስንም ፡ ሀብት ፡
በዋጋ ፡ አይሸጥ ።

፳፫ ድስቅ ፡ ፳ ። ሴቶች ፡ ማንንም ፡ አያጥምቁ ።

፳፬ ረስጣ ፡ ፵፬ ። ከመናፍቃን ፡ ጥምቀትን ፡ የተቀ
በለ ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡ እማኒ ፡ አይደለም ።

፳፭ ድስቅ ፡ ፴፬ ። ኒቅያ ፡ ፳፬ ። ወንዶች ፡ ሴቶችን ፡

እደው ፡ እንስተ ፡ ወኢእንስት ፡ እደወ ፡ እላ ፡ ይትወከፉ ፡ ተባዕት ፡ ተባዕተ ፡ ወእንስት ፡ ይትወከፋ ፡ እንስተ ።

፳፮ ረስጠብ ፡ ፴ወ፩ ፡ ወይኩን ፡ ጥምቀት ፡ ውስተ ፡ ማይ ፡ ውኂዝ ፡ እው ፡ በማይ ፡ ዘይውኅዝ ፡ ኅበ ፡ ምጥማቅ ፡ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ህየ ፡ ዓጸባ ፡ ይክዓዉ ፡ ማየ ፡ ዘረከቡ ፡ ቀዲሖሙ ፡ ኅበ ፡ ምጥማቅ ።

፳፯ ድስቅ ፡ ፴ወ፪ ፡ ዘሮሜ ፡ ፯ ፡ ወተጠምቆትነሰ ፡ በማይ ፡ ውእቱ ፡ ተሳትፎትነ ፡ በሞተ ፡ ክርስቶስ ፡ ወዕርገትነሂ ፡ እምነ ፡ ማይ ፡ ውእቱ ፡ ካዕበ ፡ አምሳለ ፡ ተንሥኦትነ ፡ ምስሌሁ ።

፳፰ በስ ፡ ፪ወ፲ ፡ ወለእመ ፡ ኢተረክበ ፡ ማይ ፡ ዘይውኅጥ ፡ ርእሶ ፡ ለዘይጠመቅ ፡ ይንሣእ ፡ መጠነ ፡ ፫ቱ ፡ ሕፍን ፡ እምነ ፡ ማይ ፡ ወይሕፅብ ፡ ርእሶ ፡ በስመ ፡ ሥላሴ ።

፳፱ ግር ፡ ወለዘተከህሎ ፡ ጥምቀት ፡ በዕለተ ፡ በጽሐ ፡ ጊዜሁ ፡ ኅበ ፡ ዝንቱ ፡ ኅርየት ፡ ኢያስተድኅሮ ፡ እስከ ፡ ጌሠም ፡ ወኢይጽናሕ ፡ በእንቲአሁ ፡ ብጽሐተ ፡ ወላድያን ፡ ወኢፍቁራን ፡ ወኢያስተድኅር ፡ በምክንያተ ፡ ልብስ ፡ ዘይትሜካሕ ቦቱ ፡ ወኢይጽንሑ ፡ ጥምቀተ ፡ እስከ ፡ ይመጽእ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ እው ፡ ጳጳስ ፡ እው ፡ ኤጲስቆጳስ ፡ እው ፡ ቀሲስ ፡ ባሕቱ ፡ ዘይደልዎ ፡ መባሕት ፡ ለመልእክተ ፡ ኀይለ ፡ ጥምቀት ፡ እስመ ፡ ኀይለ ፡ ጥምቀት ፡ እሐቲ ፡ ይእቲ ፡ በሰረና ። ወዘይትኃሠሥ ፡ በእንቲአሁ ፡ ከመ ፡ ኢይኩን ፡ ካህን ፡ ዘያጠምቆ ፡ ዘነኪር ፡ እምቤተ ፡ ክርስቲያን ። ይቤ ፡ በእንተ ፡ ሐራ ፡ ጥቃ ፡ ዘተግህደ ፡ ዕልወቱ ፡ ወኢይእበይ ፡ ባዕል ፡ ከመ ፡ ኢይጠመቅ ፡ ምስለ ፡ ነዳይ ፡ ወኢ ፡ እግዚእ ፡ ከመ ፡ ኢይጠመቅ ፡ ምስለ ፡ ገብር ።

፴ ረስጠብ ፡ ፴ወ፩ ። ወያዕርቅዎሙ ፡ ወያቅድሙ ፡ እጥምቆ ፡ ሕፃናት ፡ ወዘክህሉ ፡ ተናግሮ ፡ በእንተ ፡ ነፍሶሙ ፡ በባሕቲቶሙ ፡ ይትናገሩ ፡ ወለእመሰ ፡ ኢክህሉ ፡ ተናግሮ ፡ ይትናገሩ ፡ አበዊሆሙ ፡ ህየንቲሆሙ ፡ ለለ፩፩ ፡ ፩ዱ ፡ እው ፡ እምእዝማዲሆሙ ፡ ይትናገሩ ፡ በእንቲአሆሙ ፡ ወድኅረ ፡ ያጥምቅዎሙ ፡ ለእደው ፡ ዓቢያን ፡ ወእምድኅሬሆሙ ፡ ለአንስት ፡ እንዘ ፡ ይፈትሑ ፡ ሥዕርተ ፡ ርእሶን ፡ ወኢያንብራ ፡ እንስት ፡ በእደዊሆን ፡ ሠርጐ ፡ ወርቅ ፡ እንተ ፡ ላዕሌሆን ፡



ሴቶችም ፡ ወንዶችን ፡ ክርስትና ፡ እያንሱ ። ወንዶች ፡ ወንዶችን ፡ ሴቶች ፡ ሴቶችን ፡ ያንሱ ፡ እንጂ ።

፳፮ ረስጠብ ፡ ፴፩ ። ጥምቀት ፡ በወራጅ ፡ ውሀ ፡ ወይም ፡ ወደ ፡ ማጥመቂያው ፡ በሚፈስ ፡ ውሀ ፡ ይሁን ። በዚያ ፡ የውሀ ፡ ችግር ፡ ቢኖር ፡ ያገኙትን ፡ ውሀ ፡ ቀድተው ፡ ወደ ፡ ማጥመቂያው ፡ ያፍስሱ ።

፳፯ ድስቅ ፡ ፴፪ ። ሮሜ ፡ ፯ ። በውሀ ፡ መጠመቃችን በክርስቶስ ፡ ሞት ፡ አንድ ፡ መሆናችን ፡ ነው ። ከውሀውም ፡ መውጣታችን ፡ ሁለተኛ ፡ ከእርሱ ጋር ፡ የመነሣታችን ፡ ምሳሌ ፡ ነው ። ( ሮሜ ፡ ፯ ፡ ፫ - ፳ ። )

፳፰ በስ ፡ ፪፲ ። የሚጠመቀውን ፡ ሰው ፡ ራስ ፡ የሚያጠልቅ ፡ ውሀ ፡ ባይገኝ ፡ እፍኝ ፡ ያህል ፡ ውሀ ፡ ወስዶ ፡ በሥላሴ ፡ ስም ፡ ራሱን ፡ ያጥምቀው ።

፳፱ ግር ። ጊዜው ፡ በደረሰ ፡ ጊዜ ፡ ለመጠመቅ ፡ የተቻለውን ፡ ሰው ፡ ለነገ ፡ እያሳድረው ። የወላጆችን ፡ ወይም ፡ የወዳጆችን ፡ መምጣት ፡ አይጠብቅ ። በሚመካበትም ፡ ልብስ ፡ ምክንያት ፡ እያዘግየው ። ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ወይም ፡ ጳጳስ ፡ ኤጲስቆጳስ ፡ ወይም ፡ ቄስ ፡ ሳይመጣ ፡ አናጠምቅም ፡ እይበሉ ። የማጥመቅ ፡ ሥልጣን ፡ ያለው ፡ ያጥምቀው ፡ እንጂ ። የጥምቀት ፡ ሥልጣን ፡ በትክክል ፡ አንዲት ፡ ናትና ። ስለ ፡ እርሱ ፡ የሚፈለገውስ ፡ የሚያጠምቀው ፡ ካህን ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ የተለየ ፡ እንዳይሆን ፡ ነው ፡ ክህደቱ ፡ ስለታወቀው ፡ ስለ ፡ ሐራ ፡ ጥቃ ፡ እንዲህ ፡ አለ ። ባለጸጋ ፡ ከድሀ ፡ ጋር ፡ አልጠመቅም ፡ እይበል ። ጌታም ፡ ከባሪያ ፡ ጋር ፡ አልጠመቅም ፡ እይበል ።

፴ ረስጠብ ፡ ፴፩ ። ልብሳቸውን ፡ አስወልቀው ፡ ሕፃናቱን ፡ አስቀድመው ፡ ያጥምቋቸው ። እምነትን ፡ ለመናገር ፡ የቻሉት ፡ ራሳቸው ፡ ይናገሩ ። ለመናገር ፡ ካልቻሉ ፡ ግን ፡ ወላጆቻቸው ፡ ስለ ፡ እነርሱ ፡ ለእያንዳንዳቸው ፡ ይናገሩላቸው ። ወይም ፡ ዘመዶቻቸው ፡ ስለነርሱ ፡ ይናገሩ ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ታላላቆቹን ፡ ወንዶች ፡ ያጥምቋቸው ። ከነርሱም ፡ ቀጥሎ ፡ የራሳቸውን ፡ ጠጕር ፡ ፈትተው ፡ ሴቶቹን ፡ ያጥምቋቸው ። ሴቶች ፡ ሲጠመቁ ፡ በእጃቸው ፡ ላይ ፡

ወኢያውርድ ፡ ፩ሂ ፡ ምንተኒ ፡ ነኪረ ፡ ምስሌሁ ፡ ኀበ ፡ ማይ ።

፴፩ በደስ ፡ ፲ወ፱ ፡ ወእለሂ ፡ ይጠመቁ ፡ ይትሐፀቡ ፡ በማይ ፡ በዕለተ ፡ ሐሙስ ፡ እምነ ፡ ሱባዔ ፡ ወይብልዑ ፡ ወይጹሙ ፡ በዕለተ ፡ ዓርብ ። ወለ እመ ፡ ተዳደቃ ፡ ወረከባ ፡ ለብእሲት ፡ ደመ ፡ ትከቶ ፡ ትጽናሕ ፡ እስከ ፡ ትነጽሕ ። ወበዕለተ ፡ ሰንበት ፡ ያስተጋብኦሙ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ለእለ ፡ ይጠመቁ ፡ ወየእዝዞሙ ፡ ከመ ፡ ያድንኑ ፡ አር እስቲሆሙ ፡ መንገለ ፡ ምሥራቅ ። ወይሰፋሕ ፡ እዴሁ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ ወይጸሊ ። ወሶበ ፡ ፈጸመ ፡ እምሕሎቶሙ ፡ ይንፋሕ ፡ ውስተ ፡ ገጸቲሆሙ ፡ ወይዕትብ ፡ አባሎሙ ፡ በዘይከውኑ ፡ ትጉሃነ ፡ በኵሉ ፡ ነገር ፡ ቅዱስ ፡ ወጸሎታት ። ወያቅም ምሙ ፡ ጊዜ ፡ ንቅወተ ፡ ዶርሆ ፡ ኀበ ፡ ማየ ፡ ምጥማቅ ፡ ወኤጲስቆጶስ ፡ ይጸሊ ፡ ላዕለ ፡ ቅብዐ ፡ ዘይት ፡ ዘቦቱ ፡ ያምሕሉ ፡ ወየሀቦ ፡ ለቀሲስ ፡ ወይቁም ፡ መንገለ ፡ ፀጋሙ ፡ ወይጸሊ ፡ ላዕለ ፡ ዘይተ ፡ ቅብዓት ፡ ዘውእቱ ፡ ቅብዐ ፡ እኩቴት ፡ ወየሀቦ ፡ ለካልእ ፡ ቀሲስ ፡ ወያቅሞ ፡ መንገለ ፡ የማኑ ። ወዘያጠምቅዎሂ ፡ ይሚጥ ፡ ገጾ ፡ እም ሥራቅ ፡ መንገለ ፡ ምዕራብ ፡ ውስተ ፡ ሰማይ ፡ ወይክሐዶ ፡ ለዲያብሎስ ። ወ፩ዱ ፡ ቀሲስ ፡ የአ ኀዞ ፡ እዴሁ ፡ ዘየማን ፡ ወይሚጥ ፡ ገጾ ፡ መን ገለ ፡ ምሥራቅ ፡ በአንጻረ ፡ ማይ ፡ ወእምቅድመ ርደቱ ፡ ውስተ ፡ ማይ ፡ ይትአመን ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡ ምእመን ፡ በአብ ፡ ወወልድ ፡ ወመን ፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ወከመዝ ፡ ይጠመቁ ። ወድኅረ ፡ ይትመጠዉ ፡ ቍርባነ ፡ ወኢይጥዐሙ ፡ ምን ተኒ ፡ እንበለ ፡ ይንሥኡ ፡ ምሥጢራተ ፡ ቅድ ሳት ። ወከማሁ ፡ ካልእንኒ ፡ እለ ፡ ጾሙ ፡ ምስሌ ሆሙ ። ወሶበሰ ፡ ተፈጸመ ፡ ቅዳሴ ፡ ለሙ ፡ ሥልጣን ፡ ከመ ፡ ይብልዑ ፡ ዘፈቀዱ ። በስ ፡ ፳ወ፩ ፡ ወይትመጠዉ ፡ ቍርባነ ፡ እምቅድመ ፡ ሕዝብ ።

፴፪ ሥርዋጽ ፡ ፩ዱ ፡ እምቀኖናት ፡ ወዘኮነ ፡ ሎቱ ፡ ወልድ ፡ ወልደ ፡ ዓመት ፡ ዘይልዕል ፡ ወኢያጥ መቆ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ ካህነ ፡ ይትከላእ ፡ እምተል እኮት ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ሕዝባዌ ፡ ይሰደድ ፡ እምቍርባን ፡ ወኢይመጥውዎ ፡ ቍርባነ ፡ እስከ



የወርቅ ፡ ጌጥ ፡ አያድርጉ ፡ ከጌጡ ፡ አንድስ ፡ እንኳ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ወደ ፡ ውሀው ፡ አያውርድ ።

፴፩ በደስ ፡ ፲፱ ። የሚጠመቁትም ፡ ሰዎች ፡ በሱባዔው ፡ ውስጥ ፡ በጸሎተ ፡ ሐሙስ ፡ ዕለት ፡ በውሀ ፡ ይታጠቡና ፡ ይብሉ ፡ በዕለተ ፡ ዓርብ ፡ ግን ፡ ይጹሙ ። ሴቲቱን ፡ የግዳጅ ፡ ደም ፡ ቢመ ታት ፡ እስከትነጻ ፡ ድረስ ፡ ትቈይ ። ኤጲስቆጶስ፡ በዕለተ ፡ እሑድ ፡ የሚጠመቁትን ፡ ሰብስቦ ፡ ራሳቸውን ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ እንዲያዘነብሉ ፡ ይዘዛቸው ። እጁንም ፡ በላያቸው ፡ ዘርግቶ ፡ ይጸልይ ። መሐላውን ፡ እስምሎ ፡ ከፈጸመ ፡ በኋላ ፡ በፊታቸው ፡ ላይ ፡ እፍ ፡ ይበልባቸው ። በተቀደሰ ፡ ነገር ፡ ሁሉና ፡ በጸሎትም ፡ የተጉ ፡ በሚሆኑ ፡ ገንዘብ ፡ አካላቸውን ፡ አማትቦ ፡ ይባርክ ። በዶሮ ፡ ጩኸት ፡ ጊዜ ፡ በመጠመቂያው ፡ ቦታ ፡ ያቁማቸው ። ኤጲስቆጶሱም ፡ መሐላ ፡ በሚያስምልበት ፡ በዘይቱ ፡ ቅብዓት ፡ ላይ ፡ ይጸልይ ። ለቄሱም ፡ ይሰጠው ። በግራ ውም ፡ ይቁም ፡ ይኸውም ፡ ቅብዐ ፡ ቅዱስ ፡ ነው ። በዘይቱም ፡ ቅብዓት ፡ ላይ ፡ ይጸልይ ፤ ለሁለተኛውም ፡ ቄስ ፡ ይሰጠው ። በቀኙም ፡ ያቁመው ። የሚያጠምቁትም ፡ ልጅ ፡ ፊቱን ፡ ከምሥራቅ ፡ ወደ ፡ ምዕራብ ፡ መልሶ ፡ በሰማይ ፡ አንጻር ፡ ዲያብሎስን ፡ ይካደው ። አንዱ ፡ ቄስም ፡ ቀኝ ፡ እጁን ፡ ይዞ ፡ በውሀው ፡ አንጻር ፡ ፊቱን ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ይመልሰው ። ወደ ፡ ውሀ ፡ ከመውረዱም ፡ በፊት ፡ በአብ ፡ በወልድ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ያመነ ፡ መሆኑን ፡ ያረጋግጥ ። እንዲህ ፡ አድርገው ፡ ይጠመቁ ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ይቍረቡ ። ሥጋውንና ፡ ደሙን ፡ ሳይቀበሉ ፡ ምንም ፡ ምን ፡ አይቅመሱ ። እንደ ፡ እነርሱ ፡ የጾሙት ፡ ሌሎቹም ፡ እንዲሁ ፡ ያድርጉ ። ቅዳሴው ፡ ከተፈጸመ ፡ በኋላም ፡ የወደዱትን ፡ እንዲበሉ ፡ መብት ፡ አላቸው ። በስ ፡ ፳፩ ። እነርሱም ፡ ከሕዝቡ ፡ አስቀድሞ ፡ ይቍረቡ ።

፴፪ ሥርዋጽ ፡ ፩ ። ከቀኖናት ፡ የተገኘ ። ዓመት ፡ የሞላው ፡ ልጅ ፡ ከዚያም ፡ ያለፈ ፡ ልጅ ፡ ኖሮት ፡ ያላጠመቀው ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡ ካህን ፡ ቢሆን ፡ ከማገልገል ፡ ይከልከል ። መሃይምን ፡ ቢሆን ፡ ግን ፡ ከሥጋውና ፡ ከደሙ ፡ ይለይ ። እስኪያጠ

ያጠምቆ ።
፴፫ ቀጠግ ፡ ዘ፳ ፡ ወለፅኑሳት ፡ ኢይክልእዎን ፡ እም
ተጠምቆ ፡ በአይኒ ፡ ጊዜ ፡ ዘፈቀዳ ፡ ወአልቦ ፡
ማእከለ ፡ ወላዲት ፡ ወወልዳ ፡ ተሳትፎ ፡ በጥም
ቀተ ፡ ክርስትና ። ዳእሙ ፡ ለኵሉ ፡ ሰብእ ፡ ይደ
ልዎ ፡ ከመ ፡ ይክሥት ፡ አሚኖቶ ፡ በባሕቲቱ ።

፴፬ ሥርዓጽ ፡ ፳ቱ ፡ ወዘተረፈ ፡ እምቀኖናት ፡ ይነ
ግር ፡ ከመ ፡ ለሕፃን ፡ ለእመ ፡ ይፈርሁ ፡ በእንቲ
አሁ ፡ ሞተ ፡ እምቅድመ ፡ ንጽሓ ፡ ለወላዲቱ ፡
እምደመ ፡ ሕርሳ ፡ ለያብእዎ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡
ክርስቲያን ፡ ወያጥምቅዎ ፡ ምስለ ፡ ካልእታ ።
፴፭ ድስቅ ፡ ፴ወ፬ ፡ ወይቅብዓ ፡ ኤጲስቆጳስ ፡ ርእሳ ፡
ለብእሲት ፡ ወዘተርፈ ፡ አባላ ፡ ትቅብዓ ፡ ዲያቆና
ዊት።እስመ ፡ ኢይደሉ ፡ ከመ ፡ ይነጽር ፡ ብእሲ ፡
ዕርቃነ ፡ ብእሲት ። ወነዋ ፡ ተሠርዐ ፡ ዝንቱ ፡
ሕግ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ቅብጣዊት ፡
በመጽሐፈ ፡ ጥምቀት ፡ እንተ ፡ ባሕቲቱ ፡ ዘአስ
ተጋብእዎ ፡ እምቀኖናት ፡ ዘይነግር ፡ ክዋኔሃ ፡
ለጥምቀተ ፡ ክርስትና። ወኵሎሙ ፡ ጸሎታተ ፡
እለ ፡ እሙራን ፡ ባቲ ። ወቦቱ ፡ ያጠምቅዎ ፡
ወይደሉ ፡ ከመ ፡ ይዕቀብዎ ፡ በዐቢይ ፡ ጥንቃቄ።
፴፮ ረስጣ ፡ ፵ወ፫ ፡ ወለዘሂ ፡ ተደለወ ፡ ለተጠምቆ ፡
ይሕትቱ ፡ ግብሮ ።
፴፯ በደስ ፡ ፲ወ፱ ፡ ከመ ፡ በዘመን ፡ ዘተገሠፀ ፡ ቦቱ ፡
ዘተደለዉ ፡ ለተጠምቆ ፡ ለይትኃሠሡ ፡ በእ
ንተ ፡ ገድሎሙ ፡ እንዘ ፡ ይብሉ ፡ ፈጸሙኑ ፡
ኵሎ ፡ ሠናያተ ። ወለእመ ፡ ሰምዐ ፡ ኮንዎሙ ፡
እለ ፡ እምጽእዎሙ ፡ ከመ ፡ እሙንቱ ፡ ገብሩ ፡
ዘንተ ፡ ያስምዕዎሙ ፡ ቃለ ፡ ወንጌል ፡ እምይ
እቲ ፡ ዕለት ፡ ዘእምጽእዎሙ ፡ ባቲ ። ወለእመ ፡
በጽሐ ፡ ዕለት ፡ እንተ ፡ ባቲ ፡ ያጠምቅዎሙ ፡
ያምሕሎሙ ፡ ኤጲስቆጳስ ፡ ለኵሎሙ ፡ ለለ ፡
እሐዱ ፡ እለ ፡ ኮኑ ፡ ሰምዐ ፡ በእንቲአሆሙ ፡
ከመ ፡ ያእምር ፡ እመ ፡ ንጹሓን ፡ እሙንቱ ። ወለ
እመ ፡ ተረክበ ፡ አሐዱ ፡ ዘኢኮነ ፡ ንጹሐ ፡ ይት
ፈለጥ ፡ ወይትገኀሥ ። እስመ ፡ ኢሰምዐ ፡
ውእቱ ፡ ቃለ ፡ በአሚን ።

ምቀውም ፡ ድረስ ፡ ቍርባንን ፡ አይሰጡት ።
፴፫ ቀጠግ ፡ ፳ ። የፀነሱትን ፡ ሴቶች ፡ በወደዱት ፡
በማናቸውም ፡ ጊዜ ፡ ከመጠመቅ ፡ አይከልክሏ
ቸው ። በእናትና ፡ በልጅዋ ፡ መካከል ፡ በጥም
ቀተ ፡ ክርስትና ፡ አንድነት ፡ የለም ። ለሰው ፡
ሁሉ ፡ በየራሱ ፡ እምነቱን ፡ እንዲገልጽ ፡ ይገባ
ዋል ፡ እንጂ ።
፴፬ ሥርዓጽ ፡ ፳ ። እናቱ ፡ ከአራስነት ፡ ደም ፡ ከመ
ንጻትዋ ፡ አስቀድሞ ፡ ይሞታል ፡ ብለው ፡ የሚ
ፈሩትን ፡ ሕፃን ፡ በሞግዚት ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲ
ያን ፡ አግብተው ፡ ማጥመቅ ፡ እንዲገባ ፡ ከቀኖ
ናት ፡ የቀረውን ፡ ይናገራል ።
፴፭ ድስቅ ፡ ፴፬ ። ኤጲስቆጶስ ፡ የሴቲቱን ፡ ራስ ፡
ይቅባ ፤ የቀረውን ፡ ሰውነቷን ፡ ግን ፡ ዲያቆና
ዊት ፡ ትቅባት ፤ ወንድ ፡ የሴትን ፡ ዕርቃን ፡
ያይ ፡ ዘንድ ፡ አይገባምና ። የጥምቀትን ፡ ሁና
ቴና ፡ በእርስዋ ፡ የታወቁትን ፡ ጸሎታት ፡ ከሚ
ናገሩት ፡ መጻሕፍት ፡ በሰበሰቡት ፡ በቅብጣ
ዊት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ መጽሐፈ ፡ ጥምቀት ፡
ውስጥ ፡ ይህ ፡ ሕግ ፡ እነሆ ፡ ተጻፈ ። በእርሱ ፡
ያጥምቁት ። በትልቅ ፡ ጥንቃቄም ፡ ይጠብቁት ፡
ዘንድ ፡ ይገባል ።
፴፮ ረስጣ ፡ ፵፫ ። ለመጠመቅ ፡ የተዘጋጀውን ፡
ሰው ፡ ግብሩን ፡ ይመርምሩት ።
፴፯ በደስ ፡ ፲፱ ። ለአመክሮ ፡ በተወሰነላቸው ፡
ዘመን ፡ በጎ ፡ ነገርን ፡ ሁሉ ፡ ፈጽመዋልን ፡
እያሉ ፡ ስለ ፡ ገድላቸው ፡ ይመርምሩ ። ያመጧ
ቸው ፡ ሰዎች ፡ እነርሱ ፡ ይህን ፡ እንደ ፡ ሠሩ ፡
ምስክር ፡ ቢሆኑዋቸው ፡ ከአመጧቸው ፡ ቀን ፡
ጀምሮ ፡ የወንጌልን ፡ ቃል ፡ ያሰሟቸው ። የሚ
ያጠምቁበትም ፡ ቀን ፡ ቢደርስ ፡ ስለነርሱ ፡
የመሰከሩትን ፡ ሁሉ ፡ ኤጲስቆጶሱ ፡ እያንዳንዳ
ቸው ፡ ያምላቸው ። ንጹሖች ፡ እንደሆኑ ፡
ያውቅ ፡ ዘንድ ። ንጹሕ ፡ ያልሆነ ፡ አንድ ፡ ቢገ
ኝ ፡ ፈጽሞ ፡ ይለይ ። እርሱ ፡ ቃሉን ፡ በሃይማ
ኖት ፡ አልተረዳምና ።



## አንቀጽ ፡ ራብዕ ፡

### በእንተ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ።

፴፰ ወመብዝኅተ ፡ ነገሮሙ ፡ ለኤጲስቆጶሳት ፡ በይደልዎሙ፡ ለሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ እስመ ፡ ይሰመይ፡ ውእቱ ፡ በውስተ ፡ ካልእን ፡ እምቀኖናት ፡ ዘኤጲስቆጶሳት ፡ ዐቢየ ፡ ወቀዳማዌ ፡ ወርእሰ ፡ ኢጲስቆጶሳት ፤ ወውእቱ ፡ ፪ቱ ፡ አክፋል ፡ ሀልው ፡ እመጽሐፍ ፡ ወልብ ።

፴፱ ቀዳማዊ ፡ እመጻሕፍት ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳትሰ ፡ ውእቶሙ ፡ ተላውያነ ፡ ክርስቶስ ፡ ወሐዋርያቲሁ ፡ ዘይቤሎሙ ፡ "ዘኪያክሙ ፡ ተወክፈ ፡ ኪያየ ፡ ተወክፈ" ። ለሊቀ ፡ ጳጳሳትሰ ፡ ሊቅናሁ ፡ ላዕለ ፡ መሢሓውያን ፡ ከመ ፡ ምስፍና ፡ ሙሴ ፡ ላዕለ ፡ እስራኤል ፡ ወማኅበረ ፡ ቅዱሳን ።

፵ ዘኒቅያ ፡ ፴ወ፯ቱ ፡ አዘዙ ፡ ከመ ፡ ይኩኑ ፡ ሊቃነ፡ ጳጳሳት ፡ ውስተ ፡ ኵሉ ፡ ዓለም ፡ ፬ቱ ፡ ባሕቲቶሙ ፡ ከመ ፡ ፬ቱ ፡ መጻሕፍተ ፡ ወንጌል ፡ ወ፬ ፡ አፍላጋት ፡ ወ፬ ፡ ሥርዓተ ፡ ዓለም ፡ ወ፬ ፡ መዓዝኒሁ ፡ ወ፬ ፡ ነፋሳት ፡ ወ፬ ፡ ጠባይዐ ፡ ፍጥረታት ።

፵፩ ወይኩን ፡ ሊቀ ፡ እምኔሆሙ ፡ ወመኰንነ ፡ በዓለ ፡ መንበረ ፡ ጴጥሮስ ፡ ዘሮምያ ፡ በከመ ፡ አዘዙ ፡ ሐዋርያት ። ወእምድኅሬሁ ፡ በዓለ ፡ እስክንድርያ ፡ ዐባይ ፡ ወውእቱ ፡ መንበረ ፡ ማርቆስ ። ወሣልስ ፡ በዓለ ፡ ኤፌሶን ፡ ውእቱ ፡ መንበረ ፡ ዮሐንስ ፡ ቴዎንሎስ ። ወራብዕ ፡ በዓለ ፡ መንበረ ፡ አንጾኪያ ፡ ወውእቱ ፡ መንበረ ፡ ጴጥሮስ ፡ ካዕበ ።

፵፪ ወይትፌለጡ ፡ ኵሎሙ ፡ ኢጲስቆጶሳት ፡ እምታሕተ ፡ እደዊሆሙ ፡ ለአሉ ፡ ፬ቱ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ ወይኩን ፡ ኵሉ ፡ ጳጳስ ፡ እምአላ ፡ አህጉር ፡ ዐበይት ፡ ይሢም ፡ ኤጲስቆጶሳተ ፡ ዘአድያሚሁ ፡ እምታሕተ ፡ እደዊሆሙ ፡ ለጳጳሳት ። ወኢያጳጵስ ፡ ሎቱሰ ፡ አሐዱኒ ፡ እምኤጲስቆጶሳቲሁ ። አስመ ፡ ውእቱ ፡ ይትሌዐል ፡ እምኔሆሙ ። ወይዕቀብ ፡ ኵሉ ፡ ብእሲ ፡ ሥርዓቶ ፡ ወኢይትዐ

## አንቀጽ አራት ።

### ስለ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ።

፴፰ ሰሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ የሚገባውን ፡ የኤጲስቆጶሳትን ፡ አብዛኛውን ፡ ነገር ፡ ይናገራል ። በኤጲስቆጶሳት ፡ አንቀጽ ፡ ውስጥ ፡ ታላቅና ፡ መጀመሪያ ፤ የኤጲስቆጶሳትም ፡ አለቃ ፡ ይባላልና ። ይኸውም ፡ ከመጽሐፍና ፡ ከልብ ፡ የተገኙ ፡ ሁለት ፡ ክፍሎች ፡ አሉት ።

፴፱ መጀመሪያው ፡ ክፍል ፡ ከመጻሕፍት ፡ የተገኘው ፡ ነው ። ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ ግን ፡ የክርስቶስና ፡ እናንተን ፡ የተቀበለ ፡ እኔን ፡ መቀበሉ ፡ ነው ፡ ያላቸው ፡ የሐዋርያት ፡ ተከታዮች ፡ ናቸው ። ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ በክርስቲያኖች ፡ ላይ ፡ ያለው ፡ ሹመቱ ፡ ሙሴ ፡ በ፳ኤል ፡ ላይ ፡ እንደ ነበረው ፡ ምስፍና ፡ ያለ ፡ ነው ።

፵ ኒቅያ ፡ ፴፯ ። ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ በዓለም ፡ ሁሉ ፡ ውስጥ ፡ አራት ፡ ብቻ ፡ እንዲሆኑ ፡ በኒቅያ ፡ የተሰበሰቡ ፡ የቅዱሳን ፡ ማኅበር ፡ አዘዙ ። እንደ ፡ ፬ቱ ፡ የወንጌል ፡ መጻሕፍትና ፡ እንደ ፡ ፬ቱ ፡ ወንዞች ፡ እንደ ፡ ፬ቱ ፡ ሥርዓታተ ፡ ዓለም ፡ እንደ ፡ ፬ቱ ፡ ማዕዝነ ፡ ዓለም ፡ እንደ ፡ ፬ቱ ፡ ነፋሳት ፡ እንደ ፡ ፬ቱ ፡ የፍጥረት ፡ ጠባዮች ።

፵፩ ከእነርሱም ፡ የሮሙ ፡ የጴጥሮስ ፡ በዓለ ፡ መንበር ፡ ሐዋርያት ፡ እንዳዘዙ ፡ አለቃ ፡ ፈራጅም ፡ ይሁን ። ከእርሱም ፡ ቀጥሎ ፡ የታላቂቱ ፡ የእስክንድርያ ፡ በዓለ ፡ መንበር ፡ ይሁን ፤ ይኸውም ፡ የማርቆስ ፡ መንበር ፡ ነው ። ሦስተኛውም ፡ የኤፌሶን ፡ በዓለ ፡ መንበር ፡ ነው ፤ ይኸውም ፡ የነባቤ ፡ መለኮት ፡ የዮሐንስ ፡ መንበር ፡ ነው ። አራተኛው ፡ የአንጾኪያው ፡ በዓለ ፡ መንበር ፡ ነው ፤ ይኸውም ፡ የጴጥሮስ ፡ ሁለተኛው ፡ መንበር ፡ ነው ።

፵፪ ኤጲስቆጶሳት ፡ ሁሉ ፡ በነዚህ ፡ በአራቱ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ ሥልጣን ፡ በታች ፡ ሆነው ፡ ይለዩ ። ጳጳስ ፡ ሁሉ ፡ ከእሊህ ፡ ከታላላቆቹ ፡ አገሮች ፡ የተሾመ ፡ ይሁን ፤ ከጳጳሳት ፡ ሥልጣን ፡ በታች ፡ የሆኑትን ፡ የየአውራጃውን ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ይሹም ፡ ዘንድ ። እርሱን ፡ ግን ፡ ከኤጲስቆጶሳቶቹ ፡ አንዱ ፡ አንኳ ፡ አያጰጵሰው ። እርሱ ፡ ከእነርሱ ፡ ይበልጣልና ። ሰው ፡ ሁሉ ፡ ሥርዓ

ዶሙ ፡ ኀበ ፡ ሥርዓተ ፡ ካልኡ ። ወዘዐለወ ፡ ዘንተ ፡ ሕገ ፡ እንተ ፡ ሠራዕናሃ ፡ ሲኖዶስ ፡ ያወግዞ ።

፴ወ፰ ፡ ወትፍልስ ፡ ሊቀ ፡ ጵጵስና ፡ ኤፌሶን ፡ ኀበ ፡ ሀገረ ፡ ንጉሥ ፡ ከመ ፡ ትኩን ፡ ዛቲ ፡ ክብረ ፡ ለነገሥት ፡ ወለካህናት ፡ ኅቡረ ። ወያከብርዎ ፡ ለኤጲስቆጶስ ፡ ዚአሃ ፡ ወኢያስተሐቅርዎ ፡ በእንተ ፡ ተማኅፆ ፡ ሊቀ ፡ ጵጵስናሁ ፡ እምኔሁ ። ወያከብርዎ ፡ በስም ፡ ሀቢይ ፡ ዘኮቶሊካ ፡ ዘውእቱ ፡ ስመ ፡ ሊቃናት ።

ወያዐብይዎ ፡ ካዕበ ፡ ለበዓለ ፡ መንበረ ፡ ተሰሎንቄ ፡ እስመ ፡ ከመዝ ፡ ይደሉ ።

ወኢይግርር ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ዘኢየሩሳሌም ፡ ለካልኡ ፡ እምኤጲስቆጶሳት ፡ አላ ፡ ያዐብይዎ ፡ ሎቱ ፡ ወያከብርዎ ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ሥዩም ፡ ላዕለ ፡ ሀገር ፡ ቅድስት ፡ ወበእዴሁ ፡ ሀሎ ፡ መስቀለ ፡ እግዚእነ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ወመካነ ፡ ትንሣኤሁ ።

ወያከብርዎ ፡ ካዕበ ፡ ለበዓለ ፡ መንበረ ፡ በግዳድ ፡ ዘውእቱ ፡ ሰልቅ ፡ እንተ ፡ ውስተ ፡ ብሔረ ፡ ምሥራቅ ፡ ወይእቲ ፡ ትሰመይ ፡ ሀገረ ፡ ምድያም ። ወያዐብይዎ ፡ ለዝንቱ ፡ ካዕበ ፡ በስመ ፡ ሊቃናት ፡ ወያብሕዎ ፡ ሎቱኒ ፡ እምይእዜ ፡ ከመ ፡ ያጵጵስ ፡ ጳጳሳተ ፡ በከመ ፡ ይገብሩ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ ከመ ፡ ኢይጸምዉ ፡ ምሥራቃውያን ፡ በሐዊሮቶሙ ፡ ኀበ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳተ ፡ እንጾኪያ ፡ በእንተ ፡ መፍቅዶሙ ። እው ፡ በተመይጦቶሙ ፡ እምኀቤሁ ። እስመ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳተ ፡ እንጾኪያ ፡ ነዋ ፡ ሠምረ ፡ በዝንቱ ፡ እምድኅረ ፡ ሰአልዎ ፡ ሎቱ ፡ ጉባኤ ፡ ማኅበር ፡ ከመ ፡ ኢይኅዝን ፡ በእንተ ፡ ዘተአተተ ፡ እምኔሁ ፡ ሥልጣነ ፡ ምሥራቅ ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ኢኀሠሠ ፡ ዘንተ ፡ ግብረ ፡ ዘእንበለ ፡ ከመ ፡ ያብእሙ ፡ ውስተ ፡ ዕረፍት ፡ ለክርስቲያን ፡ ዘብሔረ ፡ ፋርስ ።

፴ወ፱ ፡ ወለእመ ፡ መጽአ ፡ ግብር ፡ ዘይትጋብኡ ፡ ቦቱ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ውስተ ፡ ብሔረ ፡ ሮም ፡ ወመጽአ ፡ ኀቤሆሙ ፡ በዓለ ፡ ዛቲ ፡ ሢመት ፡ ዘውእቱ ፡ በዓለ ፡ ሰልቅ ፡ እንተ ፡ ይእቲ ፡ እምርት ፡ ሀገረ ፡ በግዳድ ። እስመ ፡ ይእቲ ፡ አመ ፡ ቀዳሚ ፡ ከነ ፡ ትሰመይ ፡ ሳቡር ፡ እንተ ፡ ይእቲ ፡ ዮምሰ ፡ ምድያም ። ለይትለ

ቱን ፡ ይጠብቅ ። ወደ ፡ ሌላም ፡ ሥርዓት ፡ አይተላለፍ ። ይህችን ፡ የሠራናትን ፡ ሕግ ፡ ያፈረሰውን ፡ ሲኖዶስ ፡ ያወግዘዋል ።

፶፫ ኒቅያ ፡ ፴፰ ። የኤፌሶን ፡ ሊቀ ፡ ጵጵስና ፡ ለካህናቱና ፡ ለነገሥታቱ ፡ በአንድነት ፡ ክብር ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ከተማ ፡ (ወደ ፡ ቍስጥንጥንያ፡) ትዛወር ። በእርስዋ ፡ የተሾመውንም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ያክብሩት ። ሊቀ ፡ ጵጵስናው ፡ ከእርሱ ፡ ስለሄደ ፡ አያቃልሉት ። ካቶሊክስ ፡ በሚባለውም ፡ በታላቅ ፡ ስም ፡ ያክብሩት ። ይኸውም ፡ የሊቃናት ፡ ስም ፡ ነው ።

፶፬ ደግመኛም ፡ የተሰሎንቄውን ፡ በዓለ ፡ መንበር ፡ ያክብሩት ፡ እንዲህ ፡ ሊሆን ፡ ይገባልና ።

፶፭ የኢየሩሳሌሙ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ከኤጲስቆጶሳት ፡ ለሌላው ፡ አይታዘዝ ። እርሱን ፡ ፈጽመው ፡ ያክብሩት ፡ እንጂ ። በቅድስት ፡ ሀገር ፡ በኢየሩሳሌም ፡ የተሾመ ፡ ነውና ። በእጁም ፡ የጌታችን ፡ የኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ መስቀልና ፡ የትንሣኤው ፡ ቦታ ፡ አለና ።

፶፮ ደግመኛም ፡ በምሥራቅ ፡ ክፍል ፡ የምትገኘው ፡ ሰልቅ ፡ የምትባለውን ፡ የበግዳድን ፡ በዓለ ፡ መንበር ፡ ያክብሩት ። ይህችውም ፡ የምድያም ፡ አገር ፡ ትባላለች ። ይህንንም ፡ ደግመኛ ፡ በሊቃናት ፡ ስም ፡ ያክብሩት ። ለእርሱም ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ እንደሚሠሩት ፡ ሁሉ ፡ ጳጳሳትን ፡ እንዲሾም ፡ ይፍቀዱለት ። የምሥራቅ ፡ ሰዎች ፡ የፈለጉትን ፡ ነገር ፡ ለማግኘት ፡ ወደ ፡ አንጾኪያው ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ በመሄድና ፡ ከእርሱም ፡ ዘንድ ፡ በመመለስ ፡ እንዳይደክሙ ። የአንጾኪያ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ የምሥራቅ ፡ ሥልጣን ፡ ከእርሱ ፡ በመወገድ ፡ እንዳያዝን ፡ ሠሰቱ ፡ ምእት ፡ ከለመኑት ፡ በኋላ ፡ እነሆ ፡ በዚህ ፡ ተስማምቷል ። የፋርስን ፡ አገር ፡ ክርስቲያኖች ፡ ወደ ፡ ዕረፍት ፡ ሊያገባቸው ፡ ወደደ ፡ እንጂ ፡ እርሱ ፡ ይህን ፡ ክብር ፡ አልፈለገምና ።

፶፯ ኒቅያ ፡ ፴፱ ። ኤጲስቆጶሳት ፡ በሮም ፡ የሚሰበሰቡበት ፡ ሥራ ፡ ቢመጣ ፡ የዚችም ፡ ሹመት ፡ ባለቤት ፡ ወደነርሱ ፡ ቢመጣ ፡ ይኸውም ፡ በግዳድ ፡ በመባል ፡ የታወቀችው ፡ የሰልቅ ፡ በዓለ ፡ መንበር ፡ ነው ፡ እርስዋ ፡ ቀድሞ ፡ ሳቡር ፡ ትባል ፡ ነበርና ፡ ዛሬ ፡ ግን ፡ ምድያም ፡ ትባላለች ። በአቀማመጥ ፡ ከሮም ፡ ጳጳሳት ፡ ሁሉ ፡

ሀል ፡ ወይከበር ፡ ውስተ ፡ መንበር ፡ መልዕልተ ፡ ኵሎሙ ፡ ጳጳሳተ ፡ ሮም ፡ ኅቡረ ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ በመዓርገ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ዘውስተ ፡ ብሔረ ፡ ምሥራቅ ፡ ወይኩን ፡ መንበሩ ፡ ውስተ ፡ መዓርግ ፡ ሳብዕት ፡ እምድኅረ ፡ ኤጲስ ቆጶስ ፡ ዘኢየሩሳሌም ። ወለኵሉ ፡ ዘዐሰወ ፡ ዘንተ ፡ ሕገ ፡ ሲኖዶስ ፡ ያወግዝ ።

፻፰ ዘ፳ ። ወኢያበውሕሙ ፡ ሲኖዶስ ፡ ዐቢይ ፡ ከመ ፡ ይትጋብኡ ፡ በብሔረ ፡ ስልቅ ፡ ከመ ፡ ያንብሩ ፡ ሕገጋተ ፡ ዘእንበለ ፡ በመባሕተ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ዘአንጾኪያ ። እስመ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ ሊቀሙ ፡ በመዓርገ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ በእንተ ፡ ዘኮነሙ ፡ ተባይጸተ ፡ አልበሙ ፡ መባሕት ፡ ከመ ፡ ይፍትሑ ፡ ወይእስሩ ፡ ሕገ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ወኢከመ ፡ ይወስኩ ፡ ውስቴታ ፡ አው ፡ ያሕጽጹ ፡ በምክረ ፡ ርእሶሙ ፡ አላ ፡ ይኩኑ ፡ በእንተ ፡ ኵሉ ፡ ግብር ፡ ግኑዓነ ፡ ለሊቃናት ፡ ወለማኅበረ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ።

፻፱ ሥርዋጽ ፡ ፫ ፡ ወእምድኅረ ፡ ዝንቱ ፡ መንበር ፡ ረበዩ ፡ ሊቀ ፡ ጵጵስና ፡ ዘኤፌሶን ፡ ሰበዓለ ፡ ቍስጥንጥንያ ፡ ወረሰይዎ ፡ ዳግማዌ ፡ በመዓርጊሁ ፡ ወኮነ ፡ እምሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ዘእስክንድርያ ሣልሳየ ።

፻፲ ፺፱ ። ወሰብአ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ኢይሚሙ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ እማእምራኒሆሙ ፡ ወኢበሥምረተ ፡ ርእሶሙ ። እስመ ፡ ጳጳሶሙ ፡ ይከውን ፡ እምታሕተ ፡ እዴሁ ፡ ለበዓለ ፡ እስክንድርያ ፡ ወውእቱ ፡ ዘይደልዎ ፡ ይሚም ፡ ላዕሌሆሙ ፡ ሊቀ ፡ እምኑቤሁ ፡ ዘውእቱ ፡ መትሕተ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ።

፻፲፩ ወሶበ ፡ ተሠይመ ፡ ጵጵስና ፡ ዝንቱ ፡ በገዘኩር ፡ በስመ ፡ ሊቃናት ፡ ኢብወሕ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ያጵጵስ ፡ ጳጳሳተ ፡ በከመ ፡ ያጵጵሱ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ ዳዕሙ ፡ ውእቱ ፡ ባሕቲቱ ፡ ይከብር ፡ በስመ ፡ ሊቀ ፡ ጵጵስና ፡ ዘእንበለ ፡ ይኩን ፡ ሎቱ ፡ ሥልጣነ ፡ ዝንቱ ። ወሰእመ ፡ ኮነ ፡ ግብር ፡ ዘይትጋብኡ ፡ ቦቱ ፡ ጉባኤ ፡ በምድረ ፡ ሮም ፡ ወመጽአ ፡ ኀቤሆሙ ፡ ዝንቱ ፡ ኢትዮጵያዊ ፡ ሰይንበር ፡ ውስተ ፡ መንበር ፡ ሳምን ፡ እምድኅረ ፡ በዓለ ፡ ስልቅ ፡ እንተ ፡ ይእቲ ፡ እም አህጉረ ፡ አድያም ፡ ዘውስቴቶን ፡ ባቢሎን ፡ ወአልዕራቅ ፡ ወመንግሥተ ፡ ሳቡር ፡ እስመ ፡ እብሕዎ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ይሚም ፡ ኤጲስቆጶሳተ ፡

በላይ ፡ ክፍ ፡ ብሎ ፡ በአንድነት ፡ ይከበር ። እርሱ ፡ በምሥራቅ ፡ አገር ፡ ውስጥ ፡ በሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ማዕርግ ፡ ነውና ። መንበሩም ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ በኋላ ፡ ሰባተኛ ፡ ማዕርግ ፡ ይሁን ። ይህን ፡ ሕግ ፡ ያፈረሰውንም ፡ ሲኖዶስ ፡ ያወግዘዋል ።

፻፰ ፍትሃ ፡ ፳ ። ያለ ፡ አንጾኪያው ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ፈቃድ ፡ ሕጎችን ፡ ለመወሰን ፡ በስልቅ ፡ ሀገር ፡ ይሰበሰቡ ፡ ዘንድ ፡ ትልቁ ፡ ሲኖዶስ ፡ አይፈቅድላቸውም ። አለቃቸው ፡ መተካከልን ፡ ስለፈለገ ፡ በሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ ማዕርግ ፡ ቢሆንም ፡ እንኳ ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡ ሕግ ፡ ሊያስሩ ፡ ሊፈቱ ፡ ወይም ፡ በራሳቸው ፡ ምክር ፡ በውስጥዋ ፡ ሊጨምሩም ፡ ሊያሳንሱም ፡ ሥልጣን ፡ የላቸውምና ። በሥራ ፡ ሁሉ ፡ ለአለቆችና ፡ ለማኅበረ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ የተገዙ ፡ ይሁኑ ፡ እንጂ ።

፻፱ ሥርዋጽ ፡ ፫ ። ከዚህም ፡ መንበር ፡ በኋላ ፡ የኤፌሶንን ፡ ሊቀ ፡ ጵጵስና ፡ ለቍስጥንጥንያው ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ አደረጉ ። በማዕርግም ፡ ሁለተኛ ፡ አደረጉት ። የእስክንድርያው ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳትም ፡ ሦስተኛ ፡ ሆነ ።

፻፲ ፍትሃ ፡ ፺፱ ። የኢትዮጵያ ፡ ሰዎች ፡ ከሀዋቂዎቻቸው ፡ ወገን ፡ በራሳቸውም ፡ ፈቃድ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳትን ፡ ለራሳቸው ፡ አይሹሙ ። ጳጳሳቸው ፡ ከእስክንድርያው ፡ በዓለ ፡ መንበር ፡ ሥልጣን ፡ በታች ፡ ነውና ። ከሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ በታች ፡ የሆነውን ፡ ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡ ከእርሱ ፡ ወገን ፡ ሊሾምላቸው ፡ የሚገባውም ፡ እርሱ ፡ ነው ።

፻፲፩ ይህ ፡ በሊቃናት ፡ ስም ፡ የተጠራውም ፡ ጵጵስናን ፡ በተሾመ ፡ ጊዜ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ እንደሚሾሙ ፡ ጳጳሳትን ፡ ይሾም ፡ ዘንድ ፡ አይገባውም ። የመሾም ፡ ሥልጣን ፡ ሳይኖረው ፡ እርሱ ፡ ብቻ ፡ በሊቀ ፡ ጵጵስና ፡ ስም ፡ ይከበር ፡ እንጂ ። በሮም ፡ ጉባኤ ፡ የሚሰበሰቡበት ፡ ሥራ ፡ ቢኖር ፡ ይህ ፡ ኢትዮጵያዊም ፡ ወደ ፡ እነርሱ ፡ ቢመጣ ፡ ከስልቅ ፡ በዓለ ፡ መንበር ፡ በኋላ ፡ በስምንተኛው ፡ መንበር ፡ ይቀመጥ ። ይህችውም ፡ የሳቡር ፡ መንግሥትና ፡ የአልዕራቅ ፡ የባቢሎንም ፡ አውራጃዎች ፡ ክፍል ፡ ናት ። ለአውራጃዎቹ ፡ ኤጲስቆጶሳትን ፡ እንዲሾም ፡ ፈቅደውለታልና ። ኤጲስቆጶሳትም ፡ በራሳ

ለአድያሚ ፡ ዚአሁ ። ወኢ ብዉሕ ፡ ሎሙ ፡ ከመ ፡ ይሢ.ሞዎ ፡ በርእሶሙ ፡ ኤጲስቆጶሳት ።

፶፪ ዘ፶ወ፪ ፡ ወይርአይ ፡ ሊቀ ጳጳሳት ፡ በእንተ ኵሉ ፡ ግብር ፡ ወትእዛዝ ፡ ዘይትገበርዎ ፡ ጳጳሳቲሁ ፡ ወኤጲስቆጶሳቲሁ ፡ ውስተ ፡ በሐውርቲሆሙ ፡ እንተ ፡ ተውህቦሙ ፡ ሳሰሊሆን ። ወለእመ ረከበ ፡ ዲቤሆሙ ፡ ምንተኒ ፡ ግብረ ፡ ዘኢይደሉ ለይወልጦ ፡ ወየአዝዝ ፡ ውስቴቱ ፡ በዘተርእየ ። እስመ ፡ ውእቱ ፡ አቡሆሙ ፡ ለኵሎሙ ። ወእሙንቱኒ ፡ ውሉዱ ፡

፶፫ ወጳጳስሰ ፡ ዘሥዩም ፡ ላዕሌሆሙ ፡ ያክብሩ ፡ ኪያሁ ፡ ከመ ፡ እኁ ፡ ዐቢይ ፡ ዘተሠይመ ፡ ላዕለ ፡ አኃዊሁ ፡ ወመፍትው ፡ ይትአዘዙ ፡ ሎቱ ፡ በእንተ ፡ ሥን ፡ መራሑት ፡ ወሠረዮቱ ።

፶፬ ወሊቀ ጳጳሳትኒ ፡ ከመ አብ በሥልጣኑ ላዕለ ፡ ውሉዱ ፡ ወበከመ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ቦቱ ፡ ትእዛዝ ፡ ወሥልጣን ፡ ላዕለ ፡ ዘታሕተ ፡ እዴሁ፡ ከማሁ ፡ ለበዓለ ፡ መንበረ ፡ ሮሜ ፡ ቦቱ ፡ ሥልጣን ላዕለ ፡ ኵሎሙ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ሊቅ ፡ ከመ ፡ ጴጥሮስ ፡ ዘኮነ ፡ ሎቱ ፡ ሥልጣን ፡ ላዕለ ፡ ኵሎሙ ፡ ሊቃነ ፡ ክርስቲያን ፡ ወማኅበረ ፡ ሰብእ ። እስመ ፡ ውእቱ ፡ ህየንተ ፡ ክርስቶስ ፡ እግዚእነ ፡ ላዕለ ፡ ሕዝቡ ፡ ወአብያተ ፡ ክርስቲያናቲሁ ።

፶፭ ዘ፶ወ፭ ፡ ወይትጋብኡ ፡ ኤጲስቆጶሳተ ኵሉ ፡ አህጉር ፡ ኀበ ፡ ጳጳሶሙ ፡ ፪ተ ፡ ጊዜ ፡ በበዓመት ፡ ከመ ፡ ይርአዩ ፡ ዘይደሉ ፡ በእንቲአሁ ። ወኪያሁ ፡ ለነጽሮ ፡ ከመ ፡ ትኩን ፡ እውሥአቶሙ ፡ ጽንዕተ ፡ እመ ፡ ዕለት ፡ ግርምት ፡ በዘአክሀል ምሙ ፡ ኀይለ ።

፶፮ ዘ፶ወ፮ ፡ ወከማሁ ፡ ጳጳሳትኒ ፡ ወኤጲስቆጶሳት ይትጋብኡ ፡ ኀበ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሶሙ ፡ ምዕረ ፡ በበ ዓመት ፡ በአምሳለ ፡ ውእቱ ፡ በከመ ፡ ኮኑ ፡ ሰብዓ ፡ መሳፍንተ ፡ ደቂቀ ፡ እስራኤል ፡ ያግርኑ ፡ ኀበ ፡ ሙሴ ፡ ኵሎ ፡ ዘበጽበሙ ።

፶፯ ረስጣ ፡ ዘ፩ ፡ ወኢይትፌጸም ፡ ሢመቱ ፡ ለሊቀ ጳጳሳት ፡ ዘእንበለ ፡ በህላዌሆሙ ፡ ለጉባኤ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ወመጥሮጶሊስ ፡ ዘውእቱ ፡ ጳጳስ ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ በእንተ ፡ ሢመቱ ፡ ጋእዝ ይግበሩ ፡ በምክሮሙ ፡ ለእለ ፡ ይበዝኁ ፡ እምኔ



ቸው ፡ ሊሾሙት ፡ አይገባቸውም ።

፶፪ ኒቅያ ፡ ፵፪ ። ጳጳሳቱና ፡ ኤጲስቆጶሳቱ ፡ በተሾሙ ባቸው ፡ አገሮች ፡ ውስጥ ፡ የሚያደርጉትን ፡ ትእዛዝና ፡ ሥራ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳቱ ፡ ይመልከት ። በእነርሱም ፡ ላይ ፡ ማናቸውንም ፡ የማይገባ ፡ ሥራ ፡ ሲሠራ ፡ ቢያገኝ ፡ ይለውጠው ። የተገለጠለትንም ፡ ይዘዝ ። እርሱ ፡ ለሁሉም ፡ አባታቸው ፡ ነውና ፡ እነርሱም ፡ ልጆቹ ፡ ናቸውና ።

፶፫ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ የተሾመውን ፡ ጳጳስ ፡ ግን ፡ በወንድሞቹ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተሾመ ፡ እንደ ፡ ትልቅ ፡ ወንድም ፡ ያክብሩት ፡ መሪና ፡ አስተዳዳሪ ፡ እንደ ፡ መሆኑ ፡ መጠን ፡ ሊታዘዙለት ይገባል ።

፶፬ ሊቀ ፡ ጳጳሳቱም ፡ አባት ፡ በሥልጣኑ ፡ በልጆቹ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ መሆኑ ፡ ያህል ፡ ነው ። ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ከሥልጣኑ ፡ በታች ፡ ባሉት ፡ ላይ ፡ ትእዛዝና ፡ ሥልጣን ፡ አለው ። እርሱ ፡ በክርስቲያኖች ፡ አለቆችና ፡ በሰዎች ፡ ማኅበር ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ሥልጣን ፡ እንዳለው ፡ እንደ ፡ ጴጥሮስ ፡ አለቃ ፡ ነውና ። እርሱ ፡ በሕዝቡና ፡ በአብያተ ፡ ክርስቲያናቱ ፡ ላይ ፡ የጌታችን ፡ የክርስቶስ ፡ ምትክ ፡ ነው ።

፶፭ ኒቅያ ፡ ፶፭ ። የአገሩ ፡ ሁሉ ፡ ኤጲስቆጶሳት ስለእርሱ ፡ የሚገባውን ፡ ይመረምሩ ፡ ዘንድ እርሱንም ፡ ለማየት ፡ በየዓመቱ ፡ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ ከጳጳሳቸው ፡ ዘንድ ፡ ይሰብሰቡ ። ስለ ፡ ተሰጣቸው ፡ ሥልጣን ፡ በምታስፈራዋቸ ፡ ቀን መልሳቸው ፡ የጸናች ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ።

፶፮ ኒቅያ ፡ ፶፮ ። እንዲሁም ፡ ጳጳሳትና ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ሰብዓው ፡ የደቂቀ ፡ እስራኤል ፡ መሳፍንት ፡ የቸገራቸውን ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ሙሴ ፡ ያቀርቡ ፡ እንደነበረ ፡ በዚሁ ፡ አምሳል ፡ በየመቱ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ከሊቀ ፡ ጳጳሳቸው ፡ ዘንድ ፡ ይሰብሰቡ ።

፶፯ ረስጣ ፡ ፩ ። የሊቀ ፡ ጳጳሳቱ ፡ ሹመት ፡ የኤጲስቆጶሳትና ፡ የመጥሮጶሊስ ፡ (ይኸውም ፡ ጳጳስ ፡ ማለት ፡ ነው ።) ጉባኤ ፡ ሳይሆን ፡ አይፈጸምም ። ስለ ፡ ሹመቱ ፡ ጠብ ፡ ክርክር ፡ ቢሆን ፡ በድ

ሆሙ ። ወእምዝ ፡ ዘይደልዎ ፡ ይሠየም ፡ ላዕሌሆሙ ።

፶፰ ዘኒቅያ ፡ ዘ፴ወ፮ ፡ ወለይትአዘዝ ፡ በዓለ ፡ ኵሉ ፡ ሀገር ፡ ወብሔር ፡ እመኒ ፡ ኮነት ፡ ዐባየ ፡ አው ፡ ንእስተ ፡ ዘትከውን ፡ ታሕተ ፡ እዴ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ይሥርዐ ፡ በረከተ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ በአምጣነ ፡ ትክል ፡ ወይፈንዉ ፡ ኪያሃ ፡ ኀቤሁ ፡ በበኵሉ ፡ ዓመት ፡ ከመ ፡ ይትረዳእ ፡ ባቲ ፡ ወዝንቱ ፡ አንቀጽ ፡ ዘእንበለ ፡ ግዘት ።

፶፱ ዘ፺ወ፱ ፡ ኢይበውሕ ፡ ለጳጳስ ፡ ወለኤጲስቆጶሳቲሁ ፡ ሐቲተ ፡ አበሳቲሁ ፡ ለዘአበሰ ፡ እምኤጲስቆጶሳት ፡ እለ ፡ ታሕተ ፡ እዴሁ ፡ ወፈቲሐ ፡ ፍትሕ ፡ ላዕሌሁ ፡ ወኢተወከፎተ ፡ ንስሓሁ ፡ ዘእንበለ ፡ መባሕተ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ምስሌሆሙ ፡ ወበአእምሮቱ ፡ ወትእዛዘ ፡ ዚአሁ ።

፷ ዘ፶ ፡ ወኢይትወከፉ ፡ ላዕለ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ውዴተ ፡ አሐዱ ፡ ጳጳስ ፡ ምንትኒ ፡ እምጳጳሳቲሁ ፡ እለ ፡ ታሕተ ፡ እዴሁ ፡ አው ፡ ለእመ ፡ ተረከበ ፡ በላዕሌሁ ፡ ምንትኒ ፡ እምአበሳት ፡ ዘእንበለ ፡ ይምጻእ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ካልእ ፡ እምእኅዊሁ ፡ እም፫ቲሆሙ ፡ ወነጽሮቶሙ ፡ ግብሮ። ወኢይደሉ ፡ ለአሐዱሂ ፡ እምሠለስቲሆሙ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ ለአበተዋድዮ ፡ ከመ ፡ ያብሕ ፡ ሎቱ ፡ በእንተ ፡ ውእቱ ፡ አው ፡ ይስነአዉ ፡ ላዕሌሁ ፡ ዘእንበለ ፡ መባሕተ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ካልእ ፡ እምእኅዊሁ ፡ ወነጽሮቶሙ ፡ ግብሮ ፡ በከመ ፡ አቅደምነ ፡ ነጊረ ።

፷፩ ዘ፶ወ፩ ፡ ወኢይደሉ ፡ ለአሐዱሂ ፡ እምሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ ወጳጳሳት ፡ ወኤጲስቆጶሳት ፡ ከመ ፡ ይፍታሕ ፡ ዘአሰሮ ፡ ካልኡ ፡ ዘእንበለ ፡ እምድኅረ ፡ ሞቱ ። ወሊቀ ፡ ጳጳሳትሰ ፡ ብዉሕ ፡ ውእቱ ፡ እምድኅረ ፡ ተከሥቶ ፡ ከመ ፡ ይፍታሕ፡ ማእሰሮሙ ፡ ለእሉ ፡ ኵሎሙ ፡ ሶበ ፡ ርእየ ፡ ዝከተ ። እስመ ፡ ውእቱ ፡ ከመ ፡ እግዚእ ፡ ቤት ፡ በላዕሌሆሙ ፡ ወላዕለ ፡ ኵሉ ፡ ክቡር ።

፷፪ ዘ፳ወ፮ ፡ ወለእመ ፡ ሢመ ፡ ጳጳስ ፡ አሐደ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ እምኤጲስቆጶሳት ፡ ለይፈኑ ፡ ምስሌሁ ፡ ካዕበ ፡ ኮሬ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ከመ ፡ ያብእ ፡ ሎቱ ፡ ኀበ ፡ ሀገሩ ፡ ወቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ ወያንብሮ ፡ በዕለተ ፡ ቀዳሚት ፡ ጊዜ ፡ በእቱ ፡ ዲበ ፡ መንበር ፡ ወሶበ ፡ ነበረ ፡ ውስተ ፡ ሀገሩ ፡ ፫ተ ፡



ምዕ ፡ ብልጫ ፡ ያድርጉት ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ የሚገባው ፡ በላያቸው ፡ ይሾም ።

፶፰ ኒቅያ ፡ ፴፮ ። ከተማውና ፡ ባላገሩ ፡ ሁሉ ፡ ይታዘዝ ። በሊቀ ፡ ጳጳሳቱ ፡ ሥልጣን ፡ በታች ፡ ያለች ፡ አገር ፡ ታላቅም ፡ ታናሽም ፡ ብትሆን ፡ ለሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ የሚሰጥ ፡ ገጸ ፡ በረከት ፡ የምትችለውን ፡ ያህል ፡ ይሥሩባት ። በእርሰዋም ፡ ይረዳባት ፡ ዘንድ ፡ ባያመቱ ፡ ወደእርሱ ፡ ይላኩዋት ። ይህ ፡ አንቀጽ ፡ ውግዘት ፡ የሌለበት ፡ ነው ።

፶፱ ኒቅያ ፡ ፺፱ ። ለጳጳስና ፡ ለኤጲስቆጶሳቱ ፡ ከሥልጣኑ ፡ በታች ፡ ካሉት ፡ ከኤጲስቆጶሳቱ ፡ ወገን፡ የበደለውን ፡ በደል ፡ መመርመርና ፡ በእርሱም ፡ መፍረድ ፡ በሊቀ ፡ ጳጳሳቱም ፡ ፈቃድ ፡ ካልሆነና ፡ እውቆ ፡ ካላዘዘ ፡ በቀር ፡ ኑዛዜ ፡ መቀበል ፡ አይገባቸውም ።

፷ ኒቅያ ፡ ፶ ። በሊቀ ፡ ጳጳሳቱ ፡ ላይ ፡ ከሥልጣኑ ፡ በታች ፡ ካሉት ፡ ከጳጳሳቱ ፡ ወገን ፡ የሚቀርበውን ፡ የአንዱን ፡ ጳጳስ ፡ ነገረ ፡ ሥራ ፡ (ክስ) ፡ ምንም ፡ አይቀበሉ ። ከበደል ፡ ወገን ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ቢገኝም ፡ ከሦስቱ ፡ ወንድሞቹ ፡ ሌላው ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ሳይመጣና ፡ ሥራውን ፡ ሳይመረምሩ ፡ አይቀበሉ ። ከሦስቱ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳትም ፡ ለአንዱ ፡ እንኳ ፡ እርሱን ፡ ለማጣላት ፡ እንዲያስናብተው ፡ ወይም ፡ እንዲስማሙበት ፡ ሊያደርግ ፡ አይገባውም ። አስቀድመን ፡ እንደ ፡ ተናገርን ፡ ሥራውን ፡ ከመመርመራቸውና ፡ ከወንድሞቹ ፡ ወገን ፡ የሆነ ፡ በሌላው ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ፈቃድ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ።

፷፩ ኒቅያ ፡ ፶፩ ። ከሊቃነ ፡ ጳጳሳትና ፡ ከጳጳሳት ፡ ከኤጲስቆጶሳትም ፡ ለአንዱስ ፡ እን... ፡ ሌላው ፡ ያወገዘውን ፡ መፍታት ፡ አይገባውም ። ከሞተ ፡ በኋላ ፡ ነው ፡ እንጂ ። ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ግን ፡ ይህን ፡ በመረመረ ጊዜ ፡ ከተገለጠለት ፡ በኋላ ፡ የሁሉንም ፡ ግዝት ፡ ሊፈታ ፡ ሥልጣን ፡ አለው ። እርሱ ፡ በነርሱ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ባለቤት ፡ ነውና ። በሁሉም ፡ ላይ ፡ ክቡር ፡ ነውና ።

፷፪ ኒቅያ ፡ ፳፮ ። ጳጳሱ ፡ ከኤጲስቆጶሳት ፡ ወገን ፡ አንዱን ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ቢሾም ፡ ወደ ፡ ሹመት ፡ ሀገሩና ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ያስገባው ፡ ዘንድ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ኮሬ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ (ቆሞስ) ፡ ይላክ ። በገባ ፡ ጊዜም ፡ በዕለተ ፡ ቀዳሚት ፡ በወንበሩ ፡ ያስቀምጠው ። በአገሩ ፡

አውራኅ ፡ ይሑር ፡ ኀበ ፡ ጳጳስ ፡ የሐውጾ ፡ በእንተ ፡ እምነቶ ፡ ወየአዝዞ ፡ ጳጳስ ፡ ለኵሉ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ አሙ ፡ ለርእሰ ፡ ካህናት ፡ አሙ ፡ ለርእሰ ፡ ዲያቆናት ፡ ይፍትንዎ ፡ ሕገ ፡ ኤጲስ ቆጳሳት ፡ ወቁመቶ ፡ ላዕለ ፡ ውሳኔያተ ፡ እሉ ፡ ኵሎሙ ። ወለእመ ፡ ረከብዎ ፡ ዘንዋ ፡ በቀበሙ ፡ ፍጹመ ፡ እሚሃ ፡ ያስተጸንዕ ፡ ግብሮ ፡ ወያብሖ ፡ ሎቱ ፡ ቀዊመ ፡ በኤጲስቆጶስናሁ ፡ ወይትወከፉ ፡ ትእዛዛቲሁ ። ወከማሁ ፡ ካዕበ ፡ ለይገበሩ ፡ ጳጳሳት ፡ በሊቃነ ፡ ጳጳሳቲሆሙ ። እሌ ፡ ሎቱ ፡ ለዘየዐሉ ፡ ዘንተ ፡ ሕገ ፡ ወሲኖዶስ ፡ ያወግዞ ።

፳፫ ዘኒቅያ ፡ ፵፱ ፡ ወኢይትበዋሕ ፡ አሐዱኒ ፡ እምኤጲስቆጳሳት ፡ እለ ፡ ታሕተ ፡ እደዊሆሙ ፡ ለጳጳሳት ፡ እምኀበ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ በምንትኒ ፡ ዘእንበለ ፡ በትእዛዘ ፡ ጳጳሶሙ ፡ ወእጠይቆቶ ፡ በዝንቱ ፡ ወኢይኅሥሥ ፡ መኑሂ ፡ እምጳጳሳት ፡ ወእምኤጲስቆጳሳት ፡ በዊአ ፡ ኀበ ፡ ንጉሥ ፡ ዘእንበለ ፡ መባሕተ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ። ወለዘ ፡ ዘዐለወ ፡ ዘንተ ፡ ሲኖዶስ ፡ ያወግዞ ።

፳፬ ረስጠጅ ፡ ፴ወ፩ ፡ ወኤጲስቆጳሳት ፡ ኵሉ ፡ እድ ያም ፡ ይኅልዎሙ ፡ ከመ ፡ ያእምሩ ፡ መኑ ፡ ውእቱ ፡ ሊቆሙ ፡ ወይረስይዎ ፡ ሎሙ ፡ ከመ ፡ ርእስ ፡ ወኢይግበሩ ፡ ምንተኒ ፡ ግብረ ፡ ዐቢየ ፡ ወንኡሰ ፡ ዘእንበለ ፡ በምክሩ ፡ ወውእቱኒ ፡ ካዕበ ፡ ኢይግበር ፡ ግብረ ፡ ዐቢየ ፡ ዘእንበለ ፡ በምክረ ፡ ኤጲስቆጳሳት ፡ ኵሎሙ ፡ ከመ ፡ ይኩኑ ፡ በአሐዱ ፡ ኅብረት ።

፳፭ ዳግማዊኒ ፡ ልሁናዊ ። ሊቀ ፡ ጵጵስና ፡ ሀየንተ ፡ ክርስቶስ ፡ ውስተ ፡ ዓለም ፡ በእንተ ፡ ዐቂበ ፡ ሃይማኖት ፡ ወመግቦተ ፡ መሃይምናን ፡ በግብረ ፡ ሕጋዊት ፡ መንፈሳዊት ። ወሢመት ፡ ዘይቀውም ፡ ባቲ ፡ ትእዛዝ ፡ ሥሩዕ ፡ ላዕለ ፡ መሃይምናን ፡ ወድልው ፡ ላዕለ ፡ ኵሎሙ ፡ ወይኤምር ፡ በእንቲአሁ ፡ ሕግ ፡ ወክዊን ፡ ግእዝ ። ቀዳማዊስ ፡ በእንተ ፡ ዘተሠይመ ። ወዳግም ፡ በእንተ ፡ ግእዝ ፡ ጠባይዕ ፡ ዘለባውያን ፡ ከመ ፡ ይኅሥሡ ፡ ሊቀ ፡ ዘይመርሖሙ ፡ ኀበ ፡ እእምሮ ፡ ፍኖተ ፡ ጽድቅ ፡ ወገቢረ ፡ ሠናይ ፡ ወእምተወፍዮት ፡ ኀበ ፡ ርእስ ፡ ዘይከልእሙ ፡ እምህምያት ። ወይፈትሕ ፡ ማእከሌሆሙ ፡ በእንተ ፡ ተጋእቦተ ፡ ወተጸልኦት ።



ሦስት ፡ ወር ፡ ከተቀመጠ ፡ በኋላ ፡ እጅ ፡ ለመንሳት ፡ ወደ ፡ ጳጳሱ ፡ ይሂድ ። ጳጳሱም ፡ የኤጲስ ቆጳሳትን ፡ ሕግጋት ፡ መፈጸሙንና ፡ በእነርሱም ፡ መጽናቱን ፡ ይፈትኑት ፡ ዘንድ ፡ ቆሞሱን ፡ ወይም ፡ ሊቀ ፡ ካህናቱን ፡ ወይም ፡ ሊቀ ፡ ዲያቆናቱን ፡ ይዘዝ ። ፈጽሞ ፡ ጠብቋቸው ፡ ቢያገኙት ፡ ያንጊዜ ፡ ሥራውን ፡ ያጽናለት ። በኤጲስቆጶስነቱም ፡ እንዲጸናና ፡ ትእዛዞቹን ፡ እንዲቀበሉት ፡ ያሠልጥነው ። ጳጳሳትም ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳቶቻቸው ፡ እንዲሁ ፡ ያድርጉ ። ይህን ፡ ሕግ ፡ ለሚያፈርስ ፡ ሰው ፡ ወዮለት ። ሲኖዶስም ፡ (ጉባኤ) ፡ ያወግዘዋል ።

፳፫ ኒቅያ ፡ ፵፱ ። ከጳጳሳት ፡ ሥልጣን ፡ በታች ፡ ካሉት ፡ ከኤጲስቆጳሳት ፡ ወገን ፡ አንዱ ፡ እንኳ ፡ ጳጳሳቸው ፡ ሳያዝና ፡ ሳይፈቅድ ፡ ወደ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳቱ ፡ ሊሄድ ፡ አይገባውም ። ከጳጳሳትና ፡ ከኤጲስቆጳሳትም ፡ ወገን ፡ ማንም ፡ ቢሆን ፡ ያለ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳቱ ፡ ፈቃድ ፡ ከንጉሥ ፡ ዘንድ ፡ መግባትን ፡ አይፈልግ ። ይህን ፡ ሕግ ፡ ያፈረሰውን ፡ ሁሉ ፡ ሲኖዶስ ፡ ያወግዘዋል ።

፳፬ ረስጠጅ ፡ ፴፩ ። የአውራጃው ፡ ሁሉ ፡ ኤጲስ ቆጳሳት ፡ አለቃቸው ፡ ማን ፡ እንደሆነ ፡ ማወቅ ፡ ይገባቸዋል ። እንደ ፡ አለቃም ፡ ያድርጉት ። ታላቅ ፡ ታናሽም ፡ ሥራ ፡ እርሱን ፡ ሳያማክሩ ፡ አይሥሩ ። እርሱም ፡ ደግሞ ፡ ያለ ፡ ኤጲስቆጳሳቱ ፡ ምክር ፡ ታላቅ ፡ ሥራ ፡ አይሥራ ። ሁሉም ፡ እንዲህ ፡ በአንድ ፡ ስምምነት ፡ ይሁኑ ።

፳፭ ሁለተኛው ፡ ክፍል ፡ ከልብ ፡ የኑቃ ፡ ነው ። ሊቀ ፡ ጵጵስና ፡ ሃይማኖትን ፡ ስለ ፡ መጠበቅና ፡ ምእመናንን ፡ በመንፈሳዊና ፡ በሕጋዊ ፡ ሥራ ፡ ለማስተዳደር ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ስለ ፡ ክርስቶስ ፡ ነው ። ሹመቱ ፡ የሚጸናበትም ፡ ትእዛዝ ፡ በምእመናን ፡ ላይ ፡ ተሠርታለች ። በሁሉ ፡ ላይም ፡ ተዘጋጅታለች ። ስለእርሱም ፡ ሕግና ፡ ልማድ ፡ ያስረዳል ። መጀመሪያው ፡ ስለ ፡ ተሾመው ፡ ይናገራል ። ሁለተኛውም ፡ ስለ ፡ አዋቂዎች ፡ ልማዳዊ ፡ ጠባይ ፡ የሚናገር ፡ ነው ። ወደ ፡ እውነት ፡ መንገድና ፡ ወደ ፡ መልካም ፡ ሥራ ፡ የሚመራቸውን ፡ አለቃ ፡ ይፈልጉ ፡ ዘንድ ። ከበደል ፡ የሚከለክላቸው፣ በጠብና ፡ በክርክር ፡ ጊዜ ፡ በመካከላቸው ፡ የሚፈርድ ፡ አለቃ ፡ ከመቀበላቸው ፡ የተነሣ ።

፳፭ ወሶበ ተሰየመ ዘይደልዎ ይትረከብ
ቀዊም በትእዛዝ ወይልወት ላዕለ ሰብእ
እለ የኀርዩ ፈደፋደ ። ከመ ይኅረዩ ሊተ
ለሕዝብ ። ወትእዛዛቲሁ ፡ ድልዋት ፡ ላዕለ ፡
ሰብእ እለ የኀርዩ ፡ ፫ቱ ጾታ እማንቱ ፡
እሉቱ እምአሆን እእምሮ ርትዕ ፡ እንተ
ዘከርነ ውስተ አንቀጸ ለማሰት ። ወካልእ
ታቲ ፡ እእምሮ ፡ ከመ ፡ ይብጽሑ ፡ በቱ ፡ ኀበ ፡
ጥያቄ ፡ እእምሮቱ ፡ ለዘትደልዎ ፡ ዛቲ ፡ ሢመት ፡
ወማልሰታ ፡ ከመ ፡ ያጥርዩ ፡ ምክረ ፡ ወጥበበ ፡
እለ ፡ ይመርሑ ፡ ኀበ ፡ ኅሪዮቱ ፡ ለዘመኑ ፡
ውእቱ ፡ ዘይበቍዕ ፡ ለሰብእ ፡ ዝንቱ ፡ መዋ
ዕል ፡ ወዘይኄይስ ፡ ለሕግ ፡ ወምርሐቶሙ ፡ ዘያ
ቀውም ፡ ወይኤምር ።

፳፮ ወትእዛዛት ለዘይደልዎ ሎቱ ፪ቱ ክፍል
እመጻሕፍት ፡ ወነዋ ፡ ተዘክረት ፡ በውስተ ፡
ቀዳሚት ፡ አንቀጸ ፡ ኢጲስቆጶስ ። ወበእንተ ፡
ልቡናሁ ፡ ወይእቲ ፡ ፬ቱ ፡ ጾታ ። ቀዳሚሃ ፡
ሰላም ፡ ወድኅነት ልብ ፡ ወአሃለ እንተ
ኢይትከሃል ፡ ዘእንበሌሆን ፡ ቀዊም ፡ በሊቅና ፡
ዘውእቶን ፡ ርእይ ፡ ወሰሚዐን ፡ ወልሳን ፡ ወእእ
ዳው ፡ ወእእጋር ። ወእምዝኒ ፡ ድኅነት ፡ እም
ደዌያት ፡ ዘትከልእ ፡ እምተራክቦ ፡ ምስለ ፡
ሰብእ ፡ ሢመቱ ፡ ዘከመ ፡ ዝልጋሴ ፡ ወለምጽ ።
ወራብዕታ ፡ በዘይትፌጸም ፡ ሥርዓት ፡ እመግበ፡
ወበቍዔታት ፡ ሥን ፡ ግእዝ ፡ ወሥን ፡ ምክር ፡
ወአመክሮ ፡ ወጥበብ ።

፳፯ ወእምከመ ረከቡ ሰብእ ኅሪያት ብዙኃን
ሰብእ ፡ ዘትትረከብ ፡ ውስቴቶሙ ፡ ሥርዓተ ፡
ዛቲ ፡ ሢመት ፡ ይደሉ ፡ ከመ ፡ ይኅረይዎ ፡ ለዘ
ፍጹም ፡ እምኔሆሙ ፡ በሥርዓታቲሃ ፡ ወለዘያፈ
ጥኑ ፡ ሰብእ ፡ ለተአዝዞቱ ፡ ብዙኀ ። ወለእመ ፡
አበየ ፡ ውእቱ ፡ እምኔሃ ፡ ወኢተወከፋ ፡ ለይኅ
ረዩ ፡ እምኔሆሙ ፡ ካልአ ። ወለእመ ፡ ኢኮነ ፡
ካልኡ ፡ ድልወ ፡ ኢመፍትው ፡ ይኅድግዎ ።
ወለእመ ፡ ተረክቡ ፡ ፪ቱ ፡ እለ ፡ ዕሩያን ፡ በሥር
ዓታቲሃ ፡ ያቅርቡ ፡ ወይሢምዎ ፡ ለዘይልህቅ ፡
እምኔሆሙ ፡ በእንተ ፡ ፍድፋዴ ፡ መዋዕል ።
ወባሕቱ ፡ እስመ ፡ ልሂቀ ፡ መዋዕል ፡ ለገቢረ ፡



፳፭ የሚገባው ፡ በተሾመ ፡ ጊዜም ፡ በትእዛዝ ፡
መጽናት ፡ ይደረጋል ። ለሕዝቡ ፡ አለቃን
ይመርጡ ፡ ዘንድ ፡ ስለሚመርጡ ፡ ሰዎች ፡
ፈጽሞ ፡ አግባብ ፡ አላቸው ። ለመራጮችም ፡
ትእዛዞች ፡ ተዘጋጅተውላቸዋል ። እነርሱም ፡
ሦስት ፡ ወገን ፡ ናቸው ። ከእነርሱ ፡ አንዲቱ ፡
በአንቀጸ ፡ ሰማዕት ፡ የተናገርናት ፡ የቀናች ፡
እውቀት ፡ ናት ። ሁለተኛዪቱም ፡ ለዚህ
ሹመት ፡ የሚበቃውን ፡ ወደ ፡ ማመን ፡ የምታ
ደርስ ፡ እውቀት ፡ ናት ። ሦስተኛዪቱም ለዘ
መኑ ፡ የሚስማማውን ፡ ወደ ፡ መምረጥ ፡ የሚ
መሩትን ፡ ጥበብንና ፡ ምክርን ፡ ያገኙ ፡ ዘንድ ፡
ነው ። እርሱም ፡ በዘመኑ ፡ ለሚኖሩ ፡ ሰዎች ፡
የሚጠቅም ፡ ሕግን ፡ ለመጠበቅና ፡ ለማስተ
ማር ፡ የሚስማማ ፡ የሚያጸናና ፡ የሚያስረዳ፡
ነው ።

፳፮ ለእርሱ ፡ የሚገቡትም ፡ ትእዛዞች ፡ ከመጻሕ
ፍት ፡ ፪ ፡ ክፍሎች ፡ ናቸው ። እነሆ ፡ በአንቀጸ ፡
ኤጲስቆጶሳት ፡ በመጀመሪያው ፡ ተነገረች ።
ስለ ፡ እእምሮውም ፡ ተነግራለች ። እርስዋም ፡
አራት ፡ ወገን ፡ ናት ። መጀመሪያዋ ፡ ያለነርሱ ፡
በሹመት ፡ ጸንቶ ፡ መኖር ፡ የማይቻል ፡ የአካ
ልና ፡ የልብ ፡ ድኅነት ፡ ሰላም ፡ ናቸው ። እነር
ሱም ፡ ዓይን ፡ ጆሮ ፡ አንደበት ፡ እጆችና ፡ እግ
ሮች ፡ ናቸው ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ከተሾመባ
ቸው ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ መገናኘትን ፡ ከምትከለክ
ለው ፡ ደዌ ፡ መዳን ፡ ነው ። ይህም ፡ እንደ ፡ ደዌ
ሥጋ ፡ እንደ ፡ ለምጽ ፡ ያለ ፡ ነው ። አራተኛ
ዋም ፡ የአስተዳደር ፡ ሥን ፡ ሥርዓትና ፡ ጥቅም ፡
በጎ ፡ ምግባር ፡ በጎ ፡ ምክርና ፡ ጥበብ ፡ ፍጹም ፡
የሚሆንበትን ፡ ትናገራለች ።

፳፯ መራጮች ፡ የዚህች ፡ ሹመት ፡ ሥርዓት ፡ የም
ትገኝባቸውን ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ቢያገኙ ፡ በሥር
ዓትዋ ፡ ከነርሱ ፡ ፍጹም ፡ የሆነውንና ፡ ሰዎች ፡
ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ፈጥነው ፡ የሚታዘዙለትን ፡ ሊመር
ጡት ፡ ይገባል ። የተመረጠውም ፡ እምቢ ፡
ብሎ ፡ ባይቀበላት ፡ ከነርሱ ፡ ሌላውን ፡ ይም
ረጡ ። ሌላው ፡ በቂ ፡ ሆኖ ፡ ባይገኝ ፡ ሊተዉት ፡
አይገባም ። በሥርዓቶቿ ፡ ሁለቱም ፡ ተካክ
ለው ፡ ቢገኙ ፡ ከነርሱ ፡ በዘመን ፡ የሚበልጠ
ውን ፡ አቅርበው ፡ ይሹሙት ። ነገር ፡ ግን ፡
በዘመን ፡ የሚበልጠውን ፡ መሾም ፡ ሕግን ፡
ለመፈጸም ፡ ተስማሚ ፡ አይደለም ። በዘመን ፡

ሥርዓት ፡ ኢኮነ ፡ ሥርዓተ ፡ ወለእመኒ ፡ ተሠይመ ፡ ዘይነእሶሙ ፡ በመዋዕል ፡ እምደለወ ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ዘያፈደፍድ ፡ አእምሮ ፡ ወካልኡኒ ፡ ዘይሄኒ ፡ አመማቦተ ፡ ይረስይዎ ፡ ኖላዌ ፡ ለዘይፈቅዱ ፡ ፍትሐ ፡ ዝኩ ፡ ዘመን ።

፳፱ ወለእመ ፡ ኮነት ፡ መፍቅድ ፡ ኀበ ፡ ፍድፋዴ ፡ አእምሮ ፡ መጻሕፍት ፡ በምክንያተ ፡ አስተርእዮተ ፡ ዕልወታት ፡ ይሚምዎ ፡ ለማእምረ ፡ መጻሕፍት ። ወለእመኒ ፡ ኮነት ፡ መፍቅድ ፡ ኀበ ፡ ሠናየ ፡ ምግባር ፡ ይሚምዎ ፡ ለዘይሜግብ ፡ በሠናይ ። ወእመሰ ፡ ኮነ ፡ ዕሩየ ፡ ተጋእዞቶሙ ፡ እምክሉ ፡ ፍና ፡ ወተጋእዘ ፡ ከመ ፡ ይሚሙ ፡ ካልእኒሆሙ ፡ ይግባእ ፡ ግብሮሙ ፡ ኀበ ፡ ዕፃ ፡ በዲበ ፡ ታቦት ። ወይኄይስ ፡ ኅርየተ ፡ ካልእኒሆሙ ፡ ለእመ ፡ ተረክቡ ። እስመ ፡ ተጋእዞቶሙ ፡ በእንቲአሃ ፡ ያቈስሎሙ ። ወእኮ ፡ ረኪቦተ ፡ ትሩፈ ፡ ምግባር ፡ ዘይከልእ ፡ ለንኡስ ፡ መዓርግ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ ፍጹመ ፡ ለዐቂበ ፡ ሥርዓታት ። እስመ ፡ ፍድፋዴ ፡ ትሩፋት ፡ ትብጽሕ ፡ ውስተ ፡ ኅርየት ። ወእኮ ፡ ዘተዐዱ ፡ ውስተ ፡ ሥርዓታት ፡ ድልዋት ። ወለሰብእ ፡ ኅርየት ፡ ይደልዎሙ ፡ ከመ ፡ የሀብዎ ፡ ለዛቲ ፡ ሢመት ፡ ለዘድልው ፡ ላቲ ። ወእመሰ ፡ አበዩ ፡ ይከውኖሙ ፡ አበሳ ።

፴ ወኢይደሉ ፡ ከመ ፡ ትኩን ፡ ዛቲ ፡ ሢመት ፡ ለ፪ቱ ፡ በ፩ዱ ፡ ዘመን ፡ ወበ፩ዱ ፡ መንበር ። ወእመሰ ፡ ኮነ ፡ ዝ ፡ በ፩ ፡ ሀገር ፡ ትጽናዕ ፡ ለዘተሠይመ ፡ ቅድመ ። ወለእመኒ ፡ ተውህበት ፡ ለእለ ፡ ይደልዎሙ ፡ ውስተ ፡ ፪ቱ ፡ አህጉር ፡ ትቁም ፡ ለዘተውህበት ፡ ሎቱ ፡ ቅድመ ፡ ውስተ ፡ መካን ፡ ዘደለወት ፡ ቦቱ ፡ ልማድ ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ዝንቱ ፡ ውስተ ፡ ብሔር ፡ አሐቲ ፡ ትቁም ፡ ለዘተሠይመ ፡ ቅድመ ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ዝንቱ ፡ በ፩ ፡ ጊዜ ፡ ይደሉ ፡ ለለ፩ ፡ እምኔሆሙ ፡ ይግድፍ ፡ እምላዕለ ፡ ነፍሱ ፡ ወይደልዎሙ ፡ ለእለ ፡ የኀርዩ ፡ ከመ ፡ ይኅረይዎ ፡ ለዘተሠይመ ፡ ተሠይሞ ፡ እምኔሆሙ ፡ ባቲ ። ወለእመ ፡ ተዓረዩ ፡ ይኩን ፡ በዕፃ ፡ ዘታቦት ፡ ወይቁሙ ።

፴፩ ወለእመ ፡ አዘዘ ፡ በእንቲአሃ ፡ ተሠያሚሃ ፡ ለዘ ይሠየም ፡ እምድኅሬሁ ፡ አኮ ፡ ዘየአክል ፡ በእንቲአሃ ፡ ትእዛዘ ፡ ዚአሁ ። አላ ፡ ያቅድሙ ፡ ተንርዮተ ፡ ዚአሁ ፡ ከመ ፡ ካልእኒሁ ። ወይኩን ፡

የሚያንሰው ፡ ቢሾም ፡ በተገባው ፡ ነበር ። ከነርሱ ፡ አንዱ ፡ አብዝቶ ፡ የተማረ ፡ ቢሆን ፡ ሁለተኛውም ፡ አስተዳዳሪነትን ፡ ዐዋቂ ፡ ቢሆን ፡ ጊዜ ፡ የሚፈቅደውን ፡ ይሹሙት ።

፳፱ ክህደቶች ፡ በመብዛታቸው ፡ ምክንያት ፡ መጻሕፍትን ፡ አብዝቶ ፡ የተማረው ፡ ቢፈለግ ፡ መጽሐፍ ፡ ዐዋቂውን ፡ ይሹሙት ። የተፈለገው ፡ መልካም ፡ አስተዳዳሪን ፡ ለማግኘት ፡ ቢሆን ፡ በበጎ ፡ አስተዳደር ፡ የሚያስተዳድረውን ፡ ይሹሙት ። በሁሉም ፡ መንገድ ፡ ክርክራቸው ፡ እኩል ፡ ቢሆን ፡ ወዳጆቻቸውንም ፡ ለመሾም ፡ ቢከራከሩ ፡ በታቦት ፡ ላይ ፡ ዕጣ ፡ ይጣሉ ። ቢያገኙስ ፡ ሌሎችን ፡ መምረጥ ፡ ይሻላል ። በዚህ ፡ ምክንያት ፡ መከራከራቸው ፡ ያቆስላቸዋልና ። በምግባር ፡ በትሩፋት ፡ ፍጹም ፡ የሆነውን ፡ ማግኘት ፡ ሥርዓቱን ፡ ለመፈጸም ፡ ፍጹም ፡ ከሆነ ፡ ዘንድ ፡ በማዕርግ ፡ ያነሰውን ፡ ከሹመት ፡ የሚከለክለው ፡ አይደለም ። ምግባር ፡ ትሩፋት ፡ ለመመረጥ ፡ ታበቃለችና ። የተሠሩትን ፡ ሕጎች ፡ ግን ፡ የምታፈርስ ፡ አይደለችም ። መራጮች ፡ ይህችን ፡ ሹመት ፡ ለሚገባው ፡ ሰው ፡ መስጠት ፡ ይገባቸዋል ። ይህንንም ፡ ባያደርጉ ፡ ኃጢአት ፡ ይሆንባቸዋል ።

፴ ይህች ፡ ሹመት ፡ በ፩ ፡ ዘመንና ፡ በ፩ ፡ ሀገር ፡ ለሁለት ፡ ሰዎች ፡ ልትሆን ፡ አይገባም ። ይህ ፡ በአንድ ፡ ሀገር ፡ ከተደረገ ፡ ግን ፡ አስቀድሞ ፡ ለተሾመው ፡ ትጽና ። ለሚገባቸው ፡ ሰዎች ፡ በሁለት ፡ ሀገሮች ፡ ብትሰጥ ፡ ልማድ ፡ ተገቢ ፡ በሚያደርገው ፡ አገር ፡ አስቀድሞ ፡ ለተሾመው ፡ ትጽናለት ። ይህ ፡ በአንዲት ፡ ቦታ ፡ ቢሆን ፡ አስቀድሞ ፡ ለተሾመው ፡ ትጽና ። ይህ ፡ በአንድ ፡ ጊዜ ፡ ቢሆን ፡ ከነርሱ ፡ አንዱም ፡ አንዱ ፡ ሊተዋት ፡ ይገባል ። መራጮችም ፡ አስቀድሞ ፡ የተሾመውን ፡ መምረጥ ፡ ይገባቸዋል ። ተካክለው ፡ ቢገኙ ፡ በታቦቱ ፡ ፊት ፡ ቁመው ፡ በዕጣ ፡ ይሁን ።

፴፩ ሹም ፡ የነበረው ፡ ከእርሱ ፡ ቀጥሎ ፡ ለሚሾመው ፡ ሰው ፡ ቢያዝ ፡ የእርሱ ፡ ትእዛዝ ፡ በቂ ፡ አይደለም ። እንደ ፡ ጓደኞቹ ፡ ይምረጡት ፡ እንጂ ። ይኸውም ፡ ነውር ፡ ከሌለበት ፡ ክት

ዝንቱ ፡ እምትጋሀ ፡ ሥራሑ ፡ ዘአልቦ ፡ ውስቴቱ ፡ ነውር ።

፻፬ ወይደልዎሙ ፡ ለሕዝብ ፡ ከመ ፡ ያእምሩ ፡ ተሠያሚሆ ፡ በስሙ ፡ ወእርእያሁ ፡ ወግእዙ ። ወኢይደሉ ፡ ከመ ፡ ያጠይቆ ፡ በዓይኑ ፡ ወአስተሐምሞተ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ዘእንበለ ፡ በግብሩ ፡ እምብብእ ፡ ኅርየት ፡ ወይደልዎ ፡ ሎቱ ፡ ላዕለ እዘዘ ፡ ግብራት ። ወኵሎሙ ፡ ይጠይቁ ፡ ኪያሁ ፡ ግብረ ፡ ከዊኖቱ ፡ ሎቱ ። ወይድልዉ ፡ በመዳልው ፡ ለእመ ፡ ተረከቡ ፡ ኀቢሁ ፡ ፭ቱ ፡ ግብራት ።

፻፭ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ዐቂበ ፡ ሃይማኖት ፡ በከመ ፡ ተሠርዐ ፡ እመሠረቱ ፡ ወዘቆመ ፡ በአስተጋብእ ፡ እምቃለ ፡ ሐዋርያት ፡ እምዝኒ ፡ ማኅበራት ፡ ውኩፋት ፡ ወእምዝኒ ፡ ማኅበረ ፡ አበው ፡ እለ ፡ ተጋብኡ ፡ ለተወከፎተ ፡ ቃሎሙ ፡ በመተረ ፡ ዕልወታቲሆሙ ፡ ለፍሉጣን ፡ እምሃይማኖት ፡ ወሥዒረ ፡ ሀከክ ፡ በዘትከውን ፡ ሃይማኖት ፡ ዕቅብተ ፡ እምዕቅፍት ፡ ወሕዝብኒ ፡ ይርከቡ ፡ ዳኅና ፡ እምነ ፡ ዳኅፃት ።

፻፮ ወዳግማዊ ፡ እውዕአተ ፡ ፍትሕ ፡ በጽድቅ ፡ ወመቲረ ፡ ጋእዛት ።

፻፯ ወሣልስ ፡ አብዝኆ ፡ ሀብት ፡ ለእለ ፡ ይደልዎሙ ዘእንበለ ፡ አክብሮተ ፡ አሐዱ ፡ ወኢአሕጽጾት ፡ ወውሂቦቱሂ ፡ በአሐዱ ፡ ጊዜ ፡ እንዘ ፡ ኢያቀድም ፡ ወኢያስተድኅር ።

፻፰ ወራብዕ ፡ ሠይመ ፡ ሚመታት ፡ ለእለ ፡ ይደልዎሙ ፡ ወአስተዳልዎ ፡ ንዋያት ፡ በእንተ ፡ ምጽዋት ፡ ለኄራን ፡ ወለምእመናን ።

፻፱ ወኃምስ ፡ ከመ ፡ ይርአይ ፡ ግብራተ ፡ ኵሉ ፡ ወይድልዎን ፡ ለግብራት ፡ ድልዎት ፡ በንፍሱ ፡ ወይብል ፡ ይበቍዐኒ ፡ ዘአባሕክዎሙ ፡ ውስተ ፡ ኵሉ ፡ ምግባራት ፡ ወኢይፍጥር ፡ ካልአ ፡ በርእሱ ፡ ረባሐ ፡ ኵሉ ፡ ግብራት ። ወኢይትገበር ፡ ግብረ ፡ ጣዕማት ፡ ወኢለገቢረ ፡ ቅንየት ፡ ሎቱ ፡ እስመ ፡ ቅንየትሰ ፡ ውእቱ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ባሕቲቱ ፡ ዘእንበለ ፡ ጊዜ ፡ ውሉን ። ወይደልዎ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ይትማከሮሙ ፡ ለሰብእ ፡ እእ



ጋቱ ፡ የተነሣ ፡ ይሁን ።

፻፬ ሕዝቡም ፡ የሚሾመውን ሰው ፡ በስሙና ፡ በመልኩ ፡ በጠባዩም ፡ ሊያውቁት ፡ ይገባል ። ከመራጮች ፡ ወገን ፡ በሥራው ፡ እንጂ ፡ በዓይኑ ፡ አንዱ ፡ አንኳ ፡ ጠቅሶ ፡ ሊያሳየው ፡ አይገባውም ። እርሱም ፡ በሥርዓት ፡ ጸንቶ ፡ መኖር ፡ ይገባዋል ። ሁሉም ፡ ለእርሱ ፡ የሚገባውን ፡ እርሱን ፡ ይጠይቁ ። አምስቱ ፡ ግብራት ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ይገኙ ፡ እንደሆነም ፡ ይመዝኑ ፡ ይመርምሩ ።

፻፭ ከእነርሱ ፡ አንዱ ፡ በመጽሐፍ ፡ እንደ ፡ ተጻፈው ፡ ሃይማኖትን ፡ መጠበቅና ፡ ከሐዋርያት ፡ ቃል ፡ በመሰብሰብ ፡ የጸና ፡ መሆን ፡ ነው ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ሊቀበሏቸው ፡ የተገባ ፡ ማኅበሮችን ፡ መቀበል ፡ ነው ። ከዚህም ፡ ቀጥሎ ፡ ከሃይማኖት ፡ የተለዩትን ፡ ክህደቶች ፡ በመለየት ፡ ቃላቸውን ፡ ለመቀበል ፡ የተሰበሰቡትን ፡ የአበውን ፡ ማኅበር ፡ መቀበል ፡ ነው ። ሃይማኖት ፡ ከጥርጥር ፡ የተጠበቀች ፡ በምትሆን ፡ ንንዘብ ፡ ጠብ ፡ ክርክርን ፡ ለማራቅ ፡ ሕዝቡም ፡ ከመሰነካከል ፡ ድኅነትን ፡ እንዲያገኙ ፡ ለማድረግ ፡ የተሰበሰቡትን ።

፻፮ ሁለተኛው ፡ ፍርድን ፡ በእውነት ፡ መስጠትና ፡ ጠብ ፡ ክርክርን ፡ ማራቅ ፡ ነው ።

፻፯ ሦስተኛው ፡ ለሚገባቸው ፡ ሰዎች ፡ ለአንዱ ፡ ሳያበልጥ ፡ ለአንዱ ፡ ሳያሳንስ ፡ ሀብትን ፡ (ስጦታን) ፡ አብዝቶ ፡ መስጠት ፡ ነው ። አሰጣጡም፡ ሳያዘገይና ፡ ሳያስቀድም ፡ በአንድ ፡ ጊዜ ፡ ይሁን ።

፻፰ አራተኛው ፡ የሚገባቸውን ፡ ሰዎች ፡ መሾም ፡ ነው ። ለደጎችና ፡ ለምእመናንም ፡ ስለ ፡ ምጽዋት ፡ ገንዘብ ፡ መሰብሰብ ፡ ነው ።

፻፱ አምስተኛውም ፡ የሁሉን ፡ ሥራ ፡ ይመረምር ፡ ዘንድ ፡ ነው ። የሚገቡትን ፡ ሥራዎች ፡ እርሱ ፡ ራሱ ፡ ይመርምር ። በሥራው ፡ ሁሉ ፡ ያሠለጠንኋቸው ፡ ይበቃኛል ፡ አይበል ። ለራሱ ፡ ጥሪት ፡ አያብጅ ፡ የላመ ፡ የጣመ ፡ ለመቅመስ ፡ ታዘዙኝ ፡ ለማለትም ፡ አይድከም ። ጊዜ ፡ ሳይወስኑ ፡ መገዛት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ብቻ ፡ ነውና ። የአውቀት ፡ ሰዎችን ፡ ስለ ፡ ፍርድና ፡ ስለ ፡ ቅጣት ፡ ሊያማክራቸው ፡ ይገባዋል ።

ምር ፡ በእንተ ፡ ሁነኔ ፡ ወፍትሕ ፡ ወሰስብእ ፡ ምክርኒ ፡ በእንተ ፡ ምክር ፡ ዘእንበለ ፡ ነሚት ፡ ወእፍልሶ ፡ ወዘእንበለ ፡ እሲር ፡ ወፈቲሕ ። ወለእመ ፡ እንተ ፡ ቀዊመ ፡ ዘዘይደልዎ ፡ ወያዘልፍ ፡ ምሂረ ፡ ትእዛዛት ፡ ይደልዎሙ ፡ ተአዝዞቶ ፡ ወአዕብዮቶ ፡ ወአክብሮቶ ፡ ወአጽድቆተ ፡ ቃሉ ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ዕንቡዘ ፡ ልቡናሁ ፡ ወኮኑ ፡ ይሴፈዉ ፡ ተፈውሶቶ ፡ ይጽንሕዎ ። ወእመሰ ፡ ኢይሴፈዉ ፡ ወኮነ ፡ ዘመነ ፡ ሕማሙ ፡ ኅዳጠ ፡ ጥቀ ፡ ኢይክልእዎ ፡ እምአዘልፎተ ፡ ሢመት ፡ ሎቱ ። ወሰእመሰ ፡ በዝኀ ፡ እምዘመነ ፡ ተፈውሶ ፡ ይክልእዎ ።

የምክር ፡ ሰዎችንም ፡ ያለ ፡ ማፍረስና ፡ ያለ ፡ ማፍለስ ፡ ያለ ፡ ማስርና ፡ ያለመፍታት ፡ ሊያማክራቸው ፡ ይገባዋል ። በሚገባው ፡ ጸንቶ ፡ ቢኖር ፡ ሕጎቻትንም ፡ ማስተማር ፡ ቢያዘወትር ፡ ሊታዘዙለትና ፡ ፈጽሞ ፡ ሊያከብሩት ፡ ቃሉንም ፡ ሊቀበሉት ፡ ይገባቸዋል ። አእምሮውን ፡ ያጣ ፡ ቢሆንም ፡ ይድናል ፡ ብለው ፡ ተስፋ ፡ የሚያደርጉት ፡ ከሆነ ፡ ይጠብቁት ። ይድናል ፡ ብለው ፡ ተስፋ ፡ ባያደርጉ ፡ ግን ፡ የታመመበትም ፡ ዘመን ፡ በጣም ፡ ጥቂት ፡ ቢሆን ፡ ከሹመት ፡ አይሽሩት ። ከመዳን ፡ ቢዘገይ ፡ ግን ፡ ይሽሩት ።

፫፰ ወእኮ ፡ ሁሉ ፡ ዘይትከላእ ፡ እምእኂዘ ፡ ሢመት ፡ በእንተ ፡ ደዌ ፡ ኀላፊ ፡ ለእመ ፡ ይረክብ ፡ በድኅሬሁ ፡ ጥዒና ። እስመ ፡ እኂዘ ፡ ሢመት ፡ ትቁም ፡ ሎቱ ፡ እስከ ፡ የኀሥሥ ፡ ሎቱ ፡ ዳኅና ፡ ፍጽምተ ፡ ወሰፀእትሰ ፡ እምሢመት ፡ ይትረከብ ፡ ውስቴቱ ፡ ሕጸት ፡ ፍጹም ፡ ወሶበሂ ፡ ተሞቅሐ ፡ በሕብለ ፡ ደዌ ፡ ወዘይመስሎ ፡ ለዝንቱ ፡ ድልው ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ይጽንሕዎ ፡ በእንተ ፡ ዘይሴፎ ፡ ድኂነ ። ወእመሰ ፡ ኖኀ ፡ ዘመነ ፡ ደዌሁ ፡ መፍትው ፡ ለሰብእ ፡ ኅርየት ፡ ከመ ፡ ይሚሙ ፡ ህየንቴሁ ፡ ካልአ ፡ ዘይተልዎ ። ወለእመኒ ፡ ይትፌወስ ፡ ድኅረ ፡ መፍትው ፡ ውእቱ ፡ ከመ ፡ ይሠየም ፡ ህየንቴሁ ፡ ሕያው ፡ በመባሕተ ፡ ድዉይ ፡ እስከ ፡ ይትፌወስ ፡ ወይገብእ ፡ ኀበ ፡ መንበሩ ። ወለእመሰ ፡ ተዐውቀ ፡ ከመ ፡ ይመውት ፡ ወኢይትፌወስ ፡ መፍትው ፡ ይሠየም ፡ ካልእ ፡ በከመ ፡ ነገርነ ፡ ቀዳሚ ።

፫፰ በኋላ ፡ የሚድን ፡ ከሆነ ፡ በሚያልፍ ፡ በሽታ ፡ ምክንያት ፡ ሹመትን ፡ ከመያዝ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ የሚከለከል ፡ አይደለም ። ፍጹም ፡ ድኅነትን ፡ እስኪያገኝ ፡ ድረስ ፡ ልትጸናለት ፡ ይገባልና ። ከሹመት ፡ መሻር ፡ ግን ፡ ፍጹም ፡ ጉድለት ፡ ይገኝበታል ። በደዌ ፡ ገመድና ፡ በሚመስለውም ፡ ቢያዝ ፡ ድኅነትን ፡ ተስፋ ፡ ስለሚያደርግ ፡ ሊጠብቁት ፡ ይገባል ። የበሽታው ፡ ዘመን ፡ ቢበዛ ፡ መራጮች ፡ በእርሱ ፡ ፈንታ ፡ ሌላውን ፡ ሊሾሙ ፡ ይገባቸዋል ። በኋላም ፡ ቢድን ፡ እስኪድንና ፡ ወደ ፡ መንበሩ ፡ እስኪመለስ ፡ ድረስ ፡ ጤነኛው ፡ ሰው ፡ በበሽተኛው ፡ ፈቃድ ፡ ስለእርሱ ፡ ሆኖ ፡ ሊሾም ፡ ይገባዋል ። እንደማይድንና ፡ እንደሚሞት ፡ ቢታወቅ ፡ ግን ፡ አስቀድመን ፡ እንደ ፡ ተናገርን ፡ ሌላው ፡ ሊሾም ፡ ይገባዋል ።

፫፱ ወፈጸሞተ ፡ ነገር ፡ በእንተ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ወሥርዓተ ፡ ሢመቱ ፡ ወዘይመስሎ ፡ ለዝንቱ ፡ ተነግረ ፡ በቀኖናት ፡ ከመ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ወኢይሠየሙ ፡ ኤጲስቆጳሳት ፡ ዘብሔረ ፡ መንበሩ ፡ እንበለ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ በዓለ ፡ መንበር ፡ ዘእስክንድርያ ።

፫፱ ስለ ፡ ሊቃነ ፡ ጳጳሳት ፡ የነገሩ ፡ መጨረሻ ፡ የሹመቱም ፡ ሥርዓት ፡ ይህን ፡ የሚመስለውም ፤ ለሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ የሚገባው ፡ በመጻሕፍት ፡ ተነገረ ። ያለ ፡ እስክንድርያው ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ፈቃድ ፡ በሀገረ ፡ መንበሩ ፡ ውስጥ ፡ ያሉ ፡ ኤጲስቆጳሳት ፡ አይሾሙ ።

---

## አንቀጽ ፡ ኃምስ ።

### በእንተ ፡ ኤጲስቆጳሳት ።

፩ ኤጲስቆጳስሰ ፡ ከመ ፡ ኖላዊ ፡ በከመ ፡ ተነግረ ፡ በዲድስቅልያ ። ወርእየቱ ፡ ወሀላዌሁ ፡ ይኩን ፡ በ፫ ፡ ገጻት ፡ ቀዳማዊ ፡ እምቅድመ ፡ ኅርየቱ ፡ ወሢመቱ ፡ ወዳግም ፡ ግብረ ፡ ኅርየቱ ፡ ወሣ

## አንቀጽ ፡ ፮ ።

### ስለ ፡ ኤጲስቆጳሳት ።

፩ ኤጲስቆጳስስ ፡ በዲድስቅልያ ፡ እንደ ፡ ተነገረ ፡ እንደ ፡ ጠባቂ ፡ ነው ። አስተያየቱና ፡ አኗኗሩ ፡ በ፫ ፡ ወገን ፡ ይሁን ። መጀመሪያው ፡ ከመመረጡና ፡ ከመሾሙ ፡ በፊት ፡ ሁለተኛው ፡ የአመ

ልስ ፤ እምድኅረ ፡ ሢመቱ ፡ ፍጽምት ።

፻፩ ቀዳማዊትሰ ፡ ትትከፈል ፡ ኀበ ፡ ፫ ፡ አክፋል ፡
እሐቲ ፡ እምኔሆን ፡ እንተ ፡ ታጤይቅ ፡ ከመ ፡
ውእቱ ፡ ድልው ፡ ለኤጲስቆጶስና ፡ ወካልእ
ታሂ ፡ ምክንያት ፡ እንተ ፡ ትከልእ ፡ ሎቱ ፡
እምኔሃ ፡ ወማልሰታ ፡ በዘኢይደልዎ ፡ ወኢይክ
ልእዎ ፡ እላ ፡ ኤጲስቆጶስና ፡ ምስሌሃ ፡ ድልው ፡
ሎቱ ።

፻፪ ወድልወትሰ ፡ ፰ቱ ፡ ይእቲ ፡ ቀዳሚት ፡ ወዳግ
ሚት ፡ ወሣልሲት ፡ ወራብዒት ፡ በእንተ ፡
ሑረቱ ፡ ወግዕዙ ፡ ወሕይወቱ ፡ ወተኃርዮቱ ።

፻፫ ይቤ ፡ ጳውሎስ ፡ ሐዋርያ ፡ ጤት ፡ ዘ፪ቱ ፡ “ወአ
መን ፡ ውእቱ ፡ ነገሩ ፡ እስመ ፡ ለእመ ፡ አፍ
ቀረ ፡ ፩ዱ ፡ ከመ ፡ ይሠየም ፡ ኤጲስቆጶስና ፡
ነዋ ፡ አፍቀረ ፡ ግብረ ፡ ሠናየ ። ወነዋ ፡ ይደሉ ፡
ይኩን ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ዘኢተረከበ ፡ ውስቴቱ ፡
ነውር ። ወዘአውሰበ ፡ እሐተ ፡ ብእሲተ ፡ ዘን
ቁህ ፡ በኀሊናሁ ፡ ውእቱ ፡ ጠቢብ ፡ ወመናዝዝ ፡
ወመፍቀሬ ፡ ነግድ ፡ መምህር ፡ ዘኢያበዝን ፡
ሰትየ ፡ ወይን ፡ ወዘኢያፈጥን ፡ እዴሁ ፡ ለዘቢጥ።
አላ ፡ ይኩን ፡ ትሑተ ፡ ወኢይኩን ፡ ተጋእዜ ፡
ወኢመፍቀሬ ፡ ንዋይ ፡ ወዘያሤኒ ፡ ሠሪዐ ፡ ቤቱ፡
ወሕፃናቲሁ ፡ ደቂቁ ፡ ወዘያኔብሮሙ ፡ ኀበ ፡ ተአ
ዝዞት ፡ ወኵሉ ፡ ንጽሕ ። እመሰ ፡ ውእቱ ፡ ዘኢ
ያሤኒ ፡ ሠሪዐ ፡ ቤቱ ፡ እፎ ፡ ያሤኒ ፡ ሠሪዐ ፡
ቤተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወቤተ ፡ ክርስቲያን ።
ወኢይኩን ፡ ተክለ ፡ ሐዲስ ፡ ከመ ፡ ኢይዘኀር ።
ወኢይደቅ ፡ ውስተ ፡ ሥቃየ ፡ ሰይጣን” ፡ ወይ
ደሉ ፡ ካዕበ ፡ ከመ ፡ ይኩንዎ ፡ ሎቱ ፡ ስማዕተ ፡
በሠናይ ፡ እምዐላውያን ፡ ዚአነ ፡ በሃይማኖት ፡
ከመ ፡ ኢይደቅ ፡ ውስተ ፡ ትዕይርት ፡ ወውስተ ፡
አሕባለ ፡ ሰይጣን ።

፻፬ ድስቅ ፡ ፬ቱ ፡ ወከመዝ ፡ ስማዕናሁ ፡ ለእግዚ
እነ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ እንዘ ፡ ይብል ፡
ይደልዎ ፡ ለኖላዊ ፡ ዘይሠይምዎ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡
ለአብያተ ፡ ክርስቲያናት ፡ ዘውስተ ፡ ኵሉ ፡
መካን ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ዘእንበለ ፡ ሐስ ፡ ወኢኔ



ራረጡ ፡ ሥራ ፡ ሦስተኛውም ፡ ፈጽሞ ፡ ከተ
ሾመ ፡ በኋላ ፡ ያለው ፡ ነው ።

፻፩ መጀመሪያዪቱ ፡ በሦስት ፡ ክፍሎች ፡ ትከፈላ
ለች ። ከነርሱ ፡ አንዲቱ ፡ ለኤጲስቆጶስነት ፡
የበቃ ፡ መሆኑን ፡ የምታስረዳ ፡ ናት ። ሁለተ
ኛዪቱም ፡ እርሱን ፡ ከእርስዋ ፡ (ከሹመት) ፡
የምትከለክል ፡ ምክንያት ፡ ናት ። ሦስተኛ
ዋም ፡ የማይገባውንና ፡ የማይከለክልበትን ፡
ታስረዳለች ፡ ከርስዋ ፡ ጋር ፡ ኤጲስቆጶስነት ፡
ይገባዋል ፡ እንጂ ።

፻፪ ለሹመት ፡ የሚበቃባቸው ፡ ሥራዎች ፡ ፰ ፡
ናቸው ። አንደኛዋና ፡ ሁለተኛዋ ፡ ሦስተኛዋ ፡
አራተኛዋ ፡ ስለ ፡ አኗኗሩና ፡ ስለ ፡ ጠባዩ ፡
ስለ ፡ ሕይወቱና ፡ ስለ ፡ አመራረጡ ፡ ትናገራ
ለች ።

፻፫ ሐዋርያው ፡ ጳውሎስ ፡ ጤት ፡ ፪ ፡ (፩ጢሞ ፡ ፫ ፡
፩-፯) ። እንዲህ ፡ አለ ። አንድ ፡ ሰው ፡ ኤጲስቆ
ጶስነትን ፡ ሊሾም ፡ ቢወድ ፡ እነሆ ፡ መልካም ፡
ሥራን ፡ ወደደ ። ነውር ፡ የሌለበት ፡ ሰው ፡ ኤጲ
ስቆጶስ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ይገባል ። አንዲት ፡
ሴት ፡ ያገባ ፡ በሐሳቡ ፡ ንቁ ፡ የሆነ ፡ አዋቂ ፡
የሚያረጋጋ ፡ እንግዳ ፡ ተቀባይ ፡ መጠጥ ፡ የማ
ያበዛ ፡ መምህር ፡ ይሁን ። ትሑት ፡ ይሁን ፡
እንጂ ፡ ለመማታት ፡ እጁን ፡ የማያፋጥን ፡
መሆን ፡ ይገባዋል ። ተከራካሪና ፡ ገንዘብ ፡
ወዳጅ ፡ አይሁን ። ቤተ ፡ ሰቡን ፡ የሚያስተዳ
ድርና ፡ ልጆቹን ፡ በሚገባ ፡ የሚያሳድግ ፡ ወደ ፡
መታዘዝና ፡ ወደ ፡ ንጽሕና ፡ የሚያደርሳቸውም ፡
ይሁን ። እርሱ ፡ ቤተ ፡ ሰቡን ፡ በሚገባ ፡ የማያ
ስተዳድር ፡ ከሆነ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤትና ፡
የክርስቲያንን ፡ ቤተ ፡ ሰብ ፡ እንዴት ፡ ያስተዳ
ድራል ? ። ሐዲስ ፡ ተክል ፡ በሃይማኖት ፡ አይ
ሁን ። እንዳይታበይ ፡ በሰይጣን ፡ ፈተናም ፡
እንዳይወድቅ ። ዳግመኛም ፡ በሃይማኖት ፡ ከኛ ፡
ውጭ ፡ የሆኑት ፡ ሰዎች ፡ በመልካም ፡ ሥራው ፡
የመሰከሩለት ፡ መሆን ፡ ይገባዋል ። በትዕቢ
ትና ፡ በሰይጣን ፡ አሽክላ ፡ እንዳይወድቅ ።

፻፬ ድስቅ ፡ ፬ ። ጌታችን ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ እን
ዲህ ፡ ብሎ ፡ ሲናገር ፡ ሰማነው ፤ በየቦታው ፡
ላሉ ፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናት ፡ ኤጲስቆጶስ ፡
ሆኖ ፡ የሚሾመው ፡ ጠባቂ ፡ ያለ ፡ ነውርና ፡ ያለ፡
በደል ፡ ይሁን ። ከሰው ፡ ሁሉ ፡ በደል ፡ የነጻ ፡

ጋይ ። ወይኩን ፡ ንጹሐ ፡ እምኵሉ ፡ ዓመፃ ፡ ዘሰ
ብእ ፡ ወዘኢኮነ ፡ ሕያውተ ፡ ሕጹጸ ፡ እምሃ ፡
ዓም ። ወለእመ ፡ ተከሀሎ ፡ ለይኩን ፡ ምሉእ ፡
እምኵሉ ፡ ትምህርት ፡ ወተማህሮ ፡ ወማእምረ ፡
ነገር ፡ በቃሉ ።

፹፭ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ መንበሩ ፡ ንኡሰ ፡ ወኢረከቡ ፡
ዘብዙኀ ፡ ዓመቲሁ ፡ ዐቢየ ፡ ልህቅናሁ ፡ አላ ፡
ረከቡ ፡ ሕጹጸ ፡ በዓመት ፡ ልህቅናሁ ፡ ዘይከ
ውኑ ፡ ሎቱ ፡ ሰምዐ ፡ እለ ፡ ይነብሩ ፡ ምስሌሁ ፡
ከመ ፡ ውእቱ ፡ ድልው ፡ ለኤጲስቆጶስና ፡
ወከመ ፡ ውእቱ ፡ ነዋ ፡ አርአየ ፡ በውርዝውና
ናሁ ፡ ግብረ ፡ አእሩግ ፡ በፍሥሐ ፡ ወበሥር
ዓት ፡ ወጥበብ ፡ ወለዝንቱኒ ፡ ይደሉ ፡ ከመ ፡
ይፍትንዎ ፡ ወለእመ ፡ ተረክበ ፡ በከመ ፡ ኮንዎ ፡
ሰምዐ ፡ ይሢምዎ ፡ በሰላም ።

፹፮ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ንኡሰ ፡ እው ፡ ዐቢየ ፡ ወይኩን ፡
ፍሡሐ ፡ ወትሑተ ፡ ወህዱአ ፡ እስመ ፡ እግዚእ
ብሔር ፡ ይቤ ፡ በአፈ ፡ ኢሳይያስ ፡ ነቢይ ፡
ኀበ ፡ መኑ ፡ እኔጽር ፡ ዘእንበለ ፡ ኀበ ፡ ትሑ
ታን ፡ ወየዋሃን ፡ እለ ፡ ይርዕዱ ፡ እምቃልየ ፡
በኵሉ ፡ ዘመን ። ወከማሁ ፡ ይቤ ፡ በወንጌ
ል ፡ ካዕበ ፡ በ፩ ፡ ምዕራፍ ፡ ብፁዓን ፡ የዋሃን ፡
እስመ ፡ እሙንቱ ፡ ይወርስዋ ፡ ለምድር ። ወይ
ኩን ፡ መሐሬ ፡ እስመ ፡ ይቤ ፡ ብፁዓን ፡ መሐ
ርያን ፡ እስመ ፡ ሎሙኒ ፡ ይምሕርዎሙ ። ወይ
ኩን ፡ በዓለ ፡ ሰላም ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ይቤ ፡
ብፁዓን ፡ ገባርያን ፡ ሰላም ፡ እስመ ፡ እሙንቱ ፡
ውሉደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይሰመዩ ። ወለትኩን ፡
ሕሊናሁ ፡ ሠናይተ ፡ ወንጽሕተ ፡ እምኵሉ ፡
እከይ ፡ ወዐመፃ ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ይቤ ፡ ብፁ
ዓን ፡ ንጹሐነ ፡ ልብ ፡ እስመ ፡ እሙንቱ ፡ ይሬ
እይዎ ፡ ለእግዚአብሔር ።

፹፯ ወይኩን ፡ ተዓጋሢ ፡ ቀዋሚ ፡ በኵሉ ፡ ሥር
ዓት ፡ ሠናይ ፡ ኢይኩን ፡ ተሃዋኬ ፡ ወኢሰካሬ ፡
ወኢቍጡዐ ፡ ወኢመፍቀሬ ፡ ንዋይ ፡ ወወርቅ ፡
ወይፍትንዎ ፡ ካዕበ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ዘአልቦቱ ፡
ነውር ፡ በኵሉ ፡ አምሳል ፡ ዘዝንቱ ፡ ዓለም ።
እስመ ፡ ጳውሎስ ፡ ውእቱ ፡ ዘይብል ፡ ይፍትንዎ ፡
ለዘያነብርዎ ፡ በዝየ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ዘእንበለ ፡
ነውር ። ወኢይኩን ፡ መዓትመ ፡ እስመ ፡ ትብል
ጥበብ ፡ እስመ ፡ መዓት ፡ ታማስን ፡ ጠቢባነ ።
ወይኩን ፡ መፍቀሬ ፡ ሰብእ ፡ እስመ ፡ ይብል ፡

ሰድሚውም ፡ ከ፶ ፡ ዓመት ፡ ያላነሰ ፡ ይሁን ።
ቢቻለውስ ፡ ትምህርትን ፡ ሁሉና ፡ ምክርን ፡
የተመላ ፡ ቢቃሉ ፡ ነገር ፡ አዋቂም ፡ ይሁን ።

፹፭ ሀገረ ፡ ስብከቱ ፡ ታናሽ ፡ ቢሆን ፡ በዕድሜውም ፡
ሽማግሌ ፡ የሆነ ፡ ባያገኙ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ለኤጲ
ስቆጶስነት ፡ እንደሚበቃ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ የሚ
ኖሩት ፡ ሰዎች ፡ የመሰከሩለት ፡ ወጣት ፡ ቢያ
ገኙ ፡ በጐልማስናውም ፡ ወራት ፡ የሽማግሌዎ
ችን ፡ ሥራ ፡ በደስታና ፡ በሥርዓት ፡ በዘዴ ፡
እንዳሳየ ፡ ቢመሰከሩለት ፡ ይህንን ፡ ሊፈትኑት ፡
ይገባል ። እንደ ፡ መሰከሩለት ፡ ሆኖ ፡ ቢገኝ ፡
ተስማምተው ፡ ይሹሙት ።

፹፮ ትንሽ ፡ ወይም ፡ ትልቅ ፡ ቢሆን ፡ ደስተኛና ፡
ትሑት ፡ ጸጥተኛም ፡ ይሁን ። እግዚአብሔር ፡
በነቢዩ ፡ በኢሳይያስ ፡ አፍ ፡ (ኢሳ ፡ ፷፮ ፡ ፩-፪) ።
ወደ ፡ ማን ፡ እመለከታለሁ ። ከቃሌ ፡ የተነሣ ፡
በዘመኑ ፡ ሁሉ ፡ ወደሚፈሩና ፡ ወደሚንቀጠ
ቀጡ ፡ የዋሃንና ፡ ትሑታን ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ብሏ
ልና ። እንዲሁም ፡ በወንጌል ፡ (ማቴ ፡ ፭ ፡ ፯-
፱) ። በ፭ኛው ፡ ምዕራፍ ፡ እንዲህ ፡ ተብሏል ።
የዋሃን ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ፡ እነርሱ ፡ ምድርን ፡
ይወርሳሉና ። የሚራራም ፡ ይሁን ፡ የሚራሩ ፡
ብፁዓን ፡ ናቸው ፡ ለነርሱም ፡ ይራሩላቸዋል ፡
ብሏልና ። ሰላማዊ ፡ ይሁን ፡ ሰላምን ፡ የሚያደ
ርጉ ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ፡ እነርሱ ፡ የእግዚአብ
ሔር ፡ ልጆች ፡ ይባላሉ ፡ ብሏልና ። ሐሳቡም ፡
ያማረች ፡ የጸራች ፡ ከክፋትና ፡ ከዐመፅ ፡ ሁሉ ፡
የነጻች ፡ ትሁን ። ልባቸው ፡ ንጹሕ ፡ የሆነላ
ቸው ፡ ሰዎች ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ፡ እነርሱ ፡ እግ
ዚአብሔርን ፡ ያዩታል ፡ ብሏልና ።

፹፯ የሚታገሥና ፡ በመልካም ፡ ሥርዓት ፡ ሁሉ ፡
የጸና ፡ ይሁን ። የሚታወክና ፡ የሚሰክር ፡
ቁጡ ፡ ገንዘብ ፡ ወዳጅ ፡ አይሁን ። በዚህ ፡
ዓለም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ነውር ፡ የሌለበት ፡ መሆን
አለመሆኑን ፡ ደግመኛ ፡ ይፈትኑት ። "በዚህ ፡
የሚያስቀምጡትን ፡ ይፈትኑት ፡ ነውር ፡ የሌለ
በት ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡" (፩ጢሞ ፡ ፫ ፡ ፲) ።
የሚል ፡ ጳውሎስ ፡ አለና ። ቁጡ ፡ አይሁን ፡
ጥበብ ፡ "ቍጣ ፡ አዋቂዎችን ፡ ታጠፋለች ፡
ትላለችና ፡" (ምሳ ፡ ፲፭ ፡ ፩) ። ሰውን ፡ አፍቃሪ

አሁ ፡ ወያስተፋልስም ፡ ውስተ ፡ መዓርገ ፡ ክህ
ነት ፡ በመዓርግ ፡ እምድኅረ ፡ መዓርግ ፡ በበመ
ዓርጉ ። ወለእመ ፡ ቆመ ፡ በሐራቱ ፡ በዘሰ ፡ መዓ
ርገ ፡ ድልወቱ ፡ ሰቤሃ ፡ ይሠየም ።

፺፬ ሳምን ፡ ከመ ፡ ይትኃረይ ፡ እምብዙኃን ። በስ ፡
፺፬ ፡ ወኢይሠየም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ዘእንበለ ፡
ይኅሀድዎ ፡ ፲ወ፪ ፡ እደው ። ረስጣ ፡ ፲ወ፫ ፡
ወለእመ ፡ ኮነ ፡ መካነ ፡ ምእመናን ፡ ዘውስቴቱ ፡
ኅዳጣን ፡ ወኢበዝኁ ፡ ማኅበር ፡ ከመ ፡ ይግ
በሩ ፡ ሢመተ ፡ ለኤጲስቆጶስ ፡ እስከ ፡ መጠነ ፡
፲ወ፪ ፡ እደው ፡ ለይጽሐፉ ፡ ኀበ ፡ አብያተ ፡
ክርስቲያን ፡ ዘቅርብት ፡ ብሔር ፡ ኀበ ፡ ሀለወ ፡
ውስቴታ ፡ እምመናን ፡ ብዙኃን ፡ ከመ ፡ ይምጽኡ ፡ እምእመናኒሆሙ ፡ ፫ቱ ፡ አለ ፡ ተኀርዩ ፡
ወያምክርዎሙ ፡ በአስተሐምሞ ፡ በእንተ ፡
ዘይደልዎ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ ሎቱ ፡ ሐረት ፡ ሠናይ ፡
ዘኢፀራፊ ፡ ወዘኢያደሉ ፡ ወዘይክል ፡ ተርጕሞ ፡
መጻሕፍት ።

፺፭ ወማብሬትስ ፡ እለ ፡ ይከልእ ፡ ስሱ ፡ እማንቱ ፡
ቀዳሚት ፡ ረስጠጅ ፡ ፶ወ፪ ፡ ኢይደሉ ፡ ከመ ፡
ይኩን ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ዘጋኔን ።

፺፮ ካልእት ፡ ወሣልሲት ፡ ረስጠጅ ፡ ፶ወ፪ ፡ ወኢይ
ደሉ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ዕወር ፡ ወኢጽሙም ፡
ወኢዝንጉዕ ፡ አኮ ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡ ነውር ። አላ ፡
እስመ ፡ ውእቱ ፡ ኢይክል ፡ በእንተ ፡ ፈጽሞቱ ፡
ለዘውእቱ ፡ ይትፈቀድ ፡ እምግብሬተ ፡ ቤተ ፡
ክርስቲያን ።

፺፯ ራብዕ ፡ ረስጠጅ ፡ ዘ፸ወ፫ ፡ ወዘኢኮነ ፡ ምእ
መነ ፡ ወተጠምቀ ፡ ወዘነበረ ፡ ብእሴ ፡ እኩየ ፡
ወነስሐ ፡ ኢይሠየም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ በቀዳሚ ፡
ግብሩ ። እስመ ፡ ውእቱ ፡ እምአበሳ ፡ ኢይኩን ፡
መምህረ ፡ ወኢተአምረ ፡ ኂሩቱ ፡ ዘእንበለ ፡
ለእመ ፡ ይከውን ፡ ውእቱ ፡ በአእምሮ ፡ እምእግ
ዚአብሔር ።

፺፰ ኃምስ ፡ ረስጠጅ ፡ ፲ወ፫ ፡ ወዘኀጸወ ፡ ርእሶ ፡
በፈቃዱ ፡ ኢይሠየም ። ወዘተኀጽወ ፡ በትዕ
ግልት ፡ ኢይትከላእ ፡ በእንተ ፡ ውእቱ ።

፺፱ ሳድስ ፡ ጠስ ፡ ፳ወ፰ ፡ ወለእመ ፡ ቀዳደቆ ፡ ሎቱ፡
፩ ፡ ወይቤ ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡ ኢይሜኒ ፡ ለኤጲስ
ቆጶስና ፡ ለይደኀር ፡ ግብሩ ፡ ፫ተ ፡ አውራኀ ።
ወእምዝ ፡ ይትከሠት ፡ በእንቲአሁ ፡ ግብሩ ፡
በህላዌ ፡ ዕድዉ ፡ አው ፡ በኢህላዌሁ ። ወለእመ ፡



መዓርጉ ፡ ከመዓርግ ፡ ወደ ፡ ማዕርግ ፡ ያው
ጡት ። በአካሄዱ ፡ ሁሉ ፡ በሚገባው ፡ መዓርግ ፡
ጸንቶ ፡ ቢኖር ፡ ያንጊዜ ፡ ይሹሙት ።

፺፬ ስምንተኛ ፡ ከብዙ ፡ ሰዎች ፡ ይመረጥ ፡ ዘንድ ፡
ነው ። በስ ፡ ፺፬ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ፲፪ ፡ ሰዎች ፡ ሳይ
መስክሩለት ፡ አይሾም ። ረስጣ ፡ ፲፫ ፡ የምእመ
ናኑ ፡ ቦታ ፡ በውስጡ ፡ ያሉበት ፡ ሰዎች ፡ ጥቂ
ቶች ፡ ቢሆኑ ፡ ኤጲስቆጶሱን ፡ ለመምረጥ ፡
ሰዎቹ ፡ እስከ ፡ ፲፪ ፡ ያልሞሉ ፡ ቢሆኑ ፡ ብዙዎ
ች ፡ ምእመናን ፡ ወዳሉበት ፡ በአቅራቢያቸው ፡
አገር ፡ ወደምትገኝ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ከምእ
መናኖቻቸው ፡ ወገን ፡ የተመረጡ ፡ ፫ት ፡ ሰዎች
ይመጡ ፡ ዘንድ ፡ ይጻፉ ። የሚገባውንም ፡ ለመ
ምረጥ ፡ ያማክሯቸው ። መልካም ፡ አኗኗር ፡
ያለው ፡ እንደሆነ ፡ የማይሳደብ ፡ የማያደላ ፡
መጻሕፍትን ፡ መተርጐም ፡ የሚችል ፡ እንደ
ሆነ ፡ ያማክሯቸው ።

፺፭ ከሹመት ፡ የሚከለክሉ ፡ ነገሮች ፡ ስድስት ፡
ናቸው ። መጀመሪያዪቱ ፡ ረስጠጅ ፡ ፶፪ ። ጋኔን፡
ያደረበት ፡ ሰው ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ መሆን ፡ አይገ
ባውም ።

፺፮ ሁለተኛዪቱና ፡ ሦስተኛዪቱ ፡ ረስጠጅ ፡ ፶፪ ።
ዓይነ ፡ ስውር ፡ ደንቆሮ ፡ ዝንጉዕ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡
ኤጲስቆጶስ ፡ ሊሆን ፡ አይገባውም ። ነውር ፡
ሆኖ ፡ አይደለም ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሥራ ፡
ወገን ፡ ከርሱ ፡ የሚሻውን ፡ ሥራ ፡ ለመፈጸም ፡
ስለማይችል ፡ ነው ፡ እንጂ ።

፺፯ አራተኛው ፡ ረስጠጅ ፡ ፸፫ ፡ አማኒ ፡ ያይደለ ፡
በኋላ ፡ የተጠመቀ ፡ ክፉ ፡ ሁኖ ፡ ኑሮ ፡ በኋላ ፡
የተመለሰ ፡ ሰው ፡ ከበደል ፡ ወገን ፡ ስለሆነ ፡
በቀደመ ፡ ሥራው ፡ ኤጲስቆጶስነት ፡ አይሾም ።
ደግነቱ ፡ ሳይታወቅ ፡ አስተማሪ ፡ አይሁን ።
ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ምልክት ፡ ካልተገኘ
ለት ፡ በቀር ።

፺፰ አምስተኛው ፡ ረስጠጅ ፡ ፲፫ ፡ በራሱ ፡ ፈቃድ ፡
አባለ ፡ ዘሩን ፡ የሰለበ ፡ አይሾም ። በግድ ፡ የተ
ሰለበ ፡ ግን ፡ በግድ ፡ ስለሆነ ፡ አይከልከል ።

፺፱ ስድስተኛው ፡ ጠስ ፡ ፳፰ ፡ አንዱ ፡ አንዱን ፡
ለኤጲስቆጶስነት ፡ አይገባም ፡ ብሎ ፡ ቢከሰው ፡
ሥራው ፡ ፫ወር ፡ ይቈይ ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ባላ
ጋራው ፡ ባለበት ፡ ወይም ፡ በሌለበት ፡ ሥራው ፡
ስለርሱ ፡ ይመርመር ። በመጽሐፍ ፡ ውስጥ ፡

ተዐውቀ ፡ ላዕሌሁ ፡ ግብር ፡ ዘይከልእ ፡ በው
ስተ ፡ ቀኖናት ፡ እምተሠይሞቱ ፡ ይትከላእ ።
ወእመ ፡ አኮሰ ፡ ለይሠየም ፡ ወዕድውኒ ፡ ዘእስ
ተዋድዮ ፡ ወኢያቀመ ፡ ላዕሌሁ ፡ ዘዘከሮ ፡
ለእመ ፡ ኮነ ፡ ካህነ ፡ ለይሰደድ ፡ እምቤተ ፡ ክር
ስቲያን ፡ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ሕዝባዌ ፡ ለይትገ
ሠፅ ፡ በከመ ፡ ይደሉ ።

፻ ወማልስ ፡ ዘኢይደሉ ፡ ወኢይከልእ ፡ ረስጠጅ ፡
፳ወ፪ቱ ፡ ወኢይትከላእ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ኤጲ
ስቆጶስ ፡ ንጺር ፡ ወኢሐንካስ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡
ይሜኒ ፡ ለዝግብር ። እስመ ፡ ነውረ ፡ ሥጋ ፡
ኢኮነ ፡ ነውረ ፡ ወባሕቱ ፡ ነውርሰ ፡ ነውረ ፡
ነፍስ ፡ ውእቱ ።

፻፩ ወገጽ ፡ ካልእ ፡ ግብረ ፡ ሢመቱ ። ድስቅ ፡ ፴ወ
፯ቱ ፡ ወይሠየም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ በዕለተ ፡ እሑድ
ወዙሎሙ ፡ ሰብእ ፡ ይነብሩ ፡ በእንተ ፡ ተሠይ
ሞቱ ፡ ሕዝብኒ ፡ ወካህናት ፡ እንዘ ፡ ሰምዐ ፡ ይከ
ውኑ ፡ ሎቱ ። ወኤጲስቆጶሳትኒ ፡ እለ ፡ መጽኡ ፡
ከመ ፡ ያንብሩ ፡ እዴዊሆሙ ፡ ዲቤሁ ፡ ይትኀ
ፀቡ ፡ እደዊሆሙ ፡ ወእምዝ ፡ ይሚምዎ ፡ ወሕ
ዝብ ፡ ቀዊሞሙ ፡ በአርምሞ ፡ ወበፍርሃት ፡
ያንሥኡ ፡ እደዊሆሙ ፡ ወያንብሩ ፡ ኤጲስቆጶ
ሳት ፡ እደዊሆሙ ፡ ዲቤሁ ፡ እንዘ ፡ ይብሉ ፡
ንሕነ ፡ ናንብር ፡ እደዊነ ፡ ዲበ ፡ ዝንቱ ፡ ገብር ፡
ኅሩይ ፡ ዘእግዚአብሔር ፡ በስመ ፡ አብ ፡ ወወ
ልድ ፡ ወመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ከመ ፡ ይቁም ፡
ውስተ ፡ ሥርዓት ፡ ሠናይት ፡ ወጽንዕት ፡ ዘአ
ሐቲ ፡ ዘእንበለ ፡ ነውር ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡
ለእግዚአብሔር ፡ ሕያው ፡ ዘአያስተርኢ ። ለገ
ቢረ ፡ ፍትሐ ፡ ርትዕ ፡ ወከሚተ ፡ ለቅዳሴ ፡
ወጸጋ ፡ ንጽሕት ፡ ወምሂር ፡ ምእመን ፡ ዘው
እቱ ፡ ዘተሠይመ ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ጉባኤ ፡
እምኀበ ፡ ሥሉስ ፡ ቅዱስ ፡ በምሥጢረ ፡ መስ
ቀል ። ወእምድኅረ ፡ ዝንቱ ፡ ያንብር ፡ ኤጲስ
ቆጶስ ፡ ቀዳማዊ ፡ እምኔሆሙ ፡ እዴሁ ፡ ዲቤሁ ።
ወይበል ፡ ጸሎተ ፡ ሢመት ፡ ወይበሉ ፡ ኵሉ ፡
ሕዝብ ፡ አሜን ።

፻፪ ሥርዋጽ ፡ ፩ቱ ፡ ጸሎተ ፡ ሢመትሰ ፡ ሀሎ ፡
ውስተ ፡ ክፍል ፡ ዘዘከርነ ፡ ወነዋ ፡ ተሠርዐ ፡
ውስተ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ አሐቲ ፡ መጽሐፈ ፡
ሢመት ፡ ወይእቲ ፡ ወካልእቲሃ ፡ ውስቴታ ፡
ወእምድኅረ ፡ ዝንቱ ፡ የእምኀዎ ፡ ኤጲስቆጶ



ከሹመት ፡ የሚከለከል ፡ ነውር ፡ ቢገኝበት ፡
ይከልከል ። ይህ ፡ ባይሆን ፡ ግን ፡ ይሾም ፡ የከሰ
ሰውም ፡ ባላጋራ ፡ የከሰሰበትን ፡ ባይረታ ፡ ካህን
ቢሆን ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ይለይ ። ሕዝባዊ ፡
ቢሆን ፡ ግን ፡ እንደሚገባ ፡ ይቀጣ ።

፻ ሦስተኛው ፡ ለሹመት ፡ የማያበቃውንና ፡ የማይ
ከለከለውን ፡ ይናገራል ። ረስጠጅ ፡ ፳፪ ፤ አንድ
ዓይና ፡ ወይም ፡ እንከሳ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ ለዚህ ፡
ሥራ ፡ ተስማሚ ፡ ከሆነ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ከመ
ሆን ፡ አይከልከል ። የአካል ፡ ጕድለት ፡ ነውር ፡
አይደለምና ። ነውርስ ፡ የነፍስ ፡ ነውር ፡ ነው ።

፻፩ ሁለተኛው ፡ ክፍል ፡ የሹመቱን ፡ ሥራ ፡ ይናገ
ራል ። ድስቅ ፡ ፴፯ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ በዕለተ ፡ እሑድ ፡
ይሾም ። በሚሾምበትም ፡ ቀን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡
ይገኙ ። ሕዝብና ፡ ካህናት ፡ መስክረውለት ፡
ይሾም ። እጃቸውን ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ሊያኖሩ ፡
የመጡ ፡ ኤጲስቆጶሳትም ፡ እጃቸውን ፡ ይታ
ጠቡ ። ከዚያ ፡ በኋላም ፡ ይሹሙት ። ሕዝቡም ፡
በፍርሃትና ፡ በጸጥታ ፡ ቆመው ፡ እጃቸውን ፡
ያንሡ ። ኤጲስቆጶሳቱም ፡ "እኛ ፡ በዚህ ፡ በተ
መረጠ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ባሪያ ፡ ላይ ፡ እጃች
ንን ፡ እናስቀምጣለን" ፡ እያሉ ፡ በአብ ፡ በወ
ልድ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ስም ፡ እጃቸውን ፡
ያስቀምጡ ። ነውር ፡ በሌለባትና ፡ አንዲት ፡
በሆነች ፡ በማይገለጥ ፡ በሕያው ፡ እግዚአብ
ሔር ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በጸናች ፡ ሥርዓት ፡
ይጸና ፡ ዘንድ ። የቀና ፡ ፍርድን ፡ ለመፍረድ ፡
ምስጋናን ፡ ለማለጥ ፡ ልጅነትን ፡ ለማስጠት ፡
ለታመነች ፡ ትምህርት ፡ ይኸውም ፡ ነገረ ፡
መስቀልን ፡ ለማስተማር ፡ ከሥሉስ ፡ ቅዱስ ፡
ዘንድ ፡ በጉባኤ ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ የተሾመ ፡
ነው ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ከነርሱ ፡ ቀዳሚ ፡ የሆ
ነው ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ እጁን ፡ ይጫንበት ። የሹመ
ቱንም ፡ ጸሎት ፡ ያድርስ ። ሕዝቡም ፡ አሜን ፡
ይበሉ ።

፻፪ ሥርዋጽ ፡ ፩ ። የሹመት ፡ መጽሐፍ ፡ ግን ፡ አስ
ቀድመን ፡ በተናገርነው ፡ ክፍል ፡ አለ ። በቤተ ፡
ክርስቲያን ፡ ውስጥ ፡ አንዲት ፡ የሹመት ፡ መጽ
ሐፍ ፡ እነሆ ፡ ተጽፋለች ። እርሷና ፡ ሌሎችም ፡
በውስጧ ፡ ይገኛሉ ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ኤጲስቆ

ሳት ፡ ወይበሉ ፡ ኵሎሙ ፡ ካህናት ፡ ወሕዝብ ፡
ይደልዎ ፡ ይደልዎ ፡ ይደልዎ ። ወየአምኅዎ ፡
ኵሎሙ ፡ ወይስተበቍዑ ፡ ሎቱ ፡ ሰላመ ።
ወእምዝ ፡ ያንብቡ ፡ ክፍላተ ፡ ዘይደሉ ፡ ወይፌ
ጽሙ ፡ ቅዳሴ ፡ በአስተታልዎ ፡ ወይትመጦ ፡
ውእቱ ፡ ቅድመ ፡ እምሥጢራት ፡ ቅድሳት ።
ወእምዝ ፡ የሀበሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ እምኔሃ ፡ በበ
መዓርጊሆሙ ፡ ወይፌንዎሙ ፡ በሰላም ፡ ወይ
ብሰሉ ፡ ፫ተ ፡ መዋዕለ ፡ በዓለ ፡ መንፈሳዊት ፡
በአምሳለ ፡ ምሥጢሩ ፡ ለዘተንሥአ ፡ በሣል
ስት ፡ ዕለት ።
፺፫ ረስጠብ ፡ ፶ወ፱ቱ ፡ ወእምእመ ፡ ሠምርዎ ፡
ኵሎሙ ፡ ይትጋብኡ ፡ ኵሉ ፡ ሕዝብ ፡ ወቀሳ
ውስት ፡ ወኤጲስቆጶሳት ፡ በዕለተ ፡ እሑድ ፡
ወይስእልዎሙ ፡ ዘየዐቢ ፡ እምኔሆሙ ፡ ለቀሳው
ስት ፡ ወዲያቆናት ፡ ወይበል ፡ ዝንቱ ፡ ዘሠመ
ርክምዎ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ሊቀ ፡ ለክሙ ። ወሶበ ፡
ይቤሉ ፡ እወ ፡ ይስእልዎሙ ፡ ካዕበ ፡ ወይበል ፡
ለዝንቱ ፡ ትደልዎኑ ፡ ሢመት ፡ ክብርት ፡
ወአርትዐኑ ፡ ሕረቶ ፡ በሠናይ ፡ ወበጥዩቅ ፡
ወኢተረክበ ፡ ላዕሌሁ ፡ ምንትኒ ፡ ወለእመ ፡
ተሠጥውዎ ፡ ኵሎሙ ፡ ወይቤሉ ፡ ከመ ፡ ውእቱ
ከመዝ ፡ እሙን ፡ ይደልዎ ፡ ሢመት ፡ በጽድቅ ፡
ወአኮ ፡ በአድልዎ ። ወይስእልዎሙ ፡ ካዕበ ፡
ሥልሰ ፡ እንዘ ፡ ይብል ፡ ድልውኑ ፡ ውእቱ ፡
በአማን ፡ ለዝንቱ ፡ ሢመት ፡ እስመ ፡ ይቀውም ፡
ኵሉ ፡ ቃል ፡ እምአፈ ፡ ፪ቱ ፡ አው ፡ ፫ቱ ። ወለ
እመ ፡ ይቤሉ ፡ በሣልስ ፡ ድልው ፡ ውእቱ ፡ ይስ
ፍሑ ፡ ወይስተጣፍሑ ፡ እደዊሆሙ ፡ ኵሎሙ ።
ወሶበ ፡ ገብሩ ፡ ዘንተ ፡ በተሰናእዎ ፡ ለይኩን ፡
አርምሞ ፡ ወዲያቆናትኒ ፡ ይፁሩ ፡ ወንጌላተ ፡
ቅዱሳተ ፡ ወውእቶን ፡ እንዘ ፡ ክሡታት ፡ ዲበ ፡
ርእሱ ፡ ለዘይሠየምዎ ፡ ወያንብርዎ ፡ ኤጲስ
ቆጶሳት ፡ ዲበ ፡ መንበር ፡ ዘድልው ፡ ሎቱ ፡
ወእምከመ ፡ ተወክፎ ፡ ኵሎሙ ፡ እግዚአብ
ሔርኒ ፡ ተወክፎ ።
፺፬ በስ ፡ ፵ወ፯ቱ ፡ ወኢይሠየም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ዘእ
ንበለ ፡ ይምጽኡ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ እምሀገር ፡ ወአኮ ፡
ውእቱ ፡ ባሕቲቱ ፡ አላ ፡ ፪ቱኒ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡
ካልአን ፡ ምስሌሁ ። ወይሠየም ፡ እምነ ፡ ፫ቱ ፡
ኤጲስቆጶሳት ፡ ወከመዝ ፡ ይሠየም ፡ እንዘ ፡ ይፀ
ሙሩ ፡ ወንጌለ ፡ ዲበ ፡ ርእሱ ። ወይጼሊ ፡ ላዕ
ሌሁ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ዘየዐቢ ፡ ከመዝ ። ወሶበ ፡

ጳሳቱ ፡ እጅ ፡ ይንሡት ። ሕዝቡና ፡ ካህናቱም ፡
ይገባዋል ፡ ይገባዋል ፡ ይገባዋል ፡ ይበሉ ። ሁላ
ቸውም ፡ እጅ ፡ ይንሡት ። በአንተ ፡ ሰላምን ፡ ይጸ
ልዩለት ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሊነበብ ፡ የሚገባውን ፡
ክፍል ፡ ያንብቡ ። አከታትለውም ፡ ቅዳሴውን፡
ይፈጽሙ ። አስቀድሞ ፡ እርሱ ፡ ሥጋውንና ፡
ደሙን ፡ ይቀበል ። ከዚያም ፡ በኋላ ፡ በየማዕረጋ
ቸው ፡ ለሁሉም ፡ ሥጋውንና ፡ ደሙን ፡ ያቀብላ
ቸው ። በሰላምም ፡ ያሰናብታቸው ። በሦስተኛ ፡
ቀን ፡ በተነሣው ፡ በጌታ ፡ ትንሣኤ ፡ አምሳል ፡
፫ ፡ ቀን ፡ መንፈሳዊ ፡ በዓልን ፡ ያክብሩ ።
፺፫ ረስጠብ ፡ ፶፱ ። ሁሉም ፡ ከመረጡት ፡ በኋላ ፡
ሕዝቡና ፡ ቀሳውስቱ ፡ ዲያቆናቱ ፡ ኤጲስቆጶሳ
ቱም ፡ በዕለተ ፡ እሑድ ፡ ይሰብሰቡ ። ከነርሱ ፡
የሚበልጠው ፡ አለቃ ፡ ይሆናችሁ ፡ ዘንድ ፡ የመ
ረጣችሁት ፡ ይህ ፡ ነውን ፡ ብሎ ፡ ቀሳውስቱ
ንና ፡ ዲያቆናቱን ፡ ይጠይቃቸው ። አዎን ፡ ቢሉ
የከበረችው ፡ ሹመት ፡ ለዚህ ፡ ትገባዋለችን ፡
ይበል ። በሚገባና ፡ በተረዳ ፡ ሥርዓት ፡ አኗኗ
ሩን ፡ አጽንቷልን ፡ ምንም ፡ በደል ፡ አልተገኘ
በትምን ፡ ይበል ። እነርሱም ፡ መልሰው ፡ እን
ደዚህ ፡ እንደሆነ ፡ ቢናገሩ ፡ በማድላት ፡ ያይደለ
በእውነት ፡ ሹመት ፡ ይገባዋል ። ሦስተኛ ፡ ደግ
ሞ ፡ ለዚህ ፡ ሹመት ፡ በእውነት ፡ ይገባ
ልን ፡ ብሎ ፡ ይጠይቃቸው ። ነገር ፡ ሁሉ ፡ በሁ
ለት ፡ ወይም ፡ በሦስት ፡ ምስክር ፡ ይጸናልና ።
በሦስተኛውም ፡ ጊዜ ፡ ይገባዋል ፡ ቢሉ ፡ ሁሉ
ም ፡ እጃቸውን ፡ ዘርግተው ፡ ያጨብጭቡ ። ይህ
ንን ፡ በስምምነት ፡ ካደረጉ ፡ በኋላ ፡ ጸጥታ ፡
ይሁን ። ዲያቆናትም ፡ ቅዱሳት ፡ ወንጌላትን ፡
ገልጠው ፡ በተሾመው ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ ይያዙ ።
ኤጲስቆጶሳቱም ፡ ለርሱ ፡ በሚገባው ፡ ወንበር ፡
ያስቀምጡት ። ሁሉም ፡ ከተቀበሉት ፡ እግዚአ
ብሔርም ፡ ይቀበለዋል ።
፺፬ በስ ፡ ፵፯ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ከሌላ ፡ አገር ፡ ሳይ
መጣ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ አይሾም ። እርሱ ፡ ብቻ ፡
አይደለም ። ሌሎችም ፡ ሁለት ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡
ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ይኑሩ ። በሦስት ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡
ይሾም ። እንደዚህ ፡ ይሾም ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ወን
ጌልን ፡ ተሸክመው ። የበለጠው ፡ ኤጲስቆጶስ ፡
እንደዚህ ፡ ይጸልይ ። ጸሎቱን ፡ ከጨረሰ ፡ በኋላ፡

ፈጸሀ ፡ ያንብቦ ፡ እዴሁ ፡ ላዕሌሁ ፡ ወይስዓሞ ፡
ወይንፋሕ ፡ ውስተ ፡ ገጹ ፡ ከመ ፡ ይትመላእ ፡
ላዕሌሁ ፡ መንፈሰ ፡ ቅዱስ ። ወእምድኅረ ፡
ዝንቱ ፡ የእምኆዎ ፡ እለ ፡ ተርፉ ፡ ካህናት ፡
ወጸታ ፡ ሕዝብሰ ፡ ይስዓሙ ፡ እዴሁ ፡ ወኢየእ
ምኑ ፡ አፉሁ ፡ ዘእንበለ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ወቀ
ሳውስት ፡ እምድኅረ ፡ ዝንቱ ፡ ይፈጽሙ ፡ ቀዳሴ።
፳፭ ድስቅ ፡ ፴ወ፩ቱ ፡ ወንኤዝዘክሙ ፡ ከመ ፡ ይሠ
የም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ እምኖቱ ፡ ኤጲስቆጶሳት ።
ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ዓጸባ ፡ እምኔቱ ፡ ኤጲስቆጶ
ሳት ። ወኢይደሉ ፡ ከመ ፡ ይሠየም ፡ ለከሙ ፡
እምፅዱ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ እስመ ፡ ስምዐ ፡ ፪ቱ ፡
እው ፡ ፫ቱ ፡ ይከውን ፡ ቀዋሚ ። ረስጣ ፡ ፶ወ
፰ቱ ፡ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ውእቱ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡
አሐዱ ፡ ዘአንበረ ፡ እደሁ ፡ ላዕሌሁ ፡ ይትፈ
ለጥ ፡ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ዝንቱ ፡ በእንተ ፡ ዓጸባ ፡
በግብር ፡ ወለእመ ፡ ኢተከህለ ፡ ከመ ፡ ይትጋ
ብኡ ፡ ማኅበር ፡ በእንተ ፡ ስደት ፡ ዘለወቅ ፡
እው ፡ በምክንያት ፡ ካልእ ፡ ዘከመዝ ፡ ወይኩን ፡
ዘተንእደ ፡ እምብዙኃን ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ወያ
ብሕዎ ፡ ሎቱ ፡ ዝንቱ ፡ ወይኩን ፡ በትእዛዞሙ ።
፳፮ ወገጽ ፡ ሣልስ ፡ እምድኅረ ፡ ተሠይሞቱ ፡ ወዝ
ንቱ ፡ ይትከፈል ፡ ኀበ ፡ ፰ቱ ፡ መክፈልታት ፡
ቀዳሚ ፡ ዘይደልዎ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ይግበር ፡ በር
እሱ ። ድስቅ ፡ ፳ወ፫ቱ ፡ ወእምከመ ፡ ተሠይመ ፡
ኤጲስቆጶስ ፡ ይንበር ፡ ፫ተ ፡ ሰባዔያተ ፡ በጾም ፡
ወኢይጥዐም ፡ ምንተኒ ፡ ዘእንበለ ፡ በዕለተ ፡
ሰንበት ፡ እምነ ፡ ኵሉ ፡ ሰባዔ ፡ ዝንቱ ፡ ለእመ ፡
ኢኮነ ፡ በመዋዕለ ፡ ፶ ፡ እምዝኒ ፡ ይፈጽም ፡
ይእተ ፡ ዓመተ ፡ በጾም ፡ በበ ፡ ሠለሰቱ ፡ ሠለ
ሰቱ ።
፳፯ ሥርዋጽ ፡ ፳ቱ ፡ ይመስለኒ ፡ ዘይቤ ፡ ከመ ፡
ይጹም ፡ ለለኵሉ ፡ ሰበት ፡ እስከ ፡ ተፍጻሜተ ፡
መዓልት ፡ እምዕለተ ፡ ሰንበት ፡ እስከ ፡ ዕለተ ፡
ሰንበት ፡ ፫ተ ፡ ሰባዔ ። ወዘተርፈ ፡ ዓመተ ፡
ይጹም ፡ በበኵሉ ፡ ሰባዔ ፡ ፫ተ ፡ ዕለታተ ፡
ረቡዐ ፡ ወዓርበ ፡ ወሰኑየ ። እስመ ፡ በሰንበት ፡
ወበእሑድ ፡ እልቦ ፡ ጾም ፡ ወኢይትፌጸምኒ ፡
ዘበኵሉ ፡ ሰባዔ ፡ ዘጸዊም ፡ በበ፫ቱ ፡ ፫ቱ ፡
ዕሙረ ፡ እላ ፡ ዘይትፌጸምሰ ፡ በትርጓሜ ፡ ዘቀ
ደመ ፡ ዘከሮቱ ።
፳፰ ወይኩን ፡ መብልዑ ፡ ለኤጲስቆጶስ ፡ ዘይበልዖ ፡



እጁን ፡ ይጫንበት ፡ ይሳመውም ። መንፈስ ፡
ቅዱስም ፡ ይመላበት ፡ ዘንድ ፡ በፊቱ ፡ እፍ ፡ ይበ
ልበት ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የቀሩት ፡ ካህናት ፡
እጅ ፡ ይንሡት ። ሕዝቡ ፡ ግን ፡ እጁን ፡ ይሳ
ሙት ። ከኤጲስቆጶሳቱና ፡ ከቀሳውስቱ ፡ በቀር ፡
አፉን ፡ አይሳሙት ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ቅዳሴውን ፡
ይፈጽሙ ።
፳፭ ድስቅ ፡ ፴፩ ። ኤጲስቆጶስ ፡ ከሦስት ፡ ኤጲስቆጶ
ሳት ፡ ይሾም ፡ ዘንድ ፡ እናዝዛችኋለን ። የችግር ፡
ዘመን ፡ ቢሆን ፡ ግን ፡ ከ፪ኤጲስቆጶሳት ፡ ይሾም።
ከአንድ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ግን ፡ ሊሾምላችሁ ፡ አይ
ገባም ። የሁለትና ፡ የሦስት ፡ ምስክርነት ፡ የጸና ፡
ይሆናልና ። ረስጣ ፡ ፶፰ ። አንድ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡
ብቻውን ፡ የሾመ ፡ ከሆነ ፡ ይለይ ። ይህ ፡ በች
ግር ፡ ምክንያት ፡ ቢሆን ፡ በታወቀ ፡ ስደት ፡
ምክንያት ፡ ወይም ፡ ይህን ፡ በመሰለ ፡ በሌላ ፡
ምክንያት ፡ ማኅበር ፡ ለመሰብሰብ ፡ ባይችሉ ፡
በብዙዎች ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ የተመሰገነ ፡ ይሁን።
ይህንንም ፡ በትእዛዛቸው ፡ ይፍቀዱለት ።

፳፮ ሦስተኛውም ፡ ክፍል ። ከተሾመ ፡ በኋላ ፡ የሚ
ሠራውን ፡ ይናገራል ። ይኸውም ፡ በ፰ ፡ ክፍ
ሎች ፡ ይከፈላል ። መጀመሪያው ፡ ለራሱ ፡ ሊሠ
ራው ፡ የሚገባውን ፡ ይናገራል ። ድስቅ ፡ ፳፫ ፡
ኤጲስቆጶስ ፡ ከተሾመ ፡ በኋላ ፡ ሦስት ፡ ሱባዔ ፡
ይጹም ። በሰንበት ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡
ሱባዔውን ፡ ሁሉ ፡ ምንም ፡ ሳይቀምስ ፡ ይጹም።
ይህም ፡ የሚሆነው ፡ ሹመቱ ፡ በበዓለ ፡ ፶ ፡ ካል
ሆነ ፡ በቀር ፡ ነው ። ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ይህችን ፡
ዓመት ፡ በሳምንቱ ፡ ውስጥ ፡ ፫ ፡ ፫ ፡ ቀን ፡ እየ
ጾመ ፡ ይጨርስ ።
፳፯ ሥርዋጽ ፡ ፳ ። ከዕለተ ፡ ሰንበት ፡ እስከ ፡ ዕለተ ፡
ሰንበት ፡ ድረስ ፡ ሦስቱን ፡ ሱባዔ ፡ እስከ ፡ ፲፪ ፡
ሰዓት ፡ ይጹም ፡ ያለ ፡ ይመስለኛል ። በዕለተ ፡
ቀዳሚትና ፡ በዕለተ ፡ እሑድ ፡ ጾም ፡ የለምና ።
የቀረውን ፡ ዓመት ፡ ግን ፡ በሳምንት ፡ ፫ቱን ፡
ቀን ፡ ረቡዕን ፡ ዓርብንና ፡ ሰኞን ፡ ይጹም ፡ ያለ ፡
ይመስለኛል ። በየሱባዔው ፡ ሦስት ፡ ሦስቱን ፡
አንድ ፡ ወገን ፡ አድርጎ ፡ በመጾም ፡ አይፈጸ
ምም ። የሚፈጸምስ ፡ አስቀድመን ፡ በተናገር
ነው ፡ ትርጓሜ ፡ ቢሆን ፡ ነው ።
፳፰ ኤጲስቆጶስ ፡ በጾሙ ፡ ወራት ፡ የሚመገበው ፡

በዓመተ ፡ ጾሙ ፡ ኅብስት ፡ ወጼው ፡ ወዘይት ፡
ወመዓር ፡ ወእሕማላተ ፡ ምድር ፡ ወይነል ፡ ኢይ
ጥዐም ፡ ወበተረፈ ፡ መዋዕለ ፡ ሕይወቱሰ ፡
ይጹም ፡ በአምጣነ ፡ ክሂሎቱ ። ወይትመጠ ፡
እምነ ፡ መብልዕ ፡ ዘዓጸባ ፡ መጠነ ፡ ዓቅሙ ፡
ወኢይብላዕ ፡ ሥጋ ፡ ለዓለም ፡ እስ ፡ እስመ ፡
ውእቱ ፡ ለእመ ፡ በልዖ ፡ ዘያረኵሶ ፡ አላ ፡ ከመ ፡
ኢይግዝፍ ፡ ልቡ ፡ ወኢያጽልም ፡ አእምሮቱ ፡
ወኢይትከሀሎ ፡ ከመ ፡ ይትጋሀ ፡ በዕረፍት ።
እስመ ፡ ዘየኀሥሥ ፡ ከመ ፡ ይፈጽም ፡ ዘንተ ፡
ግብረተ ፡ ከመዝ ፡ ይኅረይ ፡ ሎቱ ፡ ጽሙና ፡
ወዘይትዌከፍ ፡ ጽሙና ፡ ኢይትዌከፍ ፡ ሎቱ ፡
ረባኀ ፡ ከመ ፡ ይትመጠ ፡ ዘያጸንዕ ፡ ሥጋ ።
፻፱ ወለእመ ፡ ደወየ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ በይእቲ ፡
ዓመት ፡ ደዌ ፡ ዘኢይትከሀሎ ፡ በእንቲአሁ ፡
ከመ ፡ ይፈጽም ፡ ዘበህልናሁ ፡ ይብላዕ ፡ ዓሣ ፡
ወይስተይ ፡ እምወይን ፡ በዓቅም ፡ ኅዳጠ ፡ መዋ
ዕለ ፡ ከመ ፡ ኢይኩን ፡ ውዱቀ ፡ ወኢትኅጣእ ፡
ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ምግባሪሁ ፡ ወትምህርቶ ፡
ወይጽሐቅ ፡ ከመ ፡ ይትመጠ ፡ በኵሉ ፡ ዕለት ፡
ምሥጢራተ ፡ ለእመ ፡ ኢክልአ ፡ ምክንያት ፡
ከመ ፡ ይሕየው ፡ ባቲ ፡ በኵሉ ፡ ዘመን ።
፻፲ ረቡዕ ፡ ፴ወ፪ቱ ፡ ወኢይደልዎ ፡ ለኤጲስቆጶስ ፡
ከመ ፡ ይጹም ፡ ዘእንበለ ፡ በዕለት ፡ ዘይጸውሙ ፡
ቦቱ ፡ ኵሉ ፡ ሕዝብ ። እስመ ፡ ውእቱ ፡ ለእመ ፡
መጽአ ፡ ኀበ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ወአምጽአ ፡
አሐዱ ፡ ምንተኒ ፡ ኀበ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ይት
ፈቀድ ፡ ከመ ፡ ይብላዕ ፡ ምስለ ፡ ማኅበር ።
፻፲፩ ድስቅ ፡ ፩ቱ ፡ ወይትመጠ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ እመ
ብልዕ ፡ ወመስቴ ፡ ዘየአክሎ ፡ ለሕይወቱ ፡ ከመ፡
ይክሀል ፡ ወከመ ፡ ኢይትሀከይ ፡ ምሂሮቶሙ ፡
ለእለ ፡ ኢኮኑ ፡ ምሁራነ ፡ ወኢያስተዋፅእ ፡
ብዙኀ ፡ ወኢይኩን ፡ ፍሉስ ፡ ወኢዘያንጌጊ ፡
ወሐረቱኒ ፡ ኢይኩን ፡ በትፍግዕት ። ወኢይብ
ላስ ፡ ምንተኒ ፡ ኅሩየ ፡ ወይኩን ፡ ሕያወ ፡ ልብ ፡
በውስተ ፡ ትምህርት ፡ ወይምሀር ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ፡
ወያንብብ ፡ መጻሕፍተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወይ
ጠይቅ ፡ አክፋለ ፡ ከመ ፡ ይተርጐም ፡ መጻሕ
ፍተ ፡ በጥያቄ ፡ ወይተርጕም ፡ ወንጌለ ፡ ወይተ
ርጕም ፡ አሪተ ፡ ወነቢያተ ። ይቤ ፡ እግዚእ ፡
"ኅሡ ፡ ትርአዩ ፡ መጻሕፍተ ፡ እስመ ፡ እማንቱ፡
ስምዐ ፡ ይከውና ፡ በእንቲአየ" ። ወኢይፍቅድ ፡
ረባኀ ፡ ማኅበር ፡ ዘያስተኃፍር ፡ ፈድፋደሰ ፡



ምግብ ፡ ዳቦ ፡ ጨው ፡ ዘይት ፡ ማር ፡ ቅጠላቅ
ጠል ፡ ይሁን ። ወይን ፡ ግን ፡ አይጠጣ ። በቀረ ፡
ዘመኑ ፡ ግን ፡ በተቻለው ፡ መጠን ፡ ይጹም ።
ከምግብ ፡ ለዐቅመ ፡ ሥጋ ፡ ያህል ፡ ይመገብ ፡
ሥጋ ፡ ግን ፡ ለዘለዓለም ፡ አይብላ ። ቢበላው ፡
የሚያረክሰው ፡ ሁኖ ፡ አይደለም ። ልቡናው ፡
እንዳይደነድን ፡ አእምሮው ፡ እንዳይዝግ ፡ በዕ
ረፍት ፡ ሁኖ ፡ ለሥራ ፡ ለመትጋት ፡ ስለማይቻ
ለው ፡ ነው ፡ እንጂ ። ይህን ፡ ሥራ ፡ ለመፈጸም ፡
የሚሻ ፡ ሰው ፡ ከምግብ ፡ መለየት ፡ ያሻዋልና ።
ጽሙናንም ፡ የተቀበለ ፡ ሰው ፡ ትርፍ ፡ ገንዘብ ፡
አይሻምና ፡ ለቁመተ ፡ ሥጋ ፡ ያህል ፡ መቀበል ፡
ይገባዋል ፡ እንጂ ።
፻፱ ኤጲስቆጶስ ፡ ያዘዝነውን ፡ ይፈጽም ፡ ዘንድ ፡
የማያስችለው ፡ ደዌ ፡ በዚችው ፡ ዓመት ፡ ቢታ
መም ፡ ዓሣ ፡ ይብላ ። ወይንም ፡ በመጠኑ ፡
ይጠጣ ፡ ለጥቂት ፡ ጊዜ ፡ ወድቆ ፡ እንዳይኖር ።
ቤተ ፡ ክርስቲያንም ፡ አስተዳደሩንና ፡ ትምህር
ቱን ፡ እንዳታጣ ። ምክንያት ፡ ካልከለከለው ፡
በቀር ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፡ ሥጋውንና ፡ ደሙን ፡
ለመቀበል ፡ ይትጋ ። ባለው ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡
ሕያው ፡ ሁኖ ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ።
፻፲ ረቡዕ ፡ ፴፪ ። ሕዝቡ ፡ በማይጾምበት ፡ ጊዜ ፡
ካልሆነ ፡ በቀር ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ መጾም ፡ አይገባ
ውም ። እርሱ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ቢመጣ፡
አንድ ፡ ሰውም ፡ ምግብ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲ
ያን ፡ ቢያመጣ ፡ ከማኅበሩ ፡ ጋር ፡ ይብላ ፡ ዘንድ፡
ይገባዋልና ።
፻፲፩ ድስቅ ፡ ፩ ። ኤጲስቆጶስ ፡ ከምግብና ፡ ከመጠጥ ፡
ለቁመተ ፡ ሥጋ ፡ ያህል ፡ ይውሰድ ። ያልተማሩ
ትን ፡ ለማስተማር ፡ እንዲችል፡ ቸልም ፡ እንዳ
ይል ፡ አብዝቶም ፡ አያወጣጣ ፡ ዘዋሪ ፡ ሰውንም
የሚበድል ፡ አይሁን ። አኗኗሩም ፡ በተድላ ፡
በደስታ ፡ አይሁን ። የላመ ፡ የጣመ ፡ አይቅመስ ።
በማስተማር ፡ ጊዜ ፡ ትጉ ፡ ይሁን ፡ ዘወትር ፡
ያስተምር ። የእግዚአብሔርንም ፡ መጻሕፍት ፡
ይመልከት ። መጻሕፍትን ፡ አስረድቶ ፡ ይተረ
ጕም ፡ ዘንድ ፡ ክፍል ፡ ክፍሉን ፡ በጥያቄ ፡ ለይቶ
ይወቀው ። ወንጌልን ፡ኦሪትንና ፡ ነቢያትን ፡
ይተርጕም ። ጌታችን ፡ "መጻሕፍትን ፡ ተመል
ከቱ ፡ እነርሱ ፡ ስለኔ ፡ ይመሰክራሉና" ፡ አለ ።
(ዮሐ ፡ ፭ ፡ ፴፱ )። የሚያሳፍር ፡ የማኅበርን ፡
ትርፍ ፡ አይውደድ ። ይልቁንም ፡ ከዓላውያን ፡

ምስለ ፡ ዓላውያን ። ወኢይፍቅድ ፡ መክፈልተ ፡ ዘየዐቢ ፡ ወኢይኩን ፡ ተዓጋሌ ፡ ወኢመፍቀሬ ፡ አብዕልት ፡ ወጸላኤ ፡ ነዳያን ፡ ወኢያፍቅሮ ፡ በዓለ ፡ ውዴት ፡ ወኢይኩን ፡ ስምዐ ፡ በሐሰት ፡ ወኢቍጡዐ ፡ ወኢይትሐበይ ፡ ፩ደኒ ፡ ወኢያፍቅር ፡ ሢመተ ፡ ወኢይኩን ፡ ዘ፪ኤ ፡ ልቡ ፡ ወ፪ኤ ፡ ልሳኑ ፡ ወኢስማዔ ፡ ወኢያሑር ፡ ኀበ ፡ በዓላተ ፡ አሕዛብ ፡ ወኢፈታዌ ፡ ወኢመፍቀሬ ፡ ንዋይ ። እስመ ፡ እሉ ፡ ግብራት ፡ ኵሎሙ ፡ ጸላእት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ወሱቱፋኒሆሙ ፡ ለሰይጣናት ። ወይኩን ፡ ጠቢበ ፡ ወለባዌ ፡ ከመ ፡ ያእምር ፡ እኩየ ፡ ወይትዐቀብ ፡ እምኔሁ ፡ ወይኩን ፡ ፍቁረ ፡ ለኵሉ ፡ ወለኵሉ ፡ ግብር ፡ ሠናይ ፡ ዘሀሎ ፡ ላዕለ ፡ ሰብእ ፡ ለይርብሖ ፡ ለነፍሱ ፡ እስመ ፡ ኖላዊ ፡ ለእመ ፡ ርኅቀ ፡ እምዓመፃ ፡ ይስሕቦሙ ፡ ለአርዳኢሁ ፡ ወያስተናሥእሙ ፡ ከመ ፡ ይኩኑ ፡ ተመሳልያነ ፡ በምግባራቲሁ ፡ ሠናያት ፡ በአማን ። በከመ ፡ ይቤ ፡ ሆሴዕ ፡ ነቢይ ፡ "እስመ ፡ በከመ ፡ ይከውን ፡ ካህን ፡ ከማሁ ፡ ካዕበ ፡ ሕዝብኒ" ፡ ወዓዲ ፡ መምህርነ ፡ ኄር ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ አምላክነ ፡ ወጠነ ፡ ቅድመ ፡ ከመ ፡ ይግበር ፡ ወይምሀር ፡ ወይቤ ፡ "እስመ ፡ ዘይገብር ፡ ወይሜህር ፡ ዐቢየ ፡ ይሰመይ ፡ በመንግሥተ ፡ ሰማያት" ።

፻፲፪ ዘ፴ወ፰ቱ ፡ ወእምድኅረ ፡ ተሠይሞቱ ፡ ይዐመድ ፡ ውስተ ፡ ምሥዋዕ ፡ ወይጸሊ ፡ መዓልተ ፡ ወሌሊተ ። ወለእመ ፡ ጸለየ ፡ በእንተ ፡ ነፍሱ ፡ ወበእንተ ፡ ኵሉ ፡ ሕዝብ ፡ በኵሉ ፡ ሰዓት ፡ ሠናየ ፡ ገብረ ። ወየሀሉ ፡ ባሕቲቱ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ሎቱ ፡ ዘየሠምሮ ፡ ለነቢር ፡ ምስሌሁ ፡ እመ ፡ አኮ ፡ አሐዱ ፡ አው ፡ ፪ቱ ፡ ወውእቶሙ ፡ አሐቲ ፡ ነፍስ ፡ ምስሌሁ ፡ ይግበር ፡ በዘይትራድእዎ ፡ በእንተ ፡ ዘይደሉ ። ወፈድፋደስ ፡ ዘየዐቢ ፡ በእንተ ፡ ፍጻሜ ፡ ጸሎት ፡ ወተሰናእዎ ፡ ወበእንጻሮ ፡ በእንተ ፡ አስተበቍዖተ ፡ ሰንእ ፡ አሐዱ ። እስመ ፡ እግዚእነ ፡ ይቤ ፡ "ኀበ ፡ ሀለዉ ፡ ፪ቱ ፡ አው ፡ ፫ቱ ፡ ጉቡአነ ፡ በስምየ ፡ እነ ፡ እሄሉ ፡ ምስሌሆሙ" ። ወለእመ ፡ ኢይትከሀሎ ፡ አዝልፎት ፡ ይጸሊ ፡ ሰዓታተ ። ዘ፴ወ፰ቱ ፡ ወያስተብቍዖ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በኵሉ ፡ ልብ ፡ ወበኵሉ ፡ ድካም ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ቃሉ ፡ ዘይ

ጋር ፡ የሆነውን ፡ አይውደድ ። አብልጡልኝ ፡ አይበል ። ቀማኛ ፡ አይሁን ፡ ድሆችን ፡ የሚጠላ ፡ ባለጠጎችን ፡ የሚወድ ፡ አይሁን ። ነገረ ፡ ሠሪ ፡ አይውደድ ። በሐሰት ፡ አይመስክር ፡ ቍጡ ፡ አይሁን ፡ ለአንዱ ፡ ሰው ፡ እንኳ ፡ አይ ኰሽ ፡ ሹመትን ፡ አይውደድ ። ሁለት ፡ ልብ ፡ አይሁን ። ሁለት ፡ ምላስ ፡ አይሁን ። ነገረ ፡ ሠሪን ፡ የሚሰማ ፡ አይሁን ። ወደ ፡ አሕዛብ ፡ በዓል ፡ አይሂድ ። ገንዘብ ፡ ወዳጅ ፡ አይሁን ። ቀማኛም ፡ አይሁን ። እነዚህ ፡ ሥራዎች ፡ ሁሉ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ጠላቶች ፡ የሰይጣናት ፡ ተባባሪዎች ፡ ናቸውና ። ክፉን ፡ አውቆ ፡ ከርሱ ፡ ይጠበቅ ፡ ዘንድ ፡ ብልህና ፡ አስተዋይ ፡ ይሁን ። ለሁሉ ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ መልካም ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ የሚወድ ፡ ይሁን ። እርሱን ፡ ራሱን ፡ ይጥቀም ። ጠባቂ ፡ ከዓመፃ ፡ ቢርቅ ፡ ደቀ ፡ መዛሙርቱን ፡ ይስባቸዋልና ። በእውነትም ፡ የበጎ ፡ ምግባር ፡ ተከታዮች ፡ እንዲሆኑ ፡ ያነቃቃቸዋልና ። ነቢዩ ፡ ሆሴዕ ፡ "ካህኑ ፡ እንደ ሆነ ፡ ሕዝቡም ፡ ይሆናል ፡ ብሏልና ። (ሆሴ ፡ ፬ ፡ ፱) ። ዳግመኛም ፡ ደጉ ፡ መምህራችን ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ አስቀድሞ ፡ ሠርቶ ፡ ያስተምር ፡ ጀመረ ።" እየሠራ ፡ የሚያስተምርም ፡ በመንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ታላቅ ፡ ይባላል" ፡ አለ ። (ማቴ ፡ ፭ ፡ ፲፱) ።

፻፲፪ ድስቅ ፡ ፴፰ ። ከተሾመ ፡ በኋላም ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡ ውስጥ ፡ ዕሙድ ፡ ይሁን ። በመዓልትም ፡ በሌሊትም ፡ ይጸልይ ። ስለ ፡ ራሱና ፡ ስለ ፡ ሕዝቡ ፡ በየሰዓቱ ፡ ቢጸልይ ፡ መልካም ፡ አደረገ ። በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ብቻውን ፡ ይኑር ። ብቻውን ፡ መኖር ፡ ደስ ፡ የሚያሰኘው ፡ ከሆነ ፡ ይህ ፡ ግን ፡ ባይሆን ፡ ከአንድ ፡ ወይም ፡ ከሁለት ሰዎች ፡ ጋር ፡ ይኑር ። እነርሱ ፡ ከርሱ ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ አካል ፡ ናቸውና ። ስለሚገባው ፡ በሚረዱት ፡ ገንዘብ ፡ ያድርግ ። ይልቁንም ፡ የሚበልጠው ፡ በጸሎትና ፡ በስምምነት ፡ በማሳጠርም ፡ አንድ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በመለመን ፡ ነው ። ጌታ ፡ "ሁለት ፡ ወይም ፡ ሦስት ፡ ሁነው ፡ በኔ ፡ ስም ፡ ተሰብስበው ፡ ካሉበት ፡ እኔ ፡ በመካከላቸው ፡ እኖራለሁ" ፡ (ማቴ ፡ ፲፰ ፡ ፳) ። ብሏልና ። ሳያቋርጥ ፡ መጸለይ ፡ ባይቻለው ፡ በተወሰኑት ፡ ሰዓቶች ፡ ይጸልይ ። ድስቅ ፡ ፴፰ ። በፍጹም ፡ ልብ ፡ በፍጹም ፡ ድካም ፡ እግዚአብሔ

ብሎ ፡ ኪያሁ ፡ ይፈርይ ፡ ውስተ ፡ ስማስያኒሁ ፡ ፍሬ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ። ዘ፳ወ፫ቱ ፡ ወኵሎ ፡ ቃለ ፡ ዘይሜህር ፡ ይደልዎ ፡ሎቱ ፡ ከመ ፡ ያእ ምር ፡ ወይዝክር ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡ ገብሮ ፡ ቀዳሚ እምቅድመ ፡ ይምሀሮ ፡ ከመ ፡ ያእምር ፡ ዘይ ብሎ ፡ በዙሱ ፡ ሐተታ ። እስመ ፡ ውእቱ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ የአምር ፡ ዘይብሎ ፡ እለኒ ፡ ይሰም ዕዎ ፡ የአምሩ ፡ ዘይብሎሙ ።

ወዳግማዊ ፡ በእንተ ፡ ዘይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይግበሮ ምስለ ፡ ሕዝቡ ፡ ወዘይኤዝዞሙ ፡ ቦቱ ። ይቤሎ፡ ጳውሎስ ፡ ሐዋርያ ፡ ለጢሞቴዎስ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ረድኡ ፡ ዘ፫ቱ ፡ እስእለከ ፡ አኑ ፡ ቀዳሜ ፡ ኵሉ ፡ በምንትኒ ፡ ግብር ፡ ከመ ፡ ታቅድም ፡ አቅርቦ ፡ ስኢል ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ በጸሎት ፡ ወአስ ተብቍዖት ፡ ወአኰቴት ፡ በእንተ ፡ ኵሉ ፡ ሰብእ ፡ ከመ ፡ ይንበሩ ፡ በትዕግሥት ፡ ወበህድ ኣት ፡ በአርምሞ ፡ ወበፍርሃተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወበንጽሕ ። እስመ ፡ እሉን ፡ ግብራት ፡ ያበ ጽሓ ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ ማሕየዊ ፡ ዘያፈ ቅር ፡ ከመ ፡ ይሕየዉ ፡ ኵሉ ፡ ሰብእ ፡ ወያብ ጽሑ ፡ ኀበ ፡ አእምሮተ ፡ ጽድቅ ።

ዘ፫ቱ ፡ ወኩኖሙ ፡ አምሳለ ፡ ለምእመናን ፡ በቃል ፡ ወገድል ፡ ወበፍቅር ፡ ወበሃይማኖት ፡ ወንጽሕ ፡ እስከ ፡ አመጽእ ፡ ተዐቀብ ፡ በአን ብቦ ፡ ወበምሂር ፡ ወበገሥፆ ፡ ወኢታስትት ፡ ጸጋሁ ፡ ዘላዕሌከ ፡ ዘወሀበከ ፡ ምስለ ፡ ትንብዮ ፡ ወምስለ ፡ ሢመተ ፡ እደዊሆሙ ፡ ለጳጳሳት ፡ ዑቅ ፡ ወሀሉ ፡ ላዕሌሆሙ ። እስመ ፡ ለእመ ፡ ገበርከ ፡ አንተ ፡ ዘንተ ፡ ታሐይዋ ፡ ለነፍስከ ፡ ወለእለ ፡ ይሰምዑከ ። ወልሂቃነ ፡ ኢታመኵጽ ፡ አላ ፡ ስእል ፡ ኀቤሆሙ ፡ ወናዝዞሙ ፡ ወአስተፍሥ ሖሙ ፡ ከመ ፡ አብ ። ወለወራዙት ፡ ከመ ፡ አኃ ዊከ ፡ ወለሰብኢራት ፡ ከመ ፡ እማቲከ ፡ ወለውርዙ ዋት ፡ ከመ ፡ አኃቲከ ፡ በኵሉ ፡ ንጽሕ ፡ ወክ ብር ። ወለእንለ ፡ ማውታ ፡ ወለመበለታት ፡ ግበር ፡ በጽድቅ ፡ ወኢትትወከፍ ፡ ውዴተ ፡ በላዕለ ፡ ቀሲስ ፡ ዘእንበለ ፡ በስምዐ ፡ ፪ቱ ፡ እደው ፡ አው ፡ ፫ቱ ፡ ወገሥፆሙ ፡ ለእለ ፡ ይኤ ብሱ ፡ በቅድመ ፡ መኳንንት ፡ ከመ ፡ ይፍርሁ ፡ ኵሉ ፡ ሰብእ ። ወኢትግበር ፡ ምንተኒ ፡ በአድ

ርን ፡ ይሰምነው ። የሚያስተምረው ፡ ትምህ ርት ፡ በስሚዎቹ ፡ ዘንድ ፡ የመንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ ፍሬ ፡ ያፈራ ፡ ዘንድ ። ድስቅ ፡ ፳፫ ። የሚያስተ ምረውን ፡ ትምህርት ፡ ሁሉ ፡ እርሱ ፡ እንደሠ ራው ፡ አስተማረው ፡ ማወቅ ፡ ይገባዋል ። በመ ጀመሪያ ፡ አውጥቶ ፡ አውርዶ ፡ የሚያስተምረ ውን ፡ ያውቀው ፡ ዘንድ ። እርሱ ፡ የሚያስተም ረውን ፡ ካወቀ ፡ የሚሰሙትም ፡ የሚላቸውን ፡ ያውቃሉና ።

፻፲፫ ሁለተኛው ፡ ከሕዝቡ ፡ ጋር ፡ ሊያደርገው ፡ የሚ ገባውንና ፡ በርሱ ፡ የሚአዛቸውን ፡ ይናገራል ። ሐዋርያው ፡ ጳውሎስ ፡ ደቀመዝሙሩ ፡ ለነበ ረው ፡ ለኤጲስቆጶስ ፡ ጢሞቴዎስ ፡ በ፫ኛው ፡ ክፍል ፡ እንዲህ ፡ አለው ። (፩ ፡ ጢሞ ፡ ፪ ፡ ፩-፬ ። ፬ ፡ ፲፩-፲፯ ። ፭ ፡ ፩-፲) ። ስለ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በማ ናቸውም ፡ ሥራ ፡ በምትጸልይበት ፡ ጊዜ ፡ አስ ቀድመህ ፡ ልመናህን ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ታቀርብ ፡ ዘንድ ፡ እኔ ፡ እለምንሃለሁ ። በትዕግ ሥት ፡ በጸጥታ ፡ በአርምሞ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በመፍራት ፡ በንጽሕና ፡ ሁነው ፡ ይኖሩ ፡ ዘንድ። እነዚህ ፡ ሥራዎች ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ይድኑ ፡ ዘንድ፡ እውነትንም ፡ ወደማወቅ ፡ ይደርሱ ፡ ዘንድ ፡ ወደሚወድ ፡ ወደ ፡ ሕያው ፡ እግዚአብሔር ፡ ያደርሳሉና ።

፻፲፬ ፭ ። (፩ ፡ ጢሞ ፡ ፬ ፡ ፲፩ - ፲፮) ። ለምእመናን ፡ በአነጋገር ፡ በተጋድሎ ፡ በፍቅር ፡ በሃይማኖት ፡ በንጽሕና ፡ አንተ ፡ አብነት ፡ ሁናቸው ። እስከ መጣ ፡ ድረስ ፡ መጽሐፍን ፡ በመመልከት ፡ በማ ስተማር ፡ በምክር ፡ ተጠብቀህ ፡ ኑር ። ትንቢ ትን ፡ ከመናገር ፡ ጳጳሳትን ፡ በአንብሮተ ፡ እድ ፡ ከመሾም ፡ ጋራ ፡ የሰጠህን ፡ ጸጋ ፡ አታቃል ። በእነርሱ ፡ ጸንተህ ፡ እንድትኖር ፡ እወቅ ። አንተ ይህንን ፡ ብትሠራ ፡ ራስህንና ፡ የሚሰሙህን ፡ ታድናለህ ። ሽማግሎችን ፡ አታሳዝን ። እንደ ፡ አባት ፡ ጸልይላቸው ፡ አረጋጋቸው ፡ አስደስታ ቸውም ፡ እንጂ ። ለጕበዛዝትም ፡ እንደ ፡ ወንድሞ ችህ ፡ ለባልቴቶችም ፡ እንደ ፡ እናቶችህ ፡ ለቈን ጆጆችም ፡ እንደ ፡ እኅቶችህ ፡ በማናቸውም ፡ ንጽሕናና ፡ ክብር ፡ ሁነህ ፡ ጸልይላቸው ። እናት፡ አባት ፡ ለሌላቸውና ፡ ባሎቻቸው ፡ ለሞቱባ ቸው ፡ በእውነት ፡ ሥራ ። በቄስ ፡ ላይ ፡ ነገር ፡ ሥራን ፡ አትስማ ። ሁለት ፡ ወይም ፡ ሦስት ፡ ሰዎች ፡ ካልመሰከሩበት ፡ በተር ፡ ነገረ ፡ ሠሪን

ልም ፡ ገጽ ፡ ወኢ.ታፍጥን ፡ እንብርር ፡ እደ.ከ ፡ ላዕለ ፡ ፩ዱ.ሂ ። ወኢ.ትሳተፍ ፡ በኃጢአተ ፡ ነኪ.አት ፡ ካልእከ ።

፻፲፩ ዘኒት ፡ ወእለሂ ፡ አማስኑ ፡ ነፍሳቲሆሙ ፡ ወስሕቱ ፡ እምፍኖተ ፡ ርትዕ ፡ ወይመስሉሙ ፡ ከመ ፡ ፍርሃተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተማይጦ ፡ ወረባኅ ፡ ይእቲ ፡ ረኀቅ ፡ እምኔሆሙ ። ወለነሰ ፡ ረባኅቲነ ፡ ዐባይ ፡ ወይእቲ ፡ ፍርሃተ ፡ እግዚአብሔር ፡ በአእከሎ ፡ ሲሳይ ። እስመ ፡ አልቦ ፡ ዘአምጻእነ ፡ ውስተ ፡ ዓለም ፡ ምንተኒ ። ወናሁ ፡ ነአምር ፡ ንሕነ ፡ ከመ ፡ አልቦ ፡ ዘንነሥእ ፡ እምኔሁ ፡ ካዕበ ፡ ምንተኒ ፡ ወበእንተ ፡ ዝንቱ ፡ ይደሉ ፡ ዘየአክለነ ፡ እምኔሁ ፡ ንንሣእ ፡ ሲሳየ ፡ ወልብሰ ። እለሰ ፡ ያፈቅሩ ፡ ንዋየ ፡ ወይፈቅዱ ፡ ከመ ፡ ይብዐሉ ፡ ይወድቁ ፡ ውስተ ፡ መንሱት ፡ ወመሥገርት ፡ ወፍትወት ፡ ብዙኅት ፡ ዘታስሕት ፡ ወታስጥም ፡ ሰብአ ፡ ውስተ ፡ ሙስና ፡ ወሐጕል ። እስመ ፡ ሥርወ ፡ ለኵሉ ፡ እከይ ፡ አፍቅሮ ፡ ንዋይ ። ወናሁ ፡ ጽሕቁ ፡ ዘንተ ፡ ብዙኃን ፡ ሰብእ ፡ ወስሕቱ ፡ እምሃይማኖት ፡ ወአብኡ ፡ ነፍሳቲሆሙ ፡ ውስተ ፡ ምንዳቤ ፡ ብዙኅ ። ወአንተሰ ፡ አ ፡ ብእሴ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጐየይ ፡ እምዝንቱ ፡ ግብር ፡ ወዴግን ፡ ኀበ ፡ ኀሢሠ ፡ ጽድቅ ፡ ወርትዕ ፡ ወውስተ ፡ አሠረ ፡ ሃይማኖት ፡ ወተፋቅሮ ፡ ወውስተ ፡ አሠረ ፡ ትዕግሥት ፡ ወትሕትና ። ወተጋደል ፡ በእንተ ፡ ሃይማኖት ፡ ርትዕት ፡ ወሠናይት ፡ ወትረክብ ፡ ሕይወተ ፡ ዘለዓለም ፡ እንተ ፡ ላቲ ፡ ተጸዋዕከ ። ወአዝዞሙ ፡ ለአብዕልተ ፡ ዝንቱ ፡ ዓለም ፡ ከመ ፡ ኢይትዐበዩ ፡ በአልባቢሆሙ ፡ ወኢይትወከሉ ፡ በብዕሎሙ ፡ ዘአልቦ ፡ ተወክሎ ፡ በላዕሌሁ ። አላ ፡ ይትአመኑ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ሕያው ፡ ዘወሀበነ ፡ ኵሎ ፡ በብዙኅ ፡ ብዕሉ ፡ ለዕረፍተ ፡ ዚአነ ። ወከመ ፡ ይብዐሉ ፡ በምግባረ ፡ ሠናይ ፡ ወያፍጥኑ ፡ ለውሂብ ፡ በአዕርዮ ፡ ወያንብሩ ፡ ለነፍሶሙ ፡ መሠረተ ፡ ሠናየ ፡ ለግብር ፡ ዘይመጽእ ፡ ከመ ፡ ይርከቡ ፡ ሕይወተ ፡ ዘበአማን ። አ ፡ ጢሞቴዎስ ፡ ተዓቀብ ፡ ዘአማኀፀንኩከ ፡ ወጐየይ ፡ እምስሚዐ ፡ ከንቱ ወአመንኑድ ምተ ፡ ዓለም ፡ ሐሳዊ ። እስመ ፡ እለ ፡ የኀሥሡ ፡



አትስማ ። የበደሉትን ፡ በሊቃውንት ፡ ፊት ፡ ገሥጻቸው ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ይፈሩ ፡ ዘንድ ። ፊትን ፡ አይቶ ፡ በማድላት ፡ ምንም ፡ ምን ፡ አትሥራ ። ማንንም ፡ ፈጥነህ ፡ በእንብርክተ ፡ እድ ፡ አትሾም ። በዚህ ፡ የሌላውን ፡ ሰው ፡ ኃጢአት ፡ አትካፈል ።

፻፲፩ በ፯ኛውም ፡ ክፍል ፡ እንዲህ ፡ አለ ። (፩ጢሞ ፡ ፮ ፡ ፳-፳፩) ። ሰውነታቸውን ፡ በኃጢአት ፡ ያጠፉትንና ፡ ከቀናው ፡ መንገድ ፡ የራቁትን ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ ንግድና ፡ ጥቅም ፡ የሚመስላቸውን ፡ ሰዎች ፡ ተለያቸው ። እኛስ ፡ ታላቁ ፡ ጥቅማችን ፡ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ ነው ። የዕለት ፡ ምግባችንን ፡ ማግኘታችን ፡ ይበቃናል ። ወደዚህ ፡ ዓለም ፡ ያመጣነው ፡ ነገር ፡ ምንም ፡ የለምና ። እነሆ ፡ እኛ ፡ ሁለተኛ ከርሷ ፡ የምንወስደው ፡ እንደሌለን ፡ እናውቃለን ። ስለዚህ ፡ ከእርሷ ፡ ምግብና ፡ ልብስ ፡ እንወስድ ፡ ዘንድ ፡ ይበቃናል ። ገንዘብን ፡ የሚወዱ ፡ ለመበልጠግም ፡ የሚሹ ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ፈተና ፡ ወደ ፡ ወጥመድ ፡ ሰውን ፡ በፍጹም ፡ ጥፋት ፡ በምታስጥምና ፡ በምታስት ፡ ብዙ ፡ በሆነች ፡ ምኞት ፡ ይወድቃሉ ። የክፉ ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ምንጩ ፡ ገንዘብን ፡ መውደድ ፡ ነውና ። እነሆ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ይህንን ፡ ተመኝተው ፡ ከሃይማኖታቸው ፡ ወጡ ። ሰውነታቸውንም ፡ በብዙ ፡ ችግር ፡ ውስጥ ፡ ጣሉ ። አንተ ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ሆይ ፡ ከዚህ ፡ ሥራ ፡ ራቅ ። እውነትን ፡ መፈለግን ፡ ተከተል ፡ የትዕግሥትንና ፡ የትህትናን ፡ ፈለግ ፡ ተከተል ። ስለ፡ ቀናች ፡ ሃይማኖት ፡ ተጋደል ። የተጠራኸባትን ፡ የዘላለም ፡ ሕይወት ፡ ታገኛለህ ። ለእኛ ፡ ዕረፍት ፡ በብዙ ፡ ስጦታው ፡ ሁሉን ፡ በሰጠን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ይታመኑ ፡ እንጂ ፡ ሊታመኑበት ፡ በማይገባ ፡ ሀብታቸው ፡ እንዳይታመኑ ፡ በልባቸው ፡ እንዳይታበዩ ፡ የዚህን ፡ ዓለም ፡ ባለጠጎች ፡ እዘዛቸው ። በበጎ ፡ ምግባር ፡ ይበለጽጉ ፡ ዘንድ ፡ እውነተኛውንም ፡ ሕይወት ፡ ያገኙ ፡ ዘንድ ፡ ለሚመጣው ፡ ሥራ ፡ መልካም ፡ መሠረት ፡ ለነፍሳቸው ፡ ያኖሩ ፡ ዘንድ ፡ እዘዛቸው ። ጢሞቴዎስ ፡ ሆይ ፡ አደራ ፡ ያልኩህን ፡ ጠብቅ። ከንቱን ፡ ነገር ፡ ከመስማት ፡ ሐሰተኛ ፡ ከሆነው ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ተረት ፡ ራቅ ። ይህን ፡ የሚፈልጉ ፡ ሁሉ ፡ ከሃይማኖት ፡ እነሆ ፡ ወጥተ

ዘንተ ፡ ናሁ ፡ ስሕተ ፡ እምሃይማኖት ፡ ወጺጋ ፡ ምስሌከ ፡ አሜን ።

፻፲፫ ድስቅ ፡ ፬ቱ ፡ ጸሐቅ ፡ ሊቃለ ፡ ትምህርት ፡ አ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ወለእመ ፡ ኮንከ ፡ ትክል ፡ ተርጕሞ ፡ እምነ ፡ ኵሉ ፡ መጻሕፍት ፡ ቃላተ ፡ አጽግቦሙ ፡ ለሕዝብከ ፡ ወአብርህ ፡ ሎሙ ፡ እምነ ፡ ብርሃን ፡ ሕጊጋቲከ ፡ ከመ ፡ ይኩኑ ፡ በዝንቱ ፡ እብዕልተ ፡ በብዝኀ ፡ ትምህርትከ ።

፻፲፬ ወይደሉ ፡ ለከሙ ፡ አ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ከመ ፡ ትኩኑ ፡ ሰብአ ፡ ዓይን ፡ ለሕዝብ ። እስመ ፡ እስ ያንቲሁ ፡ እንትሙ ፡ ለክርስቶስ ። ወእግዚአብሔር ፡ ይቤ ፡ በአፈ ፡ ሕዝቅኤል ፡ ነቢይ ፡ በእንቲአከሙ ፡ አ ፡ ወልድ ፡ እጓለ ፡ እመሕያው ፡ ረሰይኩከ ፡ ሰብአ ፡ ዓይን ፡ ለዝንቱ ፡ ሕዝብ ፡ ትስማዕ ፡ እምአፉየ ፡ ነገረ ፡ ወትሰብኮ ፡ ወትስቀቦሙ ፡ ቦቱ ፡ እመንገለ ፡ ገጽየ ፡ እምኅቤየ ። እስመ ፡ ለእመ ፡ ኢነገርኮ ፡ ለኃጥእ ፡ ከመ ፡ ይትዐቀብ ፡ እምነ ፡ ኃጢአቱ ። ወውእቱ ፡ ኃጥእ ሰበ ፡ ሞተ ፡ በኃጢአቱ ፡ ወደሞ ፡ እትኀሠሥ ፡ እምእዴከ ። ወለእመሰ ፡ አቅደምከ ፡ ወአመርኮ ፡ ለኃጥእ ፡ ወነገርኮ ፡ ከመ ፡ ይትኀሠሥ ፡ እምእከዩ ፡ ወኢተማኅፀ ፡ እምኔሁ ፡ ውእቱ ፡ ኃጥእ ፡ ወሞተ በኃጢአቱ ፡ ወአንተ ፡ አድኀንከ ፡ ነፍሰከ ። ወበእንተ ፡ ዝንቱ ፡ መሀርዎሙ ፡ ለእለ ፡ የሐውሩ ፡ ዘእንበለ ፡ እእምሮ ፡ ወለእለ ፡ ተምህሩ ፡ አጽንዕዎሙ ፡ ወሚጥዎሙ ፡ ለስሑታን ፡ ወንግርዎሙ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ፡ በእንተ ፡ ስሕተቶሙ ።

፻፲፭ አቅም ፡ ነፍሰከ ፡ በንጽሕ ፡ ኦ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ በኵሉ ፡ ምግባርከ ። ወእእምር ፡ መንበረ ፡ ሢመትከ ፡ እስመ ፡ አንተ ፡ እምሳለ ፡ እግዚአብሔር ፡ በኀበ ፡ ሕዝብ ፡ በሢመትከ ፡ ወኮንከ ፡ ርእሰ ፡ ለሰብእ ፡ ወለኵሎሙ ፡ ካህናት ፡ ወመኳንንት ፡ ወካህናት ፡ ወለአበው ፡ ወለውሉዶሙ ፡ እለ ፡ ተምህሩ ። ወለኵሎሙ ፡ እለ ፡ ሀለዉ ፡ ታሕተ ፡ ትእዛዝከ ። ንበር ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንከ፡ ወሰብኮ ፡ በቃል ፡ እስመ ፡ ለከ ፡ ሥልጣን ፡ ከመ ፡ ትኰንን ፡ ኃጥአነ ። እስመ ፡ ለከሙ ፡ ይቤ ፡ እለ ፡ ተአስርዎሙ ፡ በምድር ፡ ይኩኑ ፡ እሱራነ ፡ በሰማያት ፡ ወእለሂ ፡ ትፈትሕዎሙ ፡ በምድር ፡ ይኩኑ ፡ ፍቱሓነ ፡ በሰማያት ። ኰንን፡ በሥልጣን በእምሳለ ፡ እግዚአብሔር ። ወለ ዘነስሐ ፡ ተወከፎ ፡ ኀቤከ ፡ እስመ ፡ እግዚአብ

ዋልና። ጸጋ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ ትሁን ፡ አሜን ።

፻፲፫ ድስቅ ፡ ፬ ። ኤጲስ ፡ ቆጶስ ፡ ሆይ ፡ ለማስተማር ፡ ትጋ ። መጻሕፍትን ፡ ሁሉ ፡ ለመተርጐም ፡ ብትችል ፡ ሕዝብህን ፡ ትምህርት ፡ አጥግባቸው ። በብዙ ፡ ትምህርተ ፡ ባለጠጎች ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ። ከሕጎችህ ፡ ብርሃን ፡ አብራላቸው ።

፻፲፬ ኤጲስቆጶሳት ፡ ሆይ ፡ ለሕዝቡ ፡ ጉበኞች ፡ ትሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ይገባችኋል ። የክርስቶስ ፡ ዓይኖቹ፡ እናንተ ፡ ናችሁና ። እግዚአብሔርም ፡ ስለእናንተ ፡ በነቢዩ ፡ በሕዝቅኤል ፡ አፍ ፡ እንዲህ ፡ አለ ። (ሕዝ ፡ ፫ ፡ ፲፯ - ፳፩) ። "የሰው ፡ ልጅ ፡ ሆይ ፡ ለዚህ ፡ ሕዝብ ፡ ጉበኛ ፡ አደረግሁህ ። ከእኔ ፡ ነገር ፡ ሰምተህ ፡ እንድታስተምር ፡ እንደኔ ፡ እንደራሴ ፡ ሆነህ ፡ ትጠብቃቸው ፡ ዘንድ ፡ ኃጥእ ፡ ከኃጢአቱ ፡ ይጠበቅ ፡ ዘንድ ፡ ባትነግረው ፡ ያህም ፡ በኃጢአቱ ፡ ሳለ ፡ ቢሞት ፡ ደሙን ፡ ከአንተ ፡ እፈልጋለሁ ። አስቀድመህ ፡ ግን ፡ ከኃጢአቱ ፡ እንዲመለስ ፡ ብትነግረው ፡ ያህ ፡ ከኃጢአቱ ፡ ባይመለስ ፡ በኃጢአቱም ፡ ቢሞት ፡ አንተ ፡ ራስህን ፡ አዳንህ" ። ስለዚህም ፡ ያለ ፡ እውቀት ፡ የሚኖሩትን ፡ አስተምሯቸው ። የተማሩትን ፡ አጽኗቸው ። የተሳሳቱትንም ፡ መልሷቸው ። በየጊዜውም ፡ ስለ ፡ ስሕተታቸው ፡ ንገሯቸው ።

፻፲፭ ኤጲስቆጶስ ፡ ሆይ ፡ በሥራው ፡ ሁሉ ፡ ራስህን ፡ በንጽሕና ፡ አጽና ። የሹመትህንም ፡ መንበሩ ፡ እወቅ ። በሕዝቡ ፡ ዘንድ ፡ በሹመትህ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነህና ። ለሕዝቡ ፡ ለንጉሥታቱ ፡ ሁሉ ፡ ለመኳንንቱ ፡ ለካህናቱ ፡ ለአባቶችና ፡ ላተማሩት ፡ ልጆቻቸው ፡ ከትእዛዝህ ፡ በታች ፡ ላሉት ፡ ሁሉ ፡ አለቃ ፡ ሁነሃልና ። በቤተ ፡ ክርስቲያንህ ፡ ተቀመጥ ። በቃልህም ፡ አስተምር ። በኃጥአን ፡ ትፈርድ ፡ ዘንድ ፡ ሥልጣን ፡ አለህና ። በምድር ፡ ያሰራችኋቸው ፡ በሰማይ ፡ የታሰሩ ፡ ይሆናሉ ፡ በምድርም ፡ የፈታችኋቸው ፡ በሰማይ ፡ የተፈቱ ፡ ይሆናሉ ፡ (ዮሐ ፡ ፳ ፳፫) ። ብሎ ፡ ለናንተ ፡ ተናግሯልና ። በእግዚአብሔር አምሳል ፡ በሥልጣንህ ፡ ፍረድ ። ንስሐ ፡ የገባውን ፡ ሰው ፡ ወደአንተ ፡ ተቀበለው ። እግዚአ

ሔር ፡ አምላከ ፡ ምሕረት ፡ ውእቱ ።

፪፲፱ ኀሥሥ ፡ ለዘይኤብስ ፡ ወኢትስድዶ ፡ ለዘይኔስሕ ። እስተሐምም ፡ አ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ለመድኀኒተ ፡ ኵሉ ፡ ሰብእ ፡ ለለ፩ ፡ እስመ ፡ ለእሙ ፡ ይብል ፡ እግዚእን ፡ ውቱ ፡ ኢታስተሐቅርዎ ፡ ለ፩ ፡ እምእሉ ፡ ንኡሳን ወአእምር ፡ በዝንቱ ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡ ይእዜ ፡ ይትኀሠሥ ፡ እምኔከ ፡ ዘብዙኅ ፡ እሙንቱ ፡ ሬድፋይስ ፡ ለዘአማኅፀንዎ ፡ ብዙኀ ፡ ይትኀሠሥዎ ፡ ብዙኀ ።

፪፳ ሀሉ ፡ አንተ ፡ እንበለ ፡ ሐሜት ፡ ከመ ፡ ኢይትሀቀፍ ፡ በእንቲአከ ፡ ፩ዱሂ ፡ ወሕዝባዊ ፡ ያስተሐምም ፡ በነፍሱ ፡ እንተሰ ፡ ያርኅ ፡ ያረ ፡ ከቡድ ። ጽሑፍ ፡ ከመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይቤሎ ፡ ለሙሴ አንተ ፡ ወአሮን ፡ ትፀውሩ ፡ አበሳሆሙ ፡ ለሕዝብ ፡ ተዓዋርያን ። መሀሮሙ ፡ ለእለ ፡ ይትሄየዩ ፡ ወአእምር ፡ ከመ ፡ ለከ ፡ ዕሤት ፡ ዐቢይ ፡ ለእመ ፡ ገበርከ ፡ ዘንተ ፡ በከመ ፡ ብከ ፡ ኵነኔ ፡ ዐቢይ ፡ ለእመ ፡ ተሀከይከ ፡ በእንቲአሁ ።

፪፳፩ ወሶበ ፡ መጽአ ፡ ኀቤከ ፡ ዘሀለወ ፡ ቦቱ ፡ ዐቢይ ፡ አበሳ ፡ ኢትትኈየይ ፡ ኪያሁ ። ይቤ ፡ ሕዝቅኤል ፡ ነቢይ ፡ በእንተ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ዘይትሄየይ ፡ እንበይነ ፡ ሕዝቡ ፡ እሌ ፡ ሎሙ ፡ ለኖሎተ ፡ እስራኤል ፡ እለ ፡ ኀደጉ ፡ አባግዒሆሙ ፡ ዘይረዐዩ ፡ ለለ፩ ፡ እኩኑ ፡ አንትሙ ፡ ኖሎት ፡ ዘትርዕዩ ፡ አባግዐ ። ወአንትሙ ፡ ለሐሊብ ፡ ትሰትዩ ፡ ወለፀምር ፡ ዘትለብስዎ ፡ ወለመግዝእኒ ፡ ሰቡሕ ፡ ዘትጠብሕዎ ፡ ወአባግዐየሰ ፡ ኢትርዕዩ ፡ ወለዘደክመ ፡ ኢታጽንዕዎ ፡ ወለዘተሰብረ ፡ ኢትፌውስዎ ፡ ወለዘተገድፈ ፡ ኢተኀሥሥዎ ፡ ወለዘተሐጕለ ፡ ኢትረክብዎ ፡ ወኢትሜህርዎሙ ፡ ትምህርተ ፡ በውዕየተ ፡ ልብ ፡ ዳዕሙ ፡ በስላቅ ። ወተዘርወ ፡ አባግዕየ ፡ በእንተ ፡ ዘአልቦሙ ፡ ኖላዊ ፡ ወኮኑ ፡ መብልዐ ፡ ለአናብስተ ፡ ገዳም ። ወይቤ ፡ ካዕበ ፡ አንስ ፡ አፈትሕ ፡ማእከለ ፡ አባግዕ ፡ ወኖሎት ፡ ወማእከለ ፡ በግዕ ፡ ወበሐዝ ፡

፪፳፪ ለዘኒ ፡ አበሰ ፡ አ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ወአውፃእኮ ፡ በግዘት ፡ ኢትኅድጎ ፡ አፍኣ ፡ እላ ፡ ሚጦ ፡ ኀበ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ። ወለዘተገድፈ ፡ ኅሥሥ ፡ ወለዘኢይሴፎ ፡ መድኀኒተ ፡ በእንተ ፡ ብዝኀ ፡ ኃጣውኢሁ ፡ ኢትኅድጎ ፡ ይትሐጐል ፡ በኵሉ ።

ብሔር ፡ የምሕረት ፡ አምላክ ፡ ነውና ።

፪፲፱ የበደለውን ፡ ምከረው ፡ ንስሐ ፡ የገባውንም ፡ አታባረው ። ኤጲስቆጶስ ፡ ሆይ ፡ እየንዳንዱ ፡ ሰውን ፡ ሁሉ ፡ ለማዳን ፡ ትጋ ። ጌታችን ፡ ለና ንተ ፡ ከታናናሾቹ ፡ አንዱን ፡ አታቃሉ ፡ ብሏ ልና ፡ (ማቴ ፡ ፲፰ ፡ ፲) ። በዚህ ፡ ካንተ ፡ ብዙ ፡ እንደሚፈለግብህ ፡ እወቅ ። ብዙ ፡ አደራ ፡ ያሉ ትን ፡ ብዙ ፡ ይፈልጉበታልና ። (ሉቃ ፡ ፲፪ ፡ ፵፰) ።

፪፳ አንዱ ፡ ሰንኳ ፡ በአንተ ፡ እንዳይሰናከል ፡ ያለ ሐሜት ፡ ኑር ። ሕዝባዊ ፡ ለራሱ ፡ ያስባል ፡ አንተ ፡ ግን ፡ ከባድ ፡ ሸክም ፡ ተሸክመሃል ። እግዚአብሔር ፡ ለሙሴ ፡ "አንተና ፡ አሮን ፡ የሕግ ፡ አፍራሾች ፡ የሕዝቡን ፡ በደል ፡ ትሸ ክማላችሁ ፡ አለው ። (ዘኍ ፡ ፲፰ ፡ ፩-፪) ። የሚል ፡ ጽሑፍ ፡ አለ ። ቸልተኞችን ፡ አስተም ራቸው ። ቸል ፡ ብትል ፡ ስለነሱ ፡ ትልቅ ፡ ቅጣት ፡ እንዳለብህ ፡ ይህንን ፡ ብታደርግ ፡ ታላቅ ፡ ዋጋ ፡ እንዳለብህ ፡ እወቅ ።

፪፳፩ ትልቅ ፡ በደል ፡ ያለበት ፡ ሰው ፡ ወዳንተ ፡ በመ ጣ ፡ ጊዜ ፡ ቸል ፡ አትበለው ። ነቢዩ ፡ ሕዝቅ ኤል ፡ ሕዝቡን ፡ ቸል ፡ ስለሚል ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ እን ዲህ ፡ አለ ። (ሕዝ ፡ ፴፬ ፡ ፪ - ፳) ። እየንዳንዱ ፡ የሚጠብቋቸውን ፡ በጎች ፡ ለተወ ፡ ለእስራ ኤል ፡ ጠባቂዎች ፡ ወዮላቸው ። በጎችን ፡ የም ትጠብቁ ፡ እረኞች ፡ እናንተ ፡ አይደላችሁምን ፡ ወተቱን ፡ የምትጠጡት ፡ ጠጕሩን ፡ የምትለብ ሱት ፡ የሰባውን ፡ ፍሪዳ ፡ የምታርዱት ፡ እና ንተ ፡ አይደላችሁምን ። በጎችን ፡ አትጠብ ቁም ፡ የደከመውን ፡ አታጸኑትም ፡ የተሰበረ ውን ፡ አትጠግኑትም ፡ የጠፋውን ፡ አታገኙ ትም ። በጎስ ፡ መንፈስ ፡ አታስተምሩዋቸ ውም ፡ በፌዝ ፡ ነው ፡ እንጂ ። በጎቼ ፡ ጠባቂ ፡ ስለሌላቸው ፡ ተበተኑ ፡ ለዱር ፡ አንበሶችም ፡ ምግብ ፡ ሆኑ" ፡ አለ ። ዳግመኛም ፡ በበጎችና ፡ በእረኞች ፡ መካከል ፡ በአውራውና ፡ በመንጋ ውም ፡ መካከል ፡ እፈርዳለሁ ፡ አለ ። (ሕዝ ፡ ፴፬ ፡ ፲፯) ።

፪፳፪ ኤጲስቆጶስ ፡ ሆይ ፡ የበደለውን ፡ አውግዘህ ፡ ብትለየው ፡ በውጭ ፡ አትተወው ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ መልሰው ፡ እንጂ ። የጠፋውንም ፡ ፈልግ ። ስለ ፡ ኃጢአቱ ፡ ብዛት ፡ እድናለሁ ፡ ብሎ ፡ ተስፋ ፡ የማያደርገውን ፡ በሁሉ ፡ ጠፍቶ ፡

ወከመዝ ፡ ይደልዎ ፡ ለኤጲስቆጶስ ፡ ይፁር ፡ ኃጢአተ ፡ ሕዝብ ፡ ሳለለ ፡ ነፍሱ ፡ ወይረሲ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ዘአበሰ ፡ ውእቱ ፡ ፈድፋደ ፡ ወይበሎ ፡ ለዘአበሰ ፡ ተመየጥ ፡ አንተ ፡ ወአነ ፡ እትዌከፍ ፡ ሞተ ፡ በየንቲከ ፡ እምሳለ ፡ እግዚእነ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ዘሞተ ፡ በእንቲአየ ፡ ወበእንተ ፡ ኵሉሙ ። ወይቤ ፡" አነ ፡ ኖላዊ ፡ ኄር ፡ ኖላዊሰ ፡ ኄር ፡ ይሜጡ ፡ ነፍሶ ፡ ህየንተ ፡ አባግዒሁ ፡ ወንዳብስ ፡ ዘኢኮነ ፡ ኖላዊ ወኢኮኑ ፡ አባግዕ ፡ ዚአሁ ፡ ሶበ ፡ ርእየ ፡ እንዘ ፡ ይመጽእ ፡ ተኩላ ፡ ዘውእቱ ፡ ዲያብሎስ ፡ የኀድጎን ፡ ለአባግዕ ፡ ወይጐይይ ፡ ወይመሥጦን ፡ ተኩላ ፡ ለእላ ፡ አባግዕ ።

ይቀር ፡ በንደ ፡ አትተወው ። እንዲሁም ፡ ኤጲስ ቆጶስ ፡ የኅጥኡን ፡ ኃጢአት ፡ ሊሸከም ፡ ይገባ ዋል ። እርሱም ፡ ፈጽሞ ፡ እንደበደለ ፡ ያድርግ ለት ። የበደለውንም ፡ "አንተ ፡ ተመለስ ፡ እኔ ም ፡ ስለእኔና ፡ ስለ ፡ ሁሉ ፡ በሞተው ፡ በጌታ ችን ፡ በኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ አምሳል ፡ ስለአ ንተ ፡ ሞትን ፡ እቀበላለሁ" ይበለው ። "እኔ ፡ ቸር ፡ ጠባቂ ፡ ነኝ ፡ ቸር ፡ ጠባቂ ፡ ስለ ፡ በጎቹ ፡ ሰውነቱን ፡ አሳልፎ ፡ ይሰጣል ፡ ጠባቂ ፡ ያል ሆነ ፡ በጎቹም ፡ የእርሱ ፡ ያይደሉ ፡ ደመወዝ ተኛ ፡ ግን ፡ ይኸውም ፡ ዲያብሎስ ፡ ነው ፡ ተኩ ላ ፡ ሲመጣ ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ በጎቹን ፡ ትቶ ፡ ይሸ ሻል ፡ በጎቹን ፡ ተኩላ ፡ ይነጥቃቸዋል ።" ይላል (ዮሐ ፡ ፲ ፡ ፲፩ - ፲፪) ።

፻፳፫ ዐቃቤ ፡ አባግዕ ፡ ኅሥሥ ፡ በግዐ ፡ ዘተግድፈ ፡ ከመ ፡ እግዚእነ ፡ ይቤ ፡ ውእቱ ፡ የኀድግ ፡ ፺ ወ፱ተ ፡ ውስተ ፡ ደብር ፡ ወየሐውር ፡ ይኅሥሥ ፡ ዘተግድፈ ፡ ወሶበ ፡ ረከቦ ፡ ይፀውሮ ፡ ዲበ ፡ መትከፍቱ ፡ ወያበውኦ ፡ ኀበ ፡ መርዔት ፡ እንዘ ፡ ይትፌሣሕ ፡ ውእቱ ፡ በእንቲአሁ ።

፻፳፫ የበጎች ፡ ጠባቂ ፡ ሆይ ፡ የጠፋውን ፡ በግ ፡ ፈልግ ፡ ዘጠና ፡ ዘጠኙን ፡ በተራራ ፡ ላይ ፡ ትቶ ፡ የጠ ፋውን ፡ ሊፈልግ ፡ ይሄዳል ፡ ባገኘውም ፡ ጊዜ ፡ በትከሻው ፡ ተሸክሞ ፡ እርሱ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ ደስ ፡ እያለው ፡ ወደ ፡ መንጋው ፡ ያገባዋል ፡ ብሎ ፡ ጌታችን ፡ እንደ ፡ ተናገረ ፡ (ሉቃ ፡ ፲፭ ፡ ፬ - ፯) ።

፻፳፬ ወለእመ ፡ ከነ ፡ ድውየ ፡ በኃጢአት ፡ የኀሥሥ ፡ ዐቃቤ ፡ ሥራይ ፡ ልብወ ፡ ዘይትረዳእ ፡ በእንተ ፡ ሕማሙ ፡ ወነዋ ፡ ይቤ ፡ እግዚእነ" ፡ እኮ ፡ ጥዑያን ፡ ዘየኀሥሥዎ ፡ ለዐቃቤ ፡ ሥራይ ፡ ዳእሙ ፡ ድውያን ፡ ወወልድ ፡ እጓለ ፡ እመሕያው ፡ ሶበ ፡ መጽአ ፡ እንዘ ፡ ውእቱ ፡ ዐቃቤ ፡ ሥራይ ፡ አድኅኖ ፡ ወፈውሶ ፡ ድውያን" ።

፻፳፬ በኃጢአት ፡ የታመመ ፡ ቢሆን ፡ ስለ ፡ ሕማሙ ፡ የሚረዳው ፡ አዋቂ ፡ ሐኪም ፡ ይፈልጋል ። እነሆ ፡ ጌታችን ፡ ሐኪምን ፡ የሚፈልጉት ፡ ጤነ ኞች ፡ አይደሉም ። በሽተኞች ፡ ናቸው ፡ እንጂ ፡ (ማቴ ፡ ፱ ፡ ፲፪ - ፲፫) ። አለ ። የሰው ፡ ልጅ ፡ ሐኪም ፡ ሆኖ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ ድውዮችን ፡ ፈጽሞ ፡ አዳነ ።

፻፳፭ ወኢታፍቅር ፡ መስተዋድያን ፡ ወኢሰሱዓን ። ወለእመ ፡ ርኢከ ፡ ለሕዝብ ፡ ገሥሥ ፡ በበንስቲት ፡ ወኢታፍቅሮን ፡ ስዲዮቶ ፡ ወአገሥሦሙ ፡ ለዲያቆናት ፡ ይርከብዎ ፡ አፍአ ፡ ወይኅትዎ ፡ ወያማብእዎ ፡ ወይጸልዩ ፡ በእንቲአሁ ፡ እሜሃ ፡ ሥረዮ ፡ ሎቱ ፡ ጾመ ፡ በእንተ ፡ ኃጢአቱ ፡ በአምጣነ ፡ ክሂሎቱ ፡ እሐደ ፡ ወ፪ተ ፡ ሰባዕያተ ፡ አው ፡ ሠለስተ ፡ አው ፡ አርባዕተ ፡ አው ፡ ሐምስተ ፡ አው ፡ ስድስተ ። ወመሀሮ ፡ ከመ ፡ ይትገሠጽ ፡ በከመ ፡ ይደሉ ፡ ለሥርየተ ፡ ኃጢአቱ ፡ ወአክብሮ ፡ ወመሀሮ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ትሑተ ፡ ወየዋሀ ፡ በርእሱ ።

፻፳፭ ነገረ ፡ ሠሪዎችንና ፡ ስስታሞችን ፡ አትውደድ ። ኃጢአተኛውን ፡ ብታገኘው ፡ ጥቂት ፡ በጥ ቂት ፡ ምከረው ። ፈጥነህ ፡ አትለየው ። ዲያቆ ናትም ፡ በውጭ ፡ አግኝተው ፡ አባብለው ፡ እንዲመልሱት ፡ ስለርሱም ፡ እንዲጸልዩ ፡ አዘ ዛቸው ። ያንጊዜ ፡ በችሎታው ፡ መጠን ፡ ጾም ፡ ሥራለት ። አንድና ፡ ሁለት ፡ ሱባዔ ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ ሦስት ፡ ወይም ፡ ፬ ፡ ወይም ፡ ፭ ፡ ወይ ም ፡ ፮ ፡ ሱባዔ ፡ ሥራለት ። ኃጢአቱን ፡ ለማስ ተሥረይ ፡ በሚገባ ፡ እንዲገሠጽ ፡ አስተምረው አክብረው ። በራሱ ፡ ትሑት ፡ የዋህ ፡ እንዲሆን አስተምረው ።

፻፳፮ ዘንቱ ፡ ወይደሉ ፡ ለክሙ ፡ ኦ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ከመ ፡ ትረስይዎ ፡ ለክሙ ፡ እርአየ ፡ ለመድኅኒነ ፡ ወንጉሥነ ፡ ወአምላክነ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስ

፻፳፮ ድስቅ ፡ ፭ ። ኤጲስቆጶሳት ፡ ሆይ ፡ መድኃኒታ ችንን ፡ ንጉሣችንን ፡ አምላካችንን ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስን ፡ አብነት ፡ ልታደርጉት ፡ ይገባች

እላ ፡ ለሊሁ ፡ በንፍሱ ፡ በዘይደሉ ፡ ወኢይእመን ዡሉ ፡ ስምዐ ፡ ሐሰት ፡ በላዕሌሆሙ ።

፻፵ ወኩን ፡ ከመ ፡ ብእሲ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእ ንጥ ፡ መንፈስከ ፡ ወኢታፅምዕ ፡ ከመ ፡ ትትወ ከፍ ፡ ቃሎ ፡ ለመስተዋድዮ፡ አኀዊሁ ፡ በሐ ሰት ፡ በእንተ ፡ ቅንእቱ ፡ ወእከዩ ። እስመ ፡ ዘከመ ፡ እሉ ፡ ኢየኀድጉ ፡ ከመ ፡ ትኩን ፡ ሰላም፡ ዘልፈ ፡ አበተሐይጾሙ ፡ ወተዐቀብ ፡ እምኔሆሙ ከመ ፡ ኢታሕጕል ፡ ዘኢኮኑ ፡ ኃጥእነ ። ወለእመ ረከብከ ፡ ጥዩቀ ፡ በከመ ፡ ውዱቶሙ ፡ ለእሉ ፡ ግብር ፡ ውስቴቱ ፡ በከመ ፡ ትምህርቱ ፡ ለእግዚ አብሔር ፡ ንሥእ ፡ ለዘአበተዋደይዎ ፡ ባሕቲቶ ፡ በባሕቲትከ ፡ ወገሥፆ ፡ ወሶበ ፡ ኢፈቀደ ፡ ከመ፡ ይነስሕ ፡ በባሕቲትከ ፡ ንሣእ ፡ ምስሌከ ፡ አሐደ ፡ በምዐ ፡ እው ፡ ክልኤተ ፡ ወአጠይቆ ፡ በፍሥሐ ፡ ትምህርተ ፡ መንፈሳዊተ ፡ ወለእመ ፡ ሠምረ ፡ በዝንቱ ፡ ነገርከሙ ፡ ሠናየ ፡ ይከውን ፡ ሎቱ ፡ ወእመሰ ፡ ኢተመይጠ ፡ እምጌጋዩ ፡ ንግሩ ፡ ለጉባኤ ፡ ከመ ፡ ይገሥጽዎ ። ወለእመ ፡ ኢተእዘዘ ፡ ለጉባኤ ፡ ንግሩ ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲ ያን ። ወለእመ ፡ ኢሰምዓ ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲ ያን ፡ ይኩን ፡ በኀቤከ ፡ እምሰለ ፡ መጥዓዊ ፡ ወመጸብሐዊ ፡ ወኢይሳተፍከ ፡ እስከ ፡ ይኔስሕ ። ወለእመ ፡ ነስሐ ፡ ወገብረ ፡ በከመ ፡ ገብረ ፡ መጸብሐዊ ፡ ወተመይጠ ፡ እምነ ፡ ስሕተቱ ፡ ያብእዎ ፡ ኀበ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ከመ ፡ ይሰ ማዕ ፡ ቃለ ፡ እግዚአብሔር ፡ እስከ ፡ ይትከሠት ፡ እምኀቤሁ ፡ ፍሬ ፡ ንስሐ ።

፻፵፩ ኦ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ኢትላተፎሙ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ፡ ጸሎታት ፤ ዳእሙ ፡ ያውዕእዎሙ ፡ እምድኅረ ፡ አንብቦተ ፡ ወንጌል ፡ ከመ ፡ ይትከዙ ፡ ላዕለ ፡ ዘኀለፈ ፡ እምኔሆሙ ፡ ወእለ ፡ ተርፉ ፡ እምኔ ሆሙ ፡ ይኩኑ ፡ ፍጹማነ ፡ ለጽዋዔ ፡ ወዘሂ ፡ ይሬእዮሙ ፡ ይትከዘን ፡ በእንቲአሆሙ ፡ ወይትዐ ቀብ ፡ ከመ ፡ ኢይደቅ ውስተ ፡ ዕልወት ፡ ወይ ፍራህ ፡ ከመ ፡ ኢይርከቦ ፡ ዘረከበ ፡ ኪያሆሙ ።

፻፵፪ ወለእመ ፡ እበስ ፡ ኃጥእ ፡ እሐደ ፡ ጊዜ ፡ እው ፡ ክልኤተ ፡ ኢትመንኖ ፡ ወኢትክልኦ ፡ እምተሳ ትፎ ፤ ዓዲ ፡ ተሳተፍ ፡ ምስሌሆሙ ፡ በጊዜ ፡ መብልዕ ፡ ወንስሐሆሙ ፡ ተወከፍ ፡ ሎሙ ፤ ወአልብሶሙ ፡ ልብሰ ፡ በአምሳለ ፡ ወልድ ፡



አይመን ፡ በሚገባ ፡ ነገር ፡ እርሱ ፡ ራሱ ፡ ይሥ ራው ፡ እንጂ ። በላያቸውም ፡ የሐሰት ፡ ምስክ ርን ፡ አይመን ።

፻፵ ልብህን ፡ በማስፋት ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ሁን ። ስለ ፡ ቅንዓቱና ፡ ስለክፋቱ ፡ ወንድ ሞቹን ፡ በሐሰት ፡ የሚከሰውን ፡ የነገረ ፡ ሠሪ ፡ ቃል ፡ ትቀበል ፡ ዘንድ ፡ አትበጣ ። እንደነዚህ ፡ ያሉት ፡ ሰዎች ፡ ሰላም ፡ ትኖር ፡ ዘንድ ፡ አይተ ውምና ። ዘወትር ፡ ተመልከታቸው ፡ ከነር ሱም ፡ ተጠበቅ ፡ ኃጢእተኞች ፡ ያልሆኑትን ፡ እንዳታጠፋ ። በተረዳ ፡ ሁናቴ ፡ እንደ ፡ ነገር ፡ ሥራቸው ፡ ሆኖ ፡ ብታገኘው ፡ እንደ ፡ እግዚአ ብሔር ፡ ትምህርት ፡ አድርግ ። (ማቴ ፡ ፲፰ ፡ ፲፭ - ፲፯) ። የከሰሱትን ፡ ሰው ፡ ብቻውን ፡ አድ ርገህ ፡ ለብቻህ ፡ ምከረው ። ብቻህን ፡ ነግረኸው ሊመለስ ፡ ባይወድ ፡ ከአንተ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ወይም ፡ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ ይዘህ ፡ በደስታ ፡ መን ፈሳዊ ፡ ትምህርትን ፡ አበረዳው ። ይህንንም ፡ መንፈሳዊ ፡ ትምህርታችሁን ፡ ቢቀበላችሁ ፡ በጎ ፡ ነገር ፡ ይሆንበታል ። ከስሕተቱ ፡ ባይመ ለስ ፡ ግን ፡ ለምእመናን ፡ ንገሩ ። ቤተ ፡ ክርስቲ ያንን ፡ ባይሰማት ፡ ግን ፡ በአንተ ፡ ዘንድ ፡ እንደ መጥዓዊና ፡ (አረማዊ) ፡ እንደ ፡ መጸብሐዊ ፡ ይሁን ። ንስሐ ፡ እስኪገባ ፡ ድረስ ፡ ከአንተ ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ አይሁን ። ቢመለስና ፡ መጸብ ሐዊ ፡ እንዳደረገው ፡ ቢያደርግ ፡ ከስሕተቱም ፡ ቢመለስ ፡ የንስሐ ፡ ፍሬ ፡ ከእርሱ ፡ ዘንድ ፡ እስ ኪገለጥ ፡ ድረስ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቃል ፡ ይሰማ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ያግ ቡት ።

፻፵፩ ኤጲስቆጶስ ፡ ሆይ ፡ በጸሎት ፡ ጊዜ ፡ ሁሉ ፡ አት ገናኛቸው ። ወንጌል ፡ ከተነበበ ፡ በኋላ ፡ ያስ ወጧቸው ፡ እንጂ ። ባለፈው ፡ ዘመናቸው ፡ ይተ ክዙ ፡ ዘንድ ፡ ከነርሱ ፡ የቀሩትም ፡ ለተጠሩበት፡ ዓላማ ፡ ፍጹማን ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ የሚያያቸ ውም ፡ ስለነርሱ ፡ ያዝን ፡ ዘንድ ፡ በስሕተ ትም ፡ እንዳይወድቅ ፡ ይጠበቅ ፡ ዘንድ ፡ እነር ሱንም ፡ ያገኘ ፡ እንዳያገኘው ፡ ያፈራ ፡ ዘንድ ።

፻፵፪ ኃጥእ ፡ ፩ ፡ ጊዜ ፡ ወይም ፡ ፪ ፡ ጊዜ ፡ ቢበድል ፡ ንቀህ ፡ ከአንድነት ፡ አትለየው ፡ በምግብ ፡ ጊዜ ፡ ከርሱ ፡ ጋር ፡ ተባበር ፡ እንጂ ። ንስሓቸ ውንም ፡ ተቀበል ፡ ተጸጽቶ ፡ ወደ ፡ አባቱ ፡ በተ መለሰው ፡ ልጅ ፡ አምሳል ፡ (ሉቃ ፡ ፲፭ ፡ ፲፯ -

ዘነሰሐ ፡ ወተመይጠ ፡ ኀበ ፡ አቡሁ ። ወአን
ብር ፡ እደ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ ህየንተ ፡ ጥምቀት ፡
እስመ ፡ በአንብሮ ፡ እዴነ ፡ እለ ፡ ይኔስሑ ፡
ይነሥኡ ፡ ጸጋ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ወሚጠሙ ፡
ኀበ ፡ ሙከናሆሙ ፡ ዘቀዳሚ ።

፻፴፫ ወከመዝ ፡ ፈውሶሙ ፡ ለኃጥአን ፡ ወግበር ፡
ሎሙ ፡ መድኃኒተ ፡ ሠናየ ፡ ወልምሉመ ፡ ወአ
ጽንዖሙ ፡ በነገረ ፡ ተግሣጽ ፡ ወአፅምም ፡ ቍስ
ላቲሆሙ ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ቍስል ፡ ለሙቱ ፡
ወምሉእ ፡ መግል ፡ ይፈውስም ፡ በመድኃኒት ፡
ጽኑዕ ፡ ዘውእቱ ፡ ነገረ ፡ ተግሣጽ ፡ ወአምድኀ
ሬሁ ፡ በነገረ ፡ ኑዛዜ ። ወለእመ ፡ ሰፍሐ ፡
ቍስል ፡ ወመተረ ፡ አባለ ፡ ወኢተረክበ ፡ ዘይ
ፌውሶ ፡ የኀሥሡ ፡ ሎቱ ፡ በጽኑዕ ፡ ሐተታ ፡
ወተዐቅቦ ፡ ወምክር ፡ ዐቃቤ ፡ ሥራይ ፡ ማእ
ምረ ፡ ወምትሮ ፡ በሕማም ፡ ወኀዘን ፡ ለአባል ፡
ዘማስነ ፡ ከመ ፡ ኢይማስኑ ፡ መለያልያት ፡ እለ ፡
ተርፉ ። እስመ ፡ ናሁ ፡ ይቤ ፡ ጽሑፍ ፡ ምልሑ ፡
እከየ ፡ እማእከሌክሙ ፡ ወኢትኩን ፡ ዘታፈ
ጥን ፡ ለመቲር ፡ ወኢይፋሬ ፡ ወኢረዋጼ ፡ ለወ
ሚር ፡ በሞሠርት ፡ ነዊኅ ፡ አሰናን ።

፻፴፬ ወእመኒ ፡ ኮነ ፡ መስተዋድይ ፡ ሐሳዌ ፡ ኢትሰ
ምዕዎ ። እስመ ፡ አንትሙ ፡ ለእመ ፡ ፈታሕ
ክሙ ፡ ፍትሐ ፡ ላዕለ ፡ ፩ኒ ፡ በዓመፃ ፡ አእምሩ ፡
ከመ ፡ ፍትሐ ፡ በቀል ፡ ትወፅእ ፡ እምነ ፡ አፉ
ክሙ ፡ ላዕለ ፡ ርእስክሙ ። ወለእመሰ ፡ ፈታሕ
ክሙ ፡ በኢያድልዎ ፡ አንትሙ ፡ ተአምሩ ፡
እምነ ፡ ዘያስተዋዲ ፡ ቢጾ ፡ በሐሰት ፡ ወዘንተ ፡
ሶበ ፡ አእመርከ ፡ ሐሳዌሁ ፡ በርእሱ ፡ ኵንኖ ፡
ከሡተ ፡ ወግበር ፡ ቦቱ ፡ በከመ ፡ ፈቀደ ፡ ይግ
በር ፡ ሰቢጹ ፡ ወረሰዮ ፡ ከሡተ ፡ ማእከለ ፡
ጉባኤ ፡ ከመ ፡ ቀታሌ ፡ እንሁ ፡ ውእቱ ፡ ወሶበ ፡
ነስሐ ፡ ሥራዕ ፡ ሎቱ ፡ ጾመ ፡ ወእምዝ ፡ አን
ብር ፡ እዴከ ፡ ላዕሌሁ ፡ ወተወከፎ ፡ እምድኅረ ፡
ተአዘዘ ፡ ውእቱ ፡ ከመ ፡ ኢይትመየጥ ፡ ወኢይ
ጽናዕ ፡ ኀበ ፡ ጌጋዩ ፡ ምዕረ ፡ ወካዕበ ፡ ወለእመ ፡
ኢተመይጠ ፡ እምነ ፡ እከዩ ፡ ይሰድድዎ ፡ እስመ
ገባሬ ፡ እኪት ፡ ውእቱ ፡ ከመ ፡ ኢያርኵሶ ፡ ቤተ ፡
ክርስቲያን ፡ ለእግዚአብሔር ።

፻፴፭ ወኢትፍትሑ ፡ በፍትሕ ፡ አሐዱ ፡ ላዕለ ፡
ኵሎን ፡ ኃጣውእ ፡ አኮ ፡ ፍትሑ ፡ ለዘይኤብስ ፡
በገቢር ፡ ከመ ፡ ዘይኤብስ ፡ በቃሉ ፡ አው ፡ በሕ
ሊናሁ ፡ እምሰብእስ ፡ ቦ ፡ ዘይደሉ ፡ ላዕሌሆሙ ፡



፳፩) ። ልብስ ፡ አልብሳቸው ፡ በጥምቀት ፡ ፈን
ታ ፡ እጅ ፡ በማኖር ፡ ባርካቸው ። ንስሐ ፡ የሚ
ገቡ ፡ ሰዎች ፡ በእጃችን ፡ በመባረክ ፡ የመን
ፈስ ፡ ቅዱስን ፡ ጸጋ ፡ ያገኛሉና ። ወደቀደመ ፡
ቦታቸውም ፡ መልሳቸው ።

፻፴፫ ኃጥአንን ፡ እንዲህ ፡ እያደረግህ ፡ አድናቸው ።
በጎ ፡ ልዝብ ፡ መድኃኒትን ፡ አድርግላቸው ፡
በምክር ፡ ቃልም ፡ አድናቸው ፡ ቍስላቸውንም ፡
አድርቅላቸው ። ቍስሉ ፡ ቢጐደጕድ ፡ መግ
ልንም ፡ የተመላ ፡ ቢሆን ፡ በጽኑዕ ፡ መድኃኒት ፡
ያድኑታል ፡ ይኸውም ፡ የምክር ፡ ቃል ፡ ነው ።
ከዚህም ፡ በኋላ ፡ በማረጋጋት ፡ ቍስሉ ፡ ቢሰፋ ፡
ሕዋሳትንም ፡ ቢቆርጥ ፡ የሚያድነውም ፡ ቢ
ታጣ ፡ አውጥተው ፡ አውርደው ፡ በመጠበቅና ፡
መክረው ፡ አዋቂ ፡ ሐኪም ፡ ይሹለታል ። የቀ
ሩት ፡ ሕዋሳት ፡ እንዳይጐዱ ፡ የተጐዳውን ፡
አባል ፡ እያዘንህ ፡ ቍረጠው ። እነሆ ፡ መጽ
ሐፍ ፡ ክፉውን ፡ ከመካከላችሁ ፡ ለዩ ፡ ብሏልና ።
(፩ ፡ ቆሮ ፡ ፭ ፡ ፪ )። ለመቍረጥ ፡ ፈጣን ፡ አት
ሁን ፡ ደፋርም ፡ አትሁን ፡ ጥርሱ ፡ ረጅም ፡ በሆ
ነ ፡ መጋዝ ፡ ለመቍረጥ ፡ የምትሮጥ ፡ አትሁን ።

፻፴፬ ነገረ ፡ ሠሪው ፡ ሐሰተኛ ፡ ቢሆን ፡ አትስሙት ።
እናንተስ ፡ በእንዱስ ፡ እንኳ ፡ በግፍ ፡ አትፍ
ረዱ ፡ የበቀል ፡ ፍርድ ፡ በራሳችሁ ፡ ላይ ፡ ከአፋ
ችሁ ፡ እንደምትወጣ ፡ እወቁ ። ባለማድላት ፡
ከፈረዳችሁ ፡ በሐሰት ፡ የሚያጣላውን ፡ ታው
ቁታላችሁ ። ሐሰተኛነቱን ፡ በራሱ ፡ ከወቅህ ፡
ገልጠህ ፡ ፍረድበት ፡ በባልንጀራው ፡ ላይ ፡
ሊያደርግ ፡ የነበረውን ፡ በእርሱ ፡ አድርግበት ።
ወንድሙን ፡ ገዳይ ፡ እንደመሆኑ ፡ በጉባኤ ፡ የተ
ገለጠ ፡ አድርገው ። ንስሐ ፡ ቢገባ ፡ ጾም ፡ ሥራ
ለት ። ንስሓ ፡ ከገባ ፡ በኋላ ፡ በእጅህ ፡ ባርከህ ፡
ተቀበለው ። ወደ ፡ ስሕተቱ ፡ ተመልሶ ፡ እንዳ
ይገባ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ ተቀበለው ።
ከኃጢአቱ ፡ ባይመለስ ፡ ግን ፡ ክፉ ፡ አድራጊ ፡
ነውና ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡
እንዳያረክስ ፡ ይለዩት ።

፻፴፭ በኃጢአቶች ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ ፩ ፡ ፍርድ ፡ አትፍ
ረዱ ። በሥራ ፡ የሚበድል ፡ ሰው ፡ ፍርድ ፡ ”
በቃሉ ፡ ወይም ፡ በሐሳቡ ፡ እንደሚበድል ፡
ሰው ፡ ፍርድ ፡ አይደለም ። ከሰዎች ፡ ወገን ፡

ተምስያ ፡ ባሕቲቱ ፡ ወበ ፡ ዘይመርሖ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ ምጽዋተ ፡ ከመ ፡ የሀቦ ፡ ለነዳያን ። ወበ ፡ ዘይመርሖ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ ጾመ ፡ ወለካልእንሂ ፡ ይሰደድዎሙ ፡ እምቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በአምሳለ ፡ ኃጢአቶሙ ፡ እንተ ፡ ገብርዋ ። እስመ ፡ ሕግ ፡ ኢይኤዝዝ ፡ አሐደ ፡ ከዊነ ፡ ላዕለ ፡ ኵሎሙ ፡ ኃጥአን ።

፻፴፮ እስመ ፡ አኮ ፡ ከዊነኡ ፡ ከመ ፡ ከዊነኡ ፡ ለዘ አበሰ ፡ ላዕለ ፡ እግዚአብሔር ፡ አው ፡ ላዕለ ፡ ካህን ፡ አው ፡ ላዕለ ፡ መቅደስ ፡ ከመ ፡ ዘአበሰ ፡ በዓመፃ ፡ ላዕለ ፡ ንዋየ ፡ አው ፡ ላዕለ ፡ አሐዱ ፡ እምነ ፡ አብያጺሁ ፡ ወኢኮነት ፡ ከዊነኡ ፡ ከመ ፡ ዘይትዔገሥ ፡ ቢጾ ፡ ወአግበርቶ ፡ ወከዊነ ፡ እምነ ፡ ዘይኤብስ ፡ ኀበ ፡ ወላድያኒሁ ፡ አው ፡ ኀበ ፡ እዝማዲሁ ። ወኢዘይኤብስ ፡ በፈቃዱ ፡ ከመ ፡ ዘይኤብስ ፡ ዘእንበለ ፡ ፈቃዱ ። እስመ ፡ ለሰብእ ፡ ይደልዎሙ ፡ ከዊነ ፡ ቦ ፡ በቀትል ፡ ወካልእንሂ ፡ በቅንዓት ፡ ቦ ፡ በፈድፋደ ፡ ንዋየሙ ፡ ወለካልእንሂ ፡ ከመ ፡ ይትገበር ፡ በሙ ፡ በከመ ፡ ገብሩ ፡ ላዕለ ፡ ቢጾሙ ። እእምሩ ፡ ከዊነ ፡ ኵሉ ፡ ኃጥአን ፡ ዘዘዚአሁ ፡ ከመ ፡ ኢይኩን ፡ በኀቢሮሙ ፡ ማዕሰ ። እስመ ፡ በከመ ፡ ኩንንክሙ ፡ ወፈታሕክሙ ፡ ይፈትሑ ፡ ላዕሌክሙ ።

፻፴፯ ዘ፲ወ፱ቱ ፡ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ኢጲስቆጶስ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይስአል ፡ በዘይከውን ፡ ሰላም ፡ ላዕለ ፡ ካልኣን ፡ ወይደሉ ፡ ሎቱ ፡ ፈድፋደ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ዝንቱ ፡ በኀቤሁ ፡ ወእመ ፡ አኮ ፡ እፎ ፡ ይሰነእዉ ፡ ብዙኃን ፡ ለእመ ፡ ኢኮነ ፡ ዝንቱ ፡ ስኢል ፡ በኀቤሁ ። ወዝንቱ ፡ ውእቱ ፡ ፈቃዱ ፡ ለክርስቶስ ፡ ከመ ፡ ይኩኑ ፡ ብዙኃን ፡ እለ ፡ ይድኅኑ ፡ ወከመ ፡ ኢትሣእ ፡ እምነ ፡ ኍልቍ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያናዊት ፡ አሐቲ ፡ ነፍስ ። ወናሁ ፡ ጸሐፍ ፡ ዘይቤ ፡ "ዘሰ ፡ ኢይትጋባእ ፡ ምስሌየ ፡ ውእቱ ፡ ይዘሩ ፡ ዘሀሎ ፡ ኀቤየ" ።

፻፴፰ ወለእመ ፡ ኮንከ ፡ ፋሉጠ ፡ እምነ ፡ አባግዕ ፡ ጸላኢሆሙ ፡ እንተ ፡ ወሰይጡ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ወማኅኮሊ ፡ አባግዕ ፡ ዘከማሆሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ ኖላዊ ። እፎ ፡ አንተ ፡ ትዘሩ ፡ ዘእስተጋብእናሆሙ ፡ ንሕነ ፡ እምነ ፡ አሕዛብ ፡



ቀኖና ፡ ብዙ ፡ የሚገባቸው ፡ አሉ ። ለድሆች ፡ ገንዘብ ፡ ይሰጡ ፡ ዘንድ ፡ የሚታዘዙም ፡ አሉ ። ጾም ፡ እንዲጾሙ ፡ የሚታዘዙም ፡ አሉ ፡ ሌሎቹን ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ሠሩት ፡ ኃጢአት ፡ መጠን ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ይለዩዋቸዋል ።

፻፴፮ ሕግ ፡ በኃጥአን ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ አንድ ፡ ፍርድን ፡ አያዝዝምና ፡ እግዚአብሔርን ፡ ወይም ፡ ካህኑን ፡ ወይም ፡ ቤተ ፡ መቅደሱን ፡ የበደለው ፡ ሰው ፡ ፍርድ ፡ በንብረት ፡ ላይ ፡ ግፍ ፡ እንደ ፡ በደለ ፡ ሰው ፡ ፍርድ ፡ ወይም ፡ ከጓደኞቹ ፡ አንዱን ፡ እንደ ፡ በደለ ፡ ሰው ፡ ፍርድ ፡ አይደለምና ። ፍርዱ ፡ ጓደኞሙንና ፡ ባሮቹን ፡ እንደሚበድል ፡ ሰው ፡ ፍርድ ፡ አይደለም ። ወላጆቹን ፡ ወይም ፡ ዘመዶቹን ፡ የሚበድል ፡ ሰው ፡ ቅጣቱ ፡ እንደ ፡ አይደለም ። በፈቃዱ ፡ የሚበድልና ፡ ያለፈቃዱ ፡ የሚበድል ፡ ቅጣቱ ፡ አንድ ፡ አይደለም ፡ ለበደሉት ፡ ሰዎች ፡ ቅጣት ፡ ይገባቸዋልና ። ሞት ፡ የሚፈረድበት ፡ አለ ፡ ሌሎችም ፡ ግርፋት ፡ የሚፈረድባቸው ፡ አሉ ፡ ገንዘብ ፡ እንዲከፍሉ ፡ የሚፈረድባቸው ፡ ሌሎችም ፡ በባልንጀራቸው ፡ ላይ ፡ እንዳደረጉት ፡ ያለ ፡ የሚፈረድባቸው ፡ አሉ ። በእናንተ ፡ ዘንድ ፡ ግፍ ፡ እንዳይፈጸም ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ የሆነውን ፡ የኃጥአንን ፡ ፍርድ ፡ እወቁ ፡ እንደፈረዳችሁ ፡ ይፈርዱባችኋልና ።

፻፴፯ ድስቅ ፡ ፲፱ ፡ ኢጲስቆጶስ ፡ ከሆነ ፡ በሌሎች ፡ ዘንድ ፡ ሰላም ፡ በሚጸና ፡ ገንዘብ ፡ መጸለይ ፡ ይገባዋል ። ይህ ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ሊሆን ፡ ይገባል ። ይህ ፡ ካልሆነ ፡ ጸሎቱም ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ካልተፈጸመ ፡ ብዙዎች ፡ እንዴት ፡ ይስማማሉ ። የክርስቶስ ፡ ፈቃዱ ፡ የሚድኑት ፡ የበዙ ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ነው ። ከቤተ ፡ ክርስቲያንም ፡ ቍጥር ፡ እንዲት ፡ ነፍስ እንኳ ፡ እንዳትጐድል ፡ ነው ። ከእኔ ፡ ጋር ፡ ያልሆነ ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ ያሉትን ፡ ይበትናቸዋል ፡ የሚል ፡ ጽሑፍ ፡ እነሆ ፡ አለ ። (ማቴ ፡ ፲፪ ፡ ፴ ፡ ሉቃ ፡ ፲፩ ፡ ፳፫)።

፻፴፰ ከበጎች ፡ የተለየህ ፡ ብትሆን ፡ ጠላታቸው ፡ አንተ ፡ ነህ ። የእግዚአብሔርም ፡ ባላጋራው ፡ ነህ ። እግዚአብሔር ፡ ጠባቂ ፡ የሆናቸውን ፡ በጎች ፡ የምታጠፋ ፡ አንተ ፡ ነህ ። እኛ ፡ ብዙ ፡ ቋንቋዎችን ፡ በመናገር ፡ በድካም ፡ በትጋትና ፡

ብዙኃን ፡ በልሳናት ፡ ብዙኅ ፡ በድካም ፡ ወበጻማ ፡ በትጋሀ ፡ ወበጸም ፡ በስኪብ ፡ ላዕለ ፡ ምድር ፡ ወተሰዶ ፡ በሙቃሔ ፡ ወሕማም ፡ ዘለዓለም ፡ እስከ ፡ ገበርነ ፡ ፈቃደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወእስከ ፡ መላእነ ፡ ቤቶ ፡ እምነ ፡ ሕዝብ ፡ ጽጡዓን ፡ ዘውእቶሙ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ጉባኤ ፡ ቅድስት ።

፻፴፱ ዘ፻፴፱ቱ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ሰፋሒ ፡ እዴሁ ፡ ዘየማን ፡ ወጸሐቅ ፡ ከመ ፡ መጋቢ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለፈጽሞ ፡ መፍቅዶን ፡ ለመበለታት ፡ ወለድኩታማን ፡ ወለእለ እልህሙ ፡ ማኅደረ ፡ ወለጽሁቃን ፡ ወለነኮሎሙ ፡ ንዳያን ፡ ምእመናን ፡ በዘ ይሴስዩ ፡ ውሉዶሙ ፡ ወበእንተ ፡ ሕማም ፡ ዘይረክቦሙ ።

፻፵ ዘ፻፵ቱ ፡ ጸሎቱ ፡ ይከውኖ ፡ በዘይተልዉ ክሙ ፡ ወጸሀቁ ለአብልዖቶሙ ፡ ወኢትኅድግዎሙ ፡ ይፀንሱ ፡ በምንትኒ ። ወለወራዛዊት ፡ ድንግል ፡ ረዐዩዋ ፡ እስከ ፡ ትበጽሕ ፡ ኀበ ፡ አምጣነ ፡ ተዋስቦ ፡ ወአስተዋስብዋ ፡ ለእሑዱ ፡ እምነ ፡ ምእመናን ፡ ወከማሁ ፡ ለወራዙት ፡ ካዕበ ፡ መሀርዎ ፡ ግብረ ፡ እድ ፡ ወአለብውዎ ፡ ወሴስይዎ ፡ በዘየሐዩ ፡ እስከ ፡ እመ ፡ ይክል ፡ ለቀውሞተ ፡ ነፍሱ ፡ በግብረ ፡ እደዊሁ ።

፻፵፩ ዘ፻፵፩ዱ ፡ ወይደልዉ ፡ ከመ ፡ ይጽሐቅ ፡ ለተማግጾ ፡ ሕዝባውያን ፡ ከመ ፡ ኢይግበሩ ፡ መርገመ ፡ በአፉሆሙ ። ወከመ ፡ ይጽሐቁ ፡ በኵሉ ፡ ለለአሐዱ ፡ እመሂ ፡ ለካህን ፡ እው ፡ ለሕዝባዊ ።

፻፵፪ በስ ፡ ዘ፻፵፪ቱ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ዘይለብስ ፡ ሜላተ ፡ እው ፡ ቀጠንተ ፡ እው ፡ ዘያሠረጉ ፡ ማእዶ ፡ በጣዕመ ፡ መባልዕት ፡ ዘበዚአሁ ፡ እንዘ ንዳያን ፡ ሀገሩ ፡ ርኁባን ፡ እሙ ፡ ስሩቃን ፡ ኢኮነ ፡ ውእቱ ፡ ኤጲስቆጶስ ።

፻፵፫ ማልስ ፡ ወይደልዎሙ ፡ ለሕዝብ ፡ ከመ ፡ ይትአዘዙ ፡ ሎቱ ፡ ወይግበሩ ፡ ምስሌሁ ፡ ዘአዘዞሙ ።

፻፵፬ ድስቅ ፡ ዘ፳ቱ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ውእቱ ፡ አዙኩሙ፡ እምኀሔተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘወሰደክሙ ፡ ዳግመ ፡ እማይ ፡ ወእመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ገሃነ ፡ ውእቱ ፡ እምላክክሙ ፡ በዲበ ፡ ምድር ፡ እምኀ



በጾም ፡ ከመሬት ፡ ላይ ፡ በመተኛትና ፡ በመሰደድ ፡ በመታሰርና ፡ በመከራ ፡ በመታመም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡ እስከመፈጸም ፡ ደርሰንና ፡ ከተጠሩት ፡ ሰዎች ፡ ወገን ፡ ቤቱን ፡ እስከ፡ መምላት ፡ ደርሰን ፡ ከብዙ ፡ ነገድ ፡ ውስጥ ፡ የሰበሰብናቸውን ፡ ምእመናን ፡ እንት ፡ እንደ ፡ ትበትናለህ ፡ እነርሱም ፡ የቅድስት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ጉባኤ ፡ ናቸው ።

፻፴፱ ድስቅ ፡ ፲፱ ። ኤጲስቆጶስ ፡ ሆይ ፡ ለመስጠት ፡ ቀኝ ፡ እጅህን ፡ ዘርጋ ። እግዚአብሔር ፡ የሾመህ ፡ መጋቢ ፡ እንደመሆንህ ፡ ረዳት ፡ የሌላቸውን ፡ ባልቴቶቹን ፡ ደካሞቹን ፡ ቤት ፡ የሌላቸውን ፡ የተጨነቁትን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ያመኑትን ፡ ድሆቹን ፡ ለመርዳት ፡ ልጆቻቸውን ፡ በሚመግቡ ፡ ገንዘብ ፡ የሚመግቡበትንና ፡ ስለ ሚያገኙቸውም ፡ መከራ ፡ ለመርዳት ፡ ትጋ ።

፻፵ ድስቅ ፡ ፲፰ ። ይከተሏቸው ፡ ዘንድ ፡ ድሀ ፡ አደጎቹን ፡ ጥሩ ፡ እነርሱን ፡ ለመመገብ ፡ ትጉ ፡ በማናቸውም ፡ ነገር ፡ ይቸገሩ ፡ ዘንድ ፡ አትተዋቸው ። ሕፃንነት ፡ ያላትንም ፡ ድንግል ፡ እካለ ፡ መጠን ፡ እስከታደርስ ፡ ድረስ ፡ ጠብቁት ፡ ከምእመናንም ፡ ለአንዱ ፡ አጋቧት ። እንደዚሁም ፡ ሕፃንነት ፡ ያለውን ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ተግባረ ፡ እድ ፡ አስተምሩት ። መጽሐፍን ፡ አስተምሩት ። ሥራ ፡ ሠርቶ ፡ ራሱን ፡ ችሎ ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ መግቡት ።

፻፵፩ ድስቅ ፡ ፳፱ ። በአፋቸው ፡ መርገም ፡ እንዳይናገሩ ፡ ሕዝቡን ፡ ለመገሠጽ ፡ ይተጋ ፡ ዘንድ ፡ ይገባል ። ለካህን ፡ ወይም ፡ ለሕዝባዊ ፡ ቢሆን ፡ ለያንዳንዱ ፡ በሥራው ፡ ሁሉ ፡ ይተጉ ፡ ዘንድ ፡ ይገባል ።

፻፵፪ በስ ፡ ፻፲፪ ። ሐር ፡ ወይም ፡ ቀጭን ፡ ልብስ ፡ የሚለብስ ፡ ወይም ፡ በአገሩ ፡ ነዳያን ፡ ተርበውና ፡ ታርዘው ፡ ሳሉ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ጣዕም ፡ ባለው ፡ ምግብ ፡ ማዕድን ፡ የሚያስጌጥ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ አይደለም ።

፻፵፫ ሦስተኛ ፡ ሕዝቡ ፡ ለርሱ ፡ መታዘዝና ፡ ያዘዛቸውንም ፡ ከርሱ ፡ ጋር ፡ መሥራት ፡ ይገባቸዋል ።

፻፵፬ ድስቅ ፡ ፳ ። ከውሃና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ዳግመኛ ፡ ከወለዳቸው ፡ ከእግዚአብሔር ፡ በታች ፡ ኤጲስቆጶሱ ፡ አባታችሁ ፡ ነው ። በእውነት ፡ ገዥ ፡ ከሆነው ፡ ከእግዚአብሔር ፡ በታች ፡

ሕተ ፡ እግዚአብሔር ፡ እምላክ ፡ ዘበእማን ። ወእግዚአብሔር ፡ ይቤ ፡ በአፈ ፡ ዳዊት ፡ ነቢይ ፡ "እንሰ ፡ እቤ ፡ አማልክት ፡ አንትሙ ፡ ወደቂቀ ፡ ልዑል ፡ ኵልክሙ ፡ ወካዕበ" ፡ ይቤ ፡ ኢትበል ፡ እኩየ ፡ ላዕለ ፡ አማልከት ፡ ወእሉ ፡ እሙንቱ ፡ ኤጲስቆጶሳት ።

፻፵፭ ዘሄቱ ፡ በእንተ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ አ ፡ ብእሲ ፡ ሰመየከ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሎቱ ፡ ወልደ ፡ እአምር ፡ በዝንቱ ፡ መጠን ፡ አክበረከ ፡ ወአክብሮ ፡ ለዘኮነከ ፡ ምክንያተ ፡ ለዝንቱ ፡ መዓርግ ፡ ዐቢይ ። እኮኑ ፡ ይቤ ፡ መጽሐፍ ፡ በእንተ ፡ እለ ፡ ወለዱከ ፡ በሥጋ ፡ አክብር ፡ "አባከ ፡ ወእመከ ፡ ከመ ፡ ትኩን ፡ ለከ ፡ ሕይወት" ። ወዘሰ ፡ ይቤ ፡ "ቃለ ፡ ሕሡመ ፡ ላዕለ ፡ አቡሁ ፡ እው ፡ ላዕለ ፡ እሙ ፡ ሞተ ፡ ለይሙት" ። እፎኑ ፡ ኢይደልወክሙ ፡ ከመ ፡ ታክብርዎሙ ፡ ፈድፋደ ፡ ለአበዊክሙ ፡ መንፈሳውያን ፡ እስመ ፡ እሙንቱ ፡ እስተብቊዕያን ፡ ለክሙ ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወወለዱክሙ ፡ ዳግመ ፡ በማይ ፡ ወበመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ወሴሰዩክሙ ፡ ሐሊበ ፡ ዘውእቱ ፡ ነገረ ፡ ትምህርት ፡ ወአጽንዑክሙ ፡ በቀኖናቲሆሙ ፡ ወረሰዩክሙ ፡ ድልዋነ ፡ ለተወክፎ ፡ ሥጋ ፡ መድኅን ፡ ወደም ፡ ክቡር ፡ ዘውእቱ ፡ ደመ ፡ እግዚእነ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ወእሙንቱ ፡ እንጽሑክሙ ፡ እምኃጢአትክሙ ፡ ወረሰዩክሙ ፡ ድልዋነ ፡ ለጸጋሁ ፡ ቅዱስ ፡ ወሱቱፋነ ፡ ለርስቱ ።

፻፵፮ ፍርህዎሙ ፡ እስመ ፡ እሙንቱ ፡ ተጸገዉ ፡ ሥልጣነ ፡ ሕይወት ፡ ወሞት ፡ እምኀበ ፡ እግዚአብብሔር ፡ ከመ ፡ ይኰንንዎ ፡ ለዘአበሰ ፡ ወይፍትሑ ፡ ላዕሌሁ ፡ ተኰንኖ ፡ በእሳት ፡ ዘለዓለም ። ወሶበ ፡ ነስሐ ፡ ይሰረዩ ፡ ሎቱ ፡ ኃጢአቶ ፡ ወያሕይውዎ ። ወበእንተ ፡ ዝንቱ ፡ ይደልወክሙ ፡ ከመ ፡ ታፍቅርዎ ፡ ለኤጲስቆጶስ ፡ በፍቅረ ፡ አብ ፡ ወትፍርህዎ ፡ ከመ ፡ ንጉሥ ፡ ወታክብርዎ ፡ አምሳለ ፡ እግዚአብሔር ።

፻፵፯ እንተኒ ፡ ይደልወከ ፡ ከመ ፡ ተሀበ ፡ ዘይደልዎ ፡ ወለውእቱኒ ፡ ይደሉ ፡ ላዕሌሁ ፡ ከመ ፡ ያሠኒ ፡ ምግባርሁ ፡ ዘተጸገወ ። እስመ ፡ ውእቱ ፡ መኰንን ፡ ዘኀረዮ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሠሪዐ ፡ ግብር ፡



በዚህ ፡ ዓለም ፡ ገዢቸሁ ፡ ነው ። እግዚአብሔርም ፡ በነቢዩ ፡ በዳዊት ፡ አፍ ፡ "እኔ ፡ ግን ፡ እናንተ ፡ አማልክት ፡ ናችሁ ፡ ሁላችሁም ፡ የልዑል ፡ ልጆች ፡ ናችሁ ፡ አልሁ ፡" ብሏል ። (መዝ ፡ ፹፩ ፡ ፮) ። ዳግመኛም ፡ በገዢዎች ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ አትናገር ፡ አለ ። (ዘፀ ፡ ፳፪ ፡ ፳፰) ። እነዚሁም ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ናቸው ።

፻፵፭ ድስቅ ፡ ፯ ። ስለ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ሲናገር ፡ ሰው ፡ ሆይ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልጁ ፡ ነህ ፡ አለህ ፡ በዚህ ፡ እንዴት ፡ እንዳከበረህ ፡ እወቅ ፡ ለዚህ ፡ ከፍተኛ ፡ ማዕረግ ፡ ምክንያት ፡ የሆነህን ፡ አክብረው ፡ መጽሐፍ ፡ "ሕይወት ፡ ትሆንልህ ፡ ዘንድ ፡ በሥጋ ፡ የወለዱህን ፡ አባትና ፡ እናትህን ፡ አክብር ፡" (ዘፀአ ፡ ፳ ፡ ፲፪ ። ፳፩ ፡ ፲፯) ። ያለ ፡ አይደለምን ። በአባቱ ፡ ወይም ፡ በእናቱ ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ቃል ፡ የተናገረ ፡ ግን ፡ ሞትን ፡ ይሙት ፡ ብሎ ፡ የለምን ፡ (ዘሌ ፡ ፳፩ ፡ ፲፰ - ፳፩) ። መንፈሳውያን ፡ አባቶቻችሁንማ ፡ እንዴት ፡ በብዙ ፡ ልታከብሩዋቸው ፡ አይገባችሁም ፡ እነሱ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ አማላጆቻችሁ ፡ ናቸውና ። ከውሀና ፡ ከመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ዳግመኛ ፡ ወለዷችሁ ። ወተት ፡ መገቧችሁ ፤ ይኸውም ፡ የትምሀርት ፡ ነገር ፡ ነው ። በሕጋቸውም ፡ አጸኑዋችሁ ፡ የሚያድን ፡ ሥጋንና ፡ የከበረ ፡ ደምን ፡ ለመቀበል ፡ እንድትበቁ ፡ አደረጓችሁ ፡ ይኸውም ፡ የጌታችን ፡ የኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ደም ፡ ነው ። እነርሱ ፡ ከኀጢአታችሁ ፡ ሁሉ ፡ አነጿችሁ ። የመንፈስ ፡ ቅዱስን ፡ ጸጋ ፡ ለመቀበል ፡ የበቃችሁና ፡ የርስቱ ፡ ተካፋዮች ፡ አደረጓችሁ ።

፻፵፮ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የሕይወትና ፡ የሞት ፡ ሥልጣን ፡ ተሰጥቷቸዋልና ፡ አክብሩዋቸው ። የበደለውን ፡ ይቀጡ ፡ ዘንድ ፤ ዘለዓለማዊ ፡ የእሳት ፡ ቅጣትንም ፡ ይፈርዱ ፡ ዘንድ ፡ ንስሐ ፡ ቢገባ ፡ ግን ፡ ኃጢአቱን ፡ አስተሥርየው ፡ ያድኑት ፡ ዘንድ ። ስለዚህም ፡ ኤጲስቆጶሱን ፡ በአባት ፡ ፍቅር ፡ ልታፈቅሩት ፡ ይገባል ፤ እንደ ንጉሥም ፡ ልትፈሩት ፤ እንደ ፡ እግዚአብሔርም ልታከብሩት ፡ ይገባችኋል ።

፻፵፯ አንተም ፡ የሚገባውን ፡ ልትሰጠው ፡ ይገባል ። እርሱም ፡ የተቀበለውን ፡ ሹመት ፡ ሊያቃናልህ፡ ይገባዋል ። የቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡ ሥራ ፡ ለመሥራት ፡ እግዚአብሔር ፡ የመረጠው ፡ ሹም ፡

ቤተ ፡ ክርስቲያናዊት ፡ ወኢይደሉ ፡ ከመ ፡ ትት
ሐሰቦ ። ወፍጻሜሁ ፡ ለዝ ፡ ቃል ፡ ተጽሕፈ ፡
በአንቀጽ ፡ ምጽዋት ።
፻፵፰ ዘኒቅያ ፡ ዘ፵ወ፰ቱ ፡ ወይኩን ፡ ላዕለ ፡ ኵሉ ፡
ሀገር ፡ ሥሩዕ ፡ በረከተ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ በአም
ጣነ ፡ ክሂሎታ ፡ ወያምጽአዋ ፡ ኪያሃ ፡ ኀቤሁ ፡
ቀሳውስት ፡ በኵሉ ፡ ዓመታት ፡ ወኀበ ፡ ሰብአ ፡
ሀገር ፡ ወአድባር ፡ ዐዊዶሙ ፡ ያምጽኡ ፡ ሎቱ ፡
ከመ ፡ ይትራዳእ ፡ በውእቱ ፡ መፍቅዶ ።
፻፵፱ ድስቅ ፡ ዘ፵፱ቱ ፡ እመቦ ፡ ዘይተሉ ፡ ኖላዌ ፡ አኩየ ፡
ሞቱ ፡ ክሡት ፡ በቅድሜሁ ።
፻፶ ረስጣ ፡ ዘ፶ወ፩ቱ ፡ አመቦ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ዘፈ
ቀደ ፡ በሕጸተ ፡ እአምሮቱ ፡ በቀለ ፡ ኢኮነ ፡
ውእቱ ፡ ኤጲስቆጶስ ። ዳእሙ ፡ ስም ፡ ሕሰው ፡
ሀሎ ፡ ላዕሌሁ ፡ እኮ ፡ ውእቱ ፡ እምኀበ ፡ እግዚአ
ብሔር ፡ ዳእሙ ፡ እምኀበ ፡ ሰብእ ።

፻፶፩ ራብዕ ፡ በእንተ ፡ ህልዎቱ ፡ ምስለ ፡ ካህናት ፡
ወምስለ ፡ ሊቃነ ፡ ካህናት ፡ ወምስለ ፡ ካህና
ትስ ፡ ባሕቲቶሙ ፡ ፈድፋደ ፡ ይቤሎ ፡ ጳው
ሎስ ፡ ሐዋርያ ፡ ለቲቶ ፡ ረድኡ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡
"አእምር ፡ ከመ ፡ አነ ፡ ኀደጉከ ፡ ታሠኒ ፡ ግብረ ፡
ዘሐፀ ፡ ወትሢም ፡ ቀሲሳነ ፡ በውስተ ፡ ሀገር ፡
ወአህጉር ፡ እለ ፡ አልቦሙ ፡ ነውር ፡ ላዕሌ
ሆሙ" ። ወፍጻሜ ፡ ዝንቱ ፡ ሀሎ ፡ በአንቀጸ ፡
ቀሳውስት ። ወነዋ ፡ ይነግር ፡ በአንቀጸ ፡ ቅዳሴ ፡
ከመ ፡ ውእቱ ፡ ይቁም ፡ በቅድመ ፡ ምሥዋዕ ፡
ወከመ ፡ ይዝክሩ ፡ ስሞ ፡ በኵሉ ፡ ጸሎት ።

፻፶፪ ረስጣ ፡ ዘ፶ወ፫ቱ ፡ ወኢይትዐበይ ፡ ኤጲስቆ
ጶስ ፡ ላዕለ ፡ ቀሳውስት ፡ ወዲያቆናት ፡ ወቀሳ
ውስትኒ ፡ ላዕለ ፡ ዲበ ፡ ሕዝብ ።
፻፶፫ ዘ፷ወ፩ዱ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ይባርክ ፡ ወኢይባርኩ ፡
ኪያሁ ፡ ወይሢም ፡ ሰብአ ፡ ወይትወከፍ ፡ አውሎ
ግያ ፡ እምኀበ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ወአኮ ፡ እም
ኀበ ፡ ቀሳውስት ፡ ወይምትር ፡ ኵሎ ፡ ካህነ ፡
ዘይደልዎ ፡ ምትረት ፡ ዘእንበለ ፡ ኤጲስቆጶስ ።
እስመ ፡ ሎቱስ ፡ ኢይደልዎ ፡ ይግበር ፡ ዘንተ ፡
እምኀቤሁ ፡ በባሕቲቱ ።
፻፶፬ ዘኒቅያ ፡ ፷ወ፪ቱ ፡ ወይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይጽሐፍ ፡
ወያእምር ፡ ኵሎ ፡ መዓርጋተ ፡ ካህናት ፡ ወሥር
ዓታቲሆሙ ፡ ከመ ፡ ኢይኩን ፡ ማእከሌሆሙ ፡

ነውና ። ልትቆጣጠረውም ፡ አይገባህም ። የዚህ
ቃል ፡ ፍጻሜ ፡ በአንቀጸ ፡ ምጽዋት ፡ ተጽፎ
አል ። (ፍትሐ ፡ ነገ ፡ ፲፯ ፡ ፮፻፵፬) ።
፻፵፰ ኒቅያ ፡ ፵፰ ። የኤጲስቆጶሱ ፡ ገጸ ፡ በረከት ፡ በያ
ገሩ ፡ እንደ ፡ ችሎታዋ ፡ መጠን ፡ ይታዘዝ ።
ቀሳውስት ፡ ይህችን ፡ በየዓመቱ ፡ ወደርሱ ፡
ያምጡት ። በዚህ ፡ ገንዘብ ፡ ሊረዳ ፡ የሚሻውን ፡
ይረዳ ፡ ዘንድ ፡ በየከተማውና ፡ በየገጠሩ ፡ ዞረ
ው ፡ ያምጡለት ።
፻፵፱ ድስቅ ፡ ፵፱ ። ክፉ ፡ ጠባዩን ፡ የሚከተል ፡ ሰው ፡
ቢኖር ፡ ሞቱ ፡ በፊቱ ፡ የተገለጠ ፡ ነው ።
፻፶ ረስጣ ፡ ፶፩ ። በአእምሮው ፡ ጕድለት ፡ ምክን
ያት ፡ በቀልን ፡ የሚሻ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ቢኖር ፡
እርሱ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ አይደለም ፤ በሐሰት ፡ ኤጲ
ስቆጶስ ፡ ይባላል ፡ እንጂ ፡ ሹመቱም ፡ ከእግዚ
አብሔር ፡ ዘንድ ፡ የተገኘ ፡ አይደለም ፤ ከሰው ፡
የተገኘ ፡ ነው ፡ እንጂ ።
፻፶፩ አራተኛው ፡ ከካህናትና ፡ ከሊቃነ ፡ ካህናት ፡
ጋር ፡ ይልቁንም ፡ ከካህናት ፡ ጋር ፡ መኖር ፡
እንደሚገባው ፡ ይናገራል ። ሐዋርያው ፡ ጳው
ሎስ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ለሆነው ፡ ለደቀመዝሙሩ ፡
ለቲቶ ፡ "የጐደለውን ፡ ትሞላ ፡ ዘንድ ፡ ነውር ፡
የሌለባቸውንም ፡ ሰዎች ፡ በከተማና ፡ በገጠር ፡
ቀሳውስት ፡ አድርገህ ፡ ትሾም ፡ ዘንድ ፡ እንደ
ተውሁህ እወቅ ፡" አለው ። (ቲቶ ፡ ፩ ፡ ፭) ።
የዚህም ፡ ፍጻሜ ፡ በአንቀጸ ፡ ቀሳውስት ፡ አለ ።
(ፍትሐ ፡ ነገ ፡ ፮ ፡ ፪፻፶፫) ። በመሠዊያው ፡ ፊት
እንዲቆም ፡ ስሙንም ፡ በጸሎት ፡ ሁሉ ፡ እንዲ
ያነሡ ፡ እነሆ ፡ በአንቀጸ ፡ ቅዳሴ ፡ ተነግሮ
አል ። (ፍትሐ ፡ ነገ ፡ ፲፪ ፡ ፭፻፷፰) ።
፻፶፪ ረስጣ ፡ ፶፫ ። ኤጲስቆጶስ ፡ በቀሳውስትና ፡ በዲ
ያቆናት ፡ ላይ ፡ አይታበይ ፤ ቄሶችም ፡ እንዲሁ ፡
በሕዝብ ፡ ላይ ፡ አይታበዩ ።
፻፶፫ ፷፩ ። ኤጲስቆጶስ ፡ ይባርክ ፡ እርሱን ፡ ግን ፡
አይባርኩት ። ሰዎችን ፡ ይሹም ። ከቄሶች ፡
ያይደለ ፡ ከኤጲስቆጶሳት ፡ ዘንድ ፡ አውሎጊያ ፡
(ቡራኬ) ፡ ይቀበል ። ሊሻር ፡ የሚገባውን ፡
ካህን ፡ ሁሉ ፡ ይሻር ፤ ይኸውም ፡ ከኤጲስቆጶስ፡
በቀር ፡ ነው ፤ ኤጲስቆጶስ ፡ ብቻውን ፡ ይህን ፡
ማድረግ ፡ አይገባውምና ።
፻፶፬ ኒቅያ ፡ ፷፪ ። የካህናቱን ፡ መዓርጋትና ፡ ሥርዓ
ታቸውን ፡ ጽፎ ፡ ማወቅ ፡ ይገባዋል ። በዚህ ፡
ሥራ ፡ በመካከላቸው ፡ ጠብ ፡ ክርክር ፡ እንዳይ

ጋእዝ ፡ በዝንቱ ፡ ግብር ። ወከመ ፡ ኢይፃመሩ ፡ ሰብአ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እንተ ፡ ሐዋርያት ፡ ምስለ ፡ ሕዝባውያን ፡ በመዓርግ ፡ ወእመ ፡ አኮ ፡ ምስለ ፡ ሊቃነ ፡ ካህናት ፡ በእምሳሊሆሙ ።

፻፶፩ ድስቅ ፡ ዘ፳ቱ ፡ ኩኑ ፡ አ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ በበይናቲከሙ ፡ በአሐዱ ፡ ልብ ፡ ወተሳተፉዎሙ ፡ በጊዜ ፡ ሕማም ፡ ወአሕይዎሙ ፡ ለአኃው ፡ ወረዐይዎሙ ፡ ለሕዝብ ፡ በተሰናእዎ ፡ ወበንጽሐ ፡ ልብ ፡ ለመድኃኒቱ ፡ ዚአሆሙ ። ወመሀርዎሙ ፡ ከመ ፡ ይኩኑ ፡ በአሐዱ ፡ ፈቃድ ፡ ወበአሐዱ ፡ መንፈስ ፡ በሐዱ ፡ ሥጋ ። ወድልዋን ፡ በአሐዱ ፡ ኃልዮ ፡ ወበአሐዱ ፡ ምክር ፡ በከመ ፡ አዘዘ ፡ እግዚእነ ።

፻፶፪ ረስጠብ ፡ ዘ፲ቱወ፩ዱ ፡ ወኢይደልዎ ፡ ለኤጲስቆጶስ ፡ ከመ ፡ ይኅድግ ፡ መንበሮ ፡ ወሀገሮ ፡ ወይሑር ፡ ኀበ ፡ ካልእ ፡ ሀገር ፡ ዘእንበለ ፡ ከመ ፡ ይዕርቅ ፡ ካልአኒሁ ፡ ኤጲስቆጶሳተ ፡ እለ ፡ ከማሁ ፡ ሀቦሙ በቀዊት ፡ ለሰብአ ፡ ይእቲ ፡ ብሔር ፡ በውስተ ፡ ሕጎሙ ፡ በእንተ ፡ ሥርየተ ፡ አበሳሆሙ ፡ ወይንበር ፡ እስከ ፡ ይትፈጸም ፡ መፍቅዶሙ ።

፻፶፫ ዘኒቅያ ፡ ዘ፯ቱ ፡ ወኢይትወከፍ ፡ አሐዱሂ ፡ እም ኤጲስቆጶሳት ፡ ብእሴ ፡ ዘአውገዞ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ካልኡ ፡ ኢእምነ ፡ ካህናት ፡ ወኢእምነ ፡ መነከሳት ፡ ወእምሕዝባውያንሂ ፡ ካዕበ ፡ ወኢይፍታሕ ፡ ዘአውገዞ ፡ ወኢይግበር ፡ ሎቱ ፡ ሥርየተ ፡ ጸሎት ፡ ከመ ፡ ኢይኩን ፡ ውእቱ ፡ አስተቃልሎ ፡ ለዘአውገዞ ፡ ኤጲስቆጶስ ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ዝኩ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ አኩየ ፡ ወገፋዒ ፡ በዘ ተዐውቀ ፡ በኀቤሆሙ ፡ ተዓድዎቱ ፡ ይደሉ ፡ ከመ ፡ ይልአኩ ፡ ኀበ ፡ ጳጳስ ፡ ዘላዕሌሁ ፡ ውኀበ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ እለ ፡ ከማሁ ፡ ከመ ፡ ይጽሐፉ ፡ ሎቱ ፡ በእንተ ፡ ግብሩ ፡ ወይንግርዎ ፡ ወእመሰ ፡ አበየ ፡ ይረድ ፡ እመዓርጊሁ ።

፻፶፬ ዘ፰ወ፷ቱ ፡ ወኢይሑር ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ኀበ ፡ ካልእ ፡ ሀገር ፡ እምነ ፡ ሀገሩ ፡ ዘኮነ ፡ ላዕሌሁ ፡ ወተሠይመ ፡ ኤጲስቆጶስና ፡ በእንተ ፡ ራኅበ ፡ ብሔር ፡ ወናእስ ፡ ዚአሃ ፡ ወውኅደተ ፡ ሰብእ ፡ ወበረከታቲሃ ፡ ወበእንተዝ ፡ ከመ ፡ ይኅሥሥ ፡ ለዘውእቱ ፡ ይኄይስ ፡ እምኔሃ ። እስመ ፡ ዝንቱስ ፡ ዘኢይድልው ፡ ሎቱ ፡ አላ ፡ ለኵሉ ፡ ሰብእ ፡ ተውህቦ ፡ መክፈልት ፡ እምኀበ ፡ እግዚአብ



ሆን ፡ ሐዋርያት ፡ የመሠረቷት ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሰዎችም ፡ በመዓርግ ፡ ከሕዝባውያን ፡ ጋር ፡ እንዳይተካከሉ ፡ ይህም ፡ ባይሆን ፡ በእነርሱ ፡ አምሳል ፡ ከሊቃነ ፡ ካህናት ፡ ጋር ፡ እንዳይገናኙ ።

፻፶፩ ድስቅ ፡ ፳ ። ኤጲስቆጶሳት ፡ ሆይ ፡ እርስበርሳችሁ ፡ አንድ ፡ ልብ ፡ ሁኑ ። በመከራም ፡ ጊዜ ተባበሩዋቸው ። ወንድሞችን ፡ አድኗቸው ለድኅነታቸውም ፡ በንጹሕ ፡ ልቡና ፡ በመስማማት ፡ ሕዝቡን ፡ ጠብቋቸው ። በአንድ ፈቃድ ፡ በአንድ ፡ መንፈስ ፡ በአንድ ፡ አካል ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ጌታችን ፡ እንዳዘዘ ፡ በአንድ ሐሳብ ፡ በአንድ ፡ ምክር ፡ የተዘጋጁ ፡ ይሆኑ ዘንድ ። (ዮሐ ፡ ፲፯ ፡ ፳ - ፳፫) ።

፻፶፪ ረስጠብ ፡ ፲፩ ። ኤጲስቆጶስ ፡ መንበሩንና ፡ ሀገረ ፡ ስብከቱን ፡ ይተው ፡ ወደሌላም ፡ አገር ፡ ይሄድ ፡ ዘንድ ፡ አይገባውም ። በሕጋቸው ፡ ውስጥ ፡ ኃጢአታቸውን ፡ ለማስተሥረይ ፡ ለዚያች ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ ጥቅም ፡ ያላቸውን ፡ ወንድሞቹን ፡ ለማስታረቅ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ ሊሄድ ፡ አይገባውም ። ፈቃዳቸውም ፡ እስኪፈጸም ፡ ድረስ ፡ ይቈይ ።

፻፶፫ ኒቅያ ፡ ፯ ። ከኤጲስቆጶሳት ፡ ወገን ፡ አንዱ ፡ ስንኳ ፡ ሌላው ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ያወገዘውን ፡ ከካህናት ፡ ወይም ፡ ከመነኮሳት ፡ ዳግመኛም ፡ ከሕዝባውያን ፡ ወገን ፡ ቢሆን ፡ አይቀበል ። ያወገዘውንም ፡ አይፍታ ፡ ጸሎተ ፡ ሥርየትም ፡ አይድገምለት ። ያወገዘውን ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ማቃለል ፡ እንዳይሆን ። ይህም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ክፉ ፡ በደለኛም ፡ ቢሆን ፡ መተላለፉ ፡ በእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ በታወቀ ፡ ግንዛብ ፡ ስለሥራው ፡ ፈጽመው ፡ ይነግሩት ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ እርሱ ፡ ወደአሉ ፡ ኤጲስቆጶሳትና ፡ ወደበላዩ ፡ ጳጳስ ፡ ሊልኩ ፡ ይገባል ፡ አንቢ ፡ ቢል ፡ ከመዓርጉ ፡ ይዋረድ ።

፻፶፬ ኒቅያ ፡ ፷፰ ። ኤጲስቆጶስ ፡ በአገሩ ፡ መስፋትና ፡ መጥበብ ፡ በሕዝቡ ፡ ማነስና ፡ ብዛት ፡ ምክንያት ፡ ኤጲስቆጶስነት ፡ ከተሾመበት ፡ አገር ፡ ወጥቶ ፡ ወደሌላ ፡ አገር ፡ አይሂድ ። ስለዚህም ፡ ከእርስዋ ፡ የሚሻለውን ፡ ሊፈልግ ፡ አይገባውም ፡ ይህ ፡ ለእርሱ ፡ አይገባውምና ። ለሰው ፡ ሁሉ ፡ ድርሻው ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ተሰጥቶታል ፡ እንጂ ። ይህ ፡ ከሕዝባውያን ፡ ወገን ፡

ሐሰ ። ወዘንቱሰ ፡ ይትሜሰል ፡ አምሳለ ፡ እለ ፡ አውሰቡ ፡ ብእሲተ ፡ እምነ ፡ ሕዝባውያን ፡ ለእመ ፡ ተበቅለ ፡ ብእሲ ፡ በብእሲቱ ፡ ዘእንበለ ፡ በምክንያተ ፡ ዝሙት ፡ ለእመ ፡ ፈቀደ ፡ ወልሂቃ ፡ በዘትሜኒ ፡ እምኔሃ ፡ ውእቱ ፡ መአብስ ፡ ፈድፋደ ። ወከማሁኬ ፡ ኤጲስቆጶሳትኒ ፡ ወካህናት ፡ እለ ፡ የኀሥሡ ፡ ፈድፋደ ፡ ዘይኄይስ ፡ እምአብያቲሆሙ ፡ በእንተ ፡ አውግዞናሆሙ ፡ ወመተርጓሆሙ ። እስመ ፡ ዝንቱሰ ፡ ልማድ ፡ እኩይ ፡ ውእቱ ።

፻፵፱ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ምክንያት ፡ ለኤጲስቆጶስ ፡ በዘይሰደድዎ ፡ እምነ ፡ ሀገሩ ፡ እስከ ፡ ኢይረክብ ፡ መካነ ፡ ዘዘይፈልስ ፡ እምኔሃ ፡ ይእተ ፡ ጊዜ ፡ ብዉሕ ፡ ሎቱ ፡ ወይደልዎ ፡ ይሰድድዎ ፡ ካልእተ ፡ ሀገረ ፡ እምከመ ፡ አእመሩ ፡ ንጽሐ ፡ ዚአሁ ፡ ወሥነ ፡ መግቦቱ ፡ ወሃይማኖቱ ፡ ከመ ፡ ኢተወለጠ ፡ በዝንቱ ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ድልወ ፡ ያፍልስዎ ፡ ኀበ ፡ ዘይትሌዓል ፡ እስመ ፡ እኮ ፡ በፍትወቱ ፡ ልቡ ፡ ዘፈለሰ ፡ እመካኑ ።

፻፶ ድስቅ ፡ ዘ፲ወ፩ዱ ፡ ወለእመ ፡ በጽሐ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ኀበ ፡ መንበረ ፡ ካልኡ ፡ እንዘ ፡ የኀሥሥ ፡ ከብረ ፡ ወውዳሴ ፡ ወነበረ ፡ ባቲ ፡ ነዋኀ ፡ ዘመነ ፡ በእንተ ፡ ዘሠነየ ፡ ፍልሰቱ ፡ ወአእመረ ፡ ሕጸተ ፡ አእምሮቱ ፡ ለኤጲስቆጶስ ፡ በዓለ ፡ ውእቱ ፡ መንበር ፡ ዘመጽአ ፡ ኀቤሁ ፡ መፍትው ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ኢይመንኖ ፡ ለኤጲስቆጶስ ፡ በዓለ ፡ መንበር ፡ ወኢያስተሐቅሮ ፡ ወኢያሰክፎሙ ፡ ለእለ ፡ ያፈቅዱ ፡ በረከተ ፡ ፍጹመ ፡ እምነ ፡ ካህናት ፡ ዲአሙ ፡ ይኩን ፡ በራኬ ፡ ለበዓለ ፡ መንበር ፡ ከመ ፡ ኢይመንንዎ ፡ ሰብእ ። ወይደሉ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ኢይግባእ ፡ ወኢይትገንዲ ፡ እምቤተ ፡ ክርስቲያን ። ወኢይደልዎ ፡ ይደግር ፡ ውስተ ፡ ግብረ ፡ መፍቅዳቲሁ ፡ ዘይበዝኅ ፡ እምሠለስቱ ፡ ሰናብት ። ወእመኒ ፡ ተገፈ ፡ ውስተ ፡ መካኑ ፡ በእንተ ፡ ግብረ ፡ እደዊሁ ፡ ኢያብዝኅ ፡ ሰብአ ፡ ዘእንበለ ፡ ሠለስቱ ፡ እደው ።

፻፶፩ ረስጠ፳ ፡ ዘ፸ ፡ ኢይትወከፉ ፡ ስምዐ ፡ ሐራ ፡ ጥቃ ፡ ዘውእቶሙ ፡ በላውያን ፡ ላዕለ ፡ ኤጲስቆጶስ ።

፻፶፪ ረስጠብ ፡ ዘ፲ወ፪ቱ ፡ ወኢይትወከፉ ፡ ላዕሌሁ ፡ ስምዐ ፡ እሐዱ ፡ ኤጲስቆጶስ ።

፻፶፫ ኅምስ ፡ በእንተ ፡ ተጋብአቶሙ ፡ ለኤጲስቆጶሳት ፡ ወውእቱ ፡ በኵሉ ፡ ዓመታት ፡ ፪ተ ፡ ጊዜ ፡



ሚስት ፡ ያገቡ ፡ ሰዎችን ፡ ይመስላል ። ያለዝሙት ፡ ምክንያት ፡ ሰው ፡ ከሚስቱ ፡ ቢሰነካከል ፡ ከእርሰዋ ፡ በምትበልጥ ፡ ሊለውጣትም ፡ ቢፈልግ ፡ እርሱ ፡ በጣም ፡ በደለኛ ፡ ነው ። ከአገራቸው ፡ የተሻለ ፡ አገርን ፡ የሚፈልጉ ፡ ኤጲስቆጶሳትም ፡ ካህናትም ፡ እንደዚሁ ፡ ናቸው ። ስለ ዚህም ፡ አውግዘን ፡ ለየናቸው ። ይህ ፡ ልማድ ፡ መጥፎ ፡ ነውና ።

፻፵፱ ኤጲስቆጶሱ ፡ የሚሰደድበት ፡ አገር ፡ እስኪያጣ ፡ ድረስ ፡ ደርሶ ፡ ምክንያቱ ፡ በሚያሳድዱት ፡ ጊዜ ፡ ቢሆን ፡ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ ይገባዋል ። ንጽሕናውና ፡ የአስተዳደሩ ፡ ችሎታ ፡ ሃይማኖቱም ፡ በዚህ ፡ እንዳልተለወጠ ፡ ካወቁ ፡ ወደሌላይቱ ፡ አገር ፡ ሊሰዱት ፡ ይገባዋል ። ያፈልሱት ፡ ዘንድ የሚበቃ ፡ ከሆነም ፡ ወደ ፡ ከፍተኛ ፡ መዓርግ ፡ ያውጡት ። ከቦታው ፡ የወጣ ፡ በራሱ ፡ ፈቃድ ፡ አይደለምና ።

፻፶ ድስቅ ፡ ፲፩ ። ኤጲስቆጶስ ፡ ክብሩ ፡ ውዳሴን ፡ በመፈለግ ፡ ወደሌላው ፡ ሀገረ ፡ ስብከት ፡ ቢመጣ ፡ ስደቱም ፡ ስለተመቸው ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ በርሷ ፡ ቢቆይ ፡ የዚያም ፡ አገር ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ያልተማረ ፡ መሆኑን ፡ ቢያውቅ ፡ የአገሩን ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ሊንቀውና ፡ ሊያቃልለው ፡ አይገባም ። ከካህናትም ፡ ወገን ፡ ከሀኑትን ፡ ለመቀበል ፡ ለሚፈልጉት ፡ ክህነትን ፡ አይስጥ ። ሰዎቹ ፡ እንዳይንቁት ፡ ቡራኬው ፡ ለበዓለ ፡ መንበር ፡ ይሁን ፡ እንጂ ። ሊሾም ፡ አይገባውም ። ከቤተ ፡ ክርስቲያንም ፡ አይዘግይ ። ፈቃዱን ፡ ለመፈጸም ፡ ከ፫ ፡ ሰንበት ፡ የበለጠ ፡ መሰንበት ፡ አይገባውም ። የእጅ ፡ ሥራ ፡ ለማሠራት ፡ ከቦታው ፡ ቢሰነብት ፡ ከሦስት ፡ ሰው ፡ በቀር ፡ ሰው ፡ አያብዛ ።

፻፶፩ ረስጠ፳ ፡ ፸ ። በኤጲስቆጶስ ፡ ላይ ፡ የሐራ ፡ ጥቃን ፡ ምስክርነት ፡ አይቀበሉ ፡ እነርሱም ፡ መናፍቃን ፡ ናቸው ።

፻፶፪ ረስጠብ ፡ ፲፪ ። በርሱ ፡ ላይ ፡ ያንዱን ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ምስክርነት ፡ አይቀበሉ ።

፻፶፫ አምስተኛው ፡ ስለ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ መሰብሰብ ፡ ይናገራል ። ይኸውም ፡ በዓመት ፡ ሁለት ፡ ጊዜ፡

ወበእንተእሆሙ ፡ ፪ቱ ፡ ቃላት ።

፻፳፬ ቀዳሚሃ ፡ ረስጠብ ፡ ዘ፳ወ፺ቱ ፡ ረስጠ፫ ፡ ዘ፳ወ፷ቱ ፡ ጳክ ፡ ዘ፳ ፡ ወይእቲ ፡ ጉባኤ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ፪ቱ ፡ ጊዜ ፡ በበዓመት ፡ ወይትናገሩ ፡ ዘይከውን ፡ በእንተ ፡ ግብረ ፡ አብያተ ፡ ክርስቲያኒሆሙ ፡ ወከሡ ፡ በዐጸበ ፡ ላዕለ ፡ መንፈቆሙ ፡ ፍትሔሁ ፡ ወሥርዓቱ ፡ ወያሰስሉ ፡ ዕቅፋታተ ፡ እለ ፡ ይከውና ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ። ወለእመ ፡ ኮነት ፡ ጽልእ ፡ ይፈጽምዋ ፡ በውናይ ። ወጊዜ ፡ ቀዳሚት ፡ ጉባኤ ፡ በራብዕ ፡ ሰብዔ ፡ እም፶ ፡ ወዳግሚትኒ ፡ አመ ፡ ፲ወ፪ ፡ ለጥምቀት ።

፻፳፭ ወዳግሚትሰ ፡ ዘኒቅ ፡ ፺ቱ ። ዘኒቅያ ፡ ፵ወ፩ ፡ ይትጋብኡ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ በኵሉ ፡ መካናት ፡ ኀበ ፡ ጳጳሶሙ ፡ አው ፡ ኀበ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳቲሆሙ ፡ ፪ቱ ፡ ጊዜ ፡ በኵሉ ፡ ዓመታት ። ቀዳሚ ፡ እምቅድመ ፡ ጾመ ፡ ፵ ፡ በዘየሐስስ ፡ እክየ ፡ ወቍጥዓ ፡ ወትኩን ፡ ቍርባኖሙ ፡ በጾም ፡ ቅድስት ፡ ንጽሕት ፡ ወክብርት ፡ ለእግዚአብሔር ። ወዳግሚትኒ ፡ በዘመን ፡ መጸው ፡ እምድኅረ ፡ በዓለ ፡ መስቀል ። እስመ ፡ ይበዝኅ ፡ ሕማመ ፡ ብድብድ ፡ ወሞት ፡ ግብት ፡ በዘመን ፡ ሐጋይ ፡ ወተወን ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ፍቅር ፡ ወሰላም ፡ እምቅድመ ፡ ሞት ፡ በዘይበጽሑ ፡ ኀበ ፡ እግዚእነ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በጽርየት ፡ ወንጽሕ ። ወከመ ፡ ይርአዩ ፡ በእንተ ፡ ፍትሑ ፡ ለዘአውፅኦ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ እምካህናት ፡ አው ፡ እምካልአኒሆሙ ፡ ከመ ፡ ኢይኩን ፡ ተአንትሎ ፡ አው ፡ በእንተ ፡ ግብር ፡ ዘይከውን ፡ ከመዝ ፡ ወይፍትሑ ፡ በከመ ፡ ይትከሠት ፡ ሎሙ ።

፻፳፮ ወለእመ ፡ ተዐውቀ ፡ ሕዱሂ ፡ እምኔሆሙ ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡ አእከየ ፡ ላዕለ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ለይትገሠፅ ፡ ተግሣጸ ፡ ፍጹመ ፡ ፡ ወይትከላእ ፡ እምበዊአ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ወትድምርት ፡ እምእመናን ። ወለእመ ፡ ተአበሰ ፡ ለኤጲስቆጶስ ፡ ኢያደልዎ ፡ ለዘኩ ፡ ከመ ፡ ይትገሠፅ ፡ ተግሣፀ ፡ እምነ ፡ ጉባኤ ፡ በእንተ ፡ ኃጢአት ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ተአመነ ፡ ከመ ፡ ይሥረዮ ፡ ሎቱ ፡ በእንተ ፡ ዘገብረ ፡ ቦቱ ፡ ቂመ ፡ ወመሥጠ ፡ ወሕሠመ ፡ ያግብኦ ፡ ኀበ ፡ መዓርጉ ፡ ዘቀዳሚ ። ወለእመ ፡ ተቀየመ ፡ ወተምዕዖ ፡ ወተንሥአ ፡ ላዕሌሁ ፡ ለይደቅ ፡ እምኀርጊሁ ።



ነው ። ስለነርሱም ፡ ሁለት ፡ ቃላት ፡ አሉ ።

፻፳፬ መጀመሪያዋ ፡ ረስጠብ ፡ ፳፺ ። ረስጠጅ ፡ ፳፷ ። ጳክ ፡ ፳ ። የኤጲስቆጶሳት ጉባኤ ፡ በዓመት ፡ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ ይሁን ። ስለ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያናቸው ፡ የሚሆነውን ፡ ሥራ ፡ ይነጋገሩ ። በእኩሌቶቹ ፡ ላይ ፡ ያስቸገረውን ፡ ሁሉ ፡ ትርጓሜውን ፡ ሥርዓቱን ፡ ሁሉ ፡ ይነጋገሩ ። በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ውስጥ ፡ የሚሆኑትንም ፡ መሰናክሎች ፡ ያስወግዱ ። ጠብ ክርክርም ፡ ቢሆን ፡ በዕርቅ ፡ ይፈጽሚት ። መጀመሪያዪቱ ፡ ጉባኤ ፡ በበዓለ ፡ ፶ ፡ በአራተኛው ፡ ሰባኤ ፡ ትሁን ። ሁለተኛዪቱም ፡ ጉባኤ በጥቅምት ፡ ፲፪ ፡ ቀን ፡ ትሁን ።

፻፳፭ ሁለተኛዋ ፡ ኒቅ ፡ ፺ ። ኒቅያ ፡ ፵፩ ። የየቦታው ፡ ሁሉ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ በየመቱ ፡ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ ከጳጳሳቸው ፡ ወይም ፡ ከሊቀ ፡ ጳጳሳቸው ፡ ዘንድ ፡ ይሰብሰቡ ። መጀመሪያ ፡ ከጾመ ፡ ፵ ፡ በፊት ፡ ይሁን ። ክፋንና ፡ ቍጣን ፡ በሚያርቁ ፡ ግንዘብ ፡ ቍርባናቸውም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ንጽሕት ፡ ክብርት ፡ ቅድስት ፡ ትሆን ፡ ዘንድ ። ሁለተኛውም ፡ ከበዓለ ፡ መስቀል ፡ በኋላ ፡ በመከር ፡ ወራት ፡ ይሁን ። በበጋና ፡ በበልግ ፡ ወራት ፡ ቸነፈር ፡ የድንገት ፡ ሞት ፡ ይበዛልና ፡ ከሞት ፡ አስቀድሞ ፡ ፍቅር ፡ ሰላም ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ። ወደ ፡ ጌታችን ፡ ወደ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በፍጹም ፡ ንጽሕና ፡ በሚቀርቡ ፡ ግንዘብ ። ከካህናት ፡ ወገን ፡ ወይም ፡ ከሕዝቡ ፡ ወገን ፡ ቢሆን ኤጲስቆጶሱ ፡ አውግዞ ፡ የለየውን ፡ ሰው ፡ ፍርድ ፡ ይመረምሩ ፡ ዘንድ ፡ ቸልታ ፡ እንዳይሆን ፡ ወይም ፡ ይህን ፡ በሚመስል ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ተገለጠላቸው ፡ ይፈርዱ ፡ ዘንድ ።

፻፳፮ ከነዚህ ፡ አንዱ ፡ ስንኳ ፡ በኤጲስቆጶሱ ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ እንደ ሠራ ፡ ቢታወቅ ፡ ፍጹም ፡ ቅጣት ፡ ይቀጣ ። ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ከመግባት ፡ ከምእመናንም ፡ ጋራ ፡ ከመገናኘት ፡ ይከልከል ። ለኤጲስቆጶሱ ፡ ከታዘዘም ፡ ስለሠራው ፡ ኃጢአት ፡ በጉባኤ ፡ ፍጹም ፡ ቅጣት ፡ ሊቀጣ ፡ አይገባውም ። ስላስቀየመው ፡ ስላስቆጣው ፡ ስላስከፋው ፡ ይቅር ፡ ይሉት ፡ ዘንድ ፡ በደሉን ፡ አምኖአልና ፡ ወደቀደመ ፡ ማዕርጉ ፡ ይመልሱት ። ተቀይሞ ፡ ተቆጥቶ ፡ በርሱ ፡ ላይ ፡ ቢበረታበት ፡ ከማዕርጉ ፡ ይዋረድ ።

አንቀጽ ፡ ፩ ።

፻፳፯ ድስት ፡ ፴ ፡ እመቦ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ዘተጸውዐ ፡ ኀበ ፡ ዘንቱ ፡ ጉባኤ ፡ ኢያስተቃልል ፡ ለበጺሕ ፡ ወኢይደንግር ፡ ዘእንበለ ፡ ለእመ ፡ ተጸደቀ ፡ ተመክንዮት ፡ ሰጠቅ ፡ ወይጽሐፍ ፡ መልእክተ ፡ እንዘ ፡ ይነግር ፡ ተመክንዮቶ ፡ ወይንግእ ፡ መበ ሕተ ።

፻፳፰ ዘኒቅያ ፡ ወእምከመ ፡ ተጋብኡ ፡ ኀበ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳቲሆሙ ፡ በእንተ ፡ ግብር ፡ ዘይደሉ ፡ ከመ ፡ ይስአልዎ ፡ በእንቲአሃ ፡ ወይፍልዋ ፡ ለኵሙ ፡ ፍትሐ ፡ ዚአሁ ፡ ወኢይክሥቱ ፡ ምሥጢሮሙ ፡ ዘእንበለ ፡ ዘይትፌቀድ ፡ ኀቤሁ ፡ ለከሢተ ፡ ዝንቱ ፡ በእንተ ፡ ብዝኀ ፡ እእምሮቱ ፡ ወሃይማኖቱ ፡ ወኢይቱም ፡ ፩ዱ ፡ ቅሩበ ፡ ኀቤሆሙ ፡ ዘእንበለ ፡ ማእምራን ፡ ወይንብሩ ፡ ማእከለ ፡ ምርፋቆሙ ፡ ፩ደ ፡ መንበረ ፡ ወይንብርዎ ፡ ዲቤሁ ፡ ለወንጌል ፡ ቅዱስ ፡ ወይንበር ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ በቅድሜሆሙ ፡ ወይሰጽዉ ፡ አፍቅጾ ፡ ወይትንሥኡ ፡ ኅቡረ ፡ ወይጸልዩ ፡ ወይግብኡ ፡ ኀበ ፡ ምርፋቆሙ ፡ ወይሕትቱ ፡ በእንተ ፡ ግብር ፡ ዘተጋብኡ ፡ በእንቲአሁ ፡ በኅቡእ ። ወሶበ ፡ ፈጸሙ ፡ ፍትሐ ፡ በተማህሎ ፡ ወፈትሖ ፡ ላዕለ ፡ ዘይደሉ ፡ ላዕሌሁ ፡ ዘንተ ፡ በከመ ፡ ይፈቅድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይክሥትዎ ፡ አንከ ።

፻፳፱ ሳድስ ፡ ረስጠጅ ፡ ዘ፸ወ፩ዱ ፡ ዘኒቅያ ፡ ፶ወ፪ቱ ፡ ጸክ ፡ ዘ፰ወ፫ቱ ፡ ኢያወርሱ ፡ ኤጲስቆጶስና ፡ ወኢታብውሕ ፡ ትእዛዝ ፡ በእንቲአሃ ፡ እስመ ፡ አምላካዊት ፡ ይእቲ ፡ ኢ ፡ ለዘመድ ፡ ወኢ ፡ ለነኪር ፡ ወለከህነትኒ ፡ ከማሁ ።

፻፴ ሳብዕ ፡ ዘኒቅያ ፡ ዘ፶ወ፩ቱ ፡ ኢይሠየሙ ፡ ፪ቱ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ላዕለ ፡ አሐቲ ፡ ሀገር ፡ ወለእመ ፡ ይትጋአዙ ፡ ሰብአ ፡ ሀገር ፡ አው ፡ አህጉር ፡ እስከ ፡ ይትከፈሉ ፡ ኀበ ፡ ፪ቱ ፡ ክፍል ፡ ወበ ዛቲ ፡ ምክንያት ፡ ተሠይመ ፡ ካልእ ፡ ኤጲስ ቆጶስ ፡ ለይሕትቱ ፡ ጥዩቀ ፡ በእንተ ፡ ዝንቱ ። ወለእመኒ ፡ ኢረከቡ ፡ ላዕለ ፡ ቀዳማዊ ፡ ኤጲስ ቆጶስ ፡ ዘይደሉ ፡ ለሎተ፡ቱ ፡ ለይንበር ፡ በመ ካኑ ፡ ወእመሰ ፡ ረከቡ ፡ በላዕሌሁ ፡ ለይሚጦ ፡ በመካኑ ፡ ዚአሁ ፡ ዘእልቦ ፡ ነውር ፡ ውስቴቱ ፡ ወለዝንቱ ፡ ያውግዝዎ ።

፻፴፩ ሥቅ ፡ ዘ፶ወ፯ቱ ፡ ኢይደሉ ፡ ከመ ፡ ይኩኑ ፡ ፪ቱ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ውስተ ፡ አሐቲ ፡ ሀገር ፡ እላ ፡ አብሮቆሮስ ፡ ወውእቱ ፡ ቆሞስ ፡ መትልዉ ፡

ስለ ፡ ኤጲስቆጶሳት ።

፻፳፯ ድስቅ ፡ ፴ ። ወደዚህ ፡ ጉባኤ ፡ የተጠራ ፡ ኤጲስ ቆጶስ ፡ ቢኖር ፡ አልመጣም ፡ አይበል ። የታ ወቀ ፡ ምክንያት ፡ ካላገኘው ፡ በቀር ፡ ወደኋላ ፡ አይቅር ። የቀረበትንም ፡ ምክንያት ፡ ይጻፍ ። ፈቃዱም ፡ ይቀበል ።

፻፳፰ ኒቅያ ። ስለሚገባው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ የተሰበሰቡ በትን ፡ ሥራ ፡ ይጠይቁት ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳታቸው ፡ ከተሰበሰቡ ፡ በኋላ ፡ ፍርዱን ፡ ይሰይላቸው ። ስለ ፡ እእምሮው ፡ ጽናት ፡ ስለሃ ይማኖቱም ፡ ምሥጢር ፡ ሊገልጹለት ፡ ለሚ ገባው ፡ ሰው ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ለማይገባው ፡ ምሥ ጢራቸውን ፡ አይግለጡ ። ከአዋቂዎች ፡ በቀር፡ አንዱ ፡ ስንኳ ፡ ወደነርሱ ፡ ቀርቦ ፡ አይቁም ። በመቀመጫቸውም ፡ መካከል ፡ አንድ ፡ ወን በር ፡ ያኑሩ ። ቅዱስ ፡ ወንጌልንም ፡ በርሱ ፡ ላይ ፡ ያስቀምጡት ። ሊቀ ፡ ጳጳሳቱም ፡ በፊታ ቸው ፡ ይቀመጥ ። በሩን ፡ ይዝጉ ። በአንድነት ፡ ተነሥተውም ፡ ይጸልዩ ። በየመቀመጫቸውም፡ ይቀመጡ ። የተሰበሰቡበትንም ፡ ሥራ ፡ በም ሥጢር ፡ (በቆይታ) ፡ ይመርምሩ ። በርኅራኄ ፡ ፍርዱን ፡ በፈጸሙ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ እን ደሚወደው ፡ የሚገባውን ፡ በርሱ ፡ ላይ ፡ ከፈ ረዱ ፡ በኋላ ፡ እንግዲህ ፡ ይግለጹለት ።

፻፳፱ ስድስተኛ ፡ ረስጠጅ ፡ ፸፩ ። ኒቅያ ፡ ፶፪ ። ጸክ ፡ ፹፫፡ ኤጲስቆጶስነትን ፡ ለሌላ ፡ አያውርሱ ። ሕግ ፡ ስለርሷ ፡ አታዝዝም ፡ የአምላክ ፡ ገንዘብ ፡ ናትና ። ለዘመድም ፡ ለባዕድም ፡ ቢሆን ። ክህነትንም ፡ እንደዚሁ ፡ አያውርሱ ።

፻፴ ሰባተኛ ። ኒቅያ ፡ ፶፩ ። በአንዲት ፡ አገር ፡ ሁለት ኤጲስቆጶሳት ፡ አይሾሙ ። የከተማና ፡ የገጠር ፡ ሰዎች ፡ ከሁለት ፡ እስከ ፡ መከፈል ፡ ደርሰው ፡ ቢጣሉ ፡ በዚህም ፡ ምክንያት ፡ ሌላ ፡ ኤጲስቆ ጶስ ፡ ቢሾም ፡ ስለዚህ ፡ ፈጽመው ፡ ይመርምሩ ። በፊተኛው ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ላይ ፡ የሚያሽር ፡ ነውር ፡ ካላገኙበት ፡ በቦታው ፡ ይቀመጥ ። በርሱ ፡ ላይ ፡ ቢያገኙበት ፡ ግን ፡ ነውር ፡ የሌለ በትን ፡ ይሹሙ ። እርሱን ፡ ግን ፡ ይለዩት ።

፻፴፩ ሥቅ ፡ ፶፯ ። በአንዲት ፡ አገር ፡ ውስጥ ፡ ሁለት ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ሊሾሙ ፡ አይገባም ። አብሮቆሮስ፡ ይኸውም ፡ የኤጲስቆጶሱ ፡ ምክትል ፡ የሚሆን ፡

ስኤጲስቆጶስ ። ወለእመ ፡ ሀለወ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ውስተ ፡ ሀገር ፡ ኢይግበር ፡ ምንተኒ ፡ ቆሞስ ፡ ዘእንበለ ፡ ምክረ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ዘሀገር ፡ አው ፡ ዘብሔር ።

፻፸፱ ሳምን ፡ ይነግር ፡ በእንተ ፡ ተመክንዮታት ፡ እንተ ፡ ሰበ ፡ ትትዐወቅ ፡ እሐቲ ፡ እምኔሆን፡ በላዕለ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ይወድቅ ፡ እመዓርጊሁ ፡ ወይትመተር ፡ እምሢመቱ ፡ ወኍልቆን ፡ በውስተ ፡ ዝንቱ ፡ አንቀጽ ፡ ፳ወ፰ቱ ፡ ተመክንዮታት ።

፻፹ ቀዳሚት ፡ ወዳግሚት ፡ ሣልሲት ፡ ወራብዒት ፡ ዘይነሥእ ፡ ለኤጲስቆጶስና ፡ በሕልያን ፡ አው ፡ በተኀይሎ ፡ አው ፡ በተመይኖ ፡ እው ፡ ዘይሁብ ፡ ኪያሃ ፡ በሕልያን ።

፻፹፩ ረስጠብ ፡ ፳ ። ኒቅያ ፡ ፶ወ፫ቱ ፡ በስ ፡ ፺ወ፰ቱ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ አው ፡ ቀሲስ ፡ አው ፡ ዲያቆን ፡ ዘይነሥእ ፡ ለዛቲ ፡ መዓርግ ፡ በሕልያን ፡ ይትመተር ። ወዘሤሞሂ ፡ ይትመተር ፡ ወኢይሳተፍዎ ፡ ማሙራ ፡ በከመ ፡ ተገብረ ፡ በሲሞን ፡ መሠርይ ፡ እምኀቤየ ፡ እነ ፡ ጴጥሮስ ።

፻፹፪ ረስጠብ ፡ ፳ወ፩ዱ ፡ ወለእመ ፡ ተራድአ ፡ በመኳንንተ ፡ ዝንቱ ፡ ዓለም ፡ ወተሠይመ ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እምኀቤሆሙ ፡ ይትመተር ፡ ወይሰደድ ፡ ውእቱኒ ፡ ወኵሎሙ ፡ አለ ፡ ተሳተፍዎ ።

፻፹፫ ረስጠጅ ፡ ፳ወ፰ቱ ፡ እው ፡ ዘአስፈወ ፡ ከመ ፡ የሀብ ፡ ሕልያን ፡ እስከ ፡ ይሠየም ፡ በጕሕሉት ፡ ኢይትወከፉ ፡ ሢመቶ ፡ ወእመኒ ፡ ሞአ ፡ በእንቲአሃ ፡ በጕሕሉት ፡ ምትር ፡ ውእቱ ፡ ወይኩን ፡ በኀቤክሙ ፡ በአምሳለ ፡ አረማዊ ፡ ወይሰደድ ፡ እምቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ለእግዚአብሔር ። ወይትገኀሡ ፡ እምተናግሮቱ ፡ ወእምትድምርቱ ፡ በከመ ፡ ተግኅሥኩ ፡ እነ ፡ ጴጥሮስ ፡ አምትድምርተ ፡ ሲሞን ፡ መሠርይ ፡ ወሰደድክዎ ፡ እምቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ በትእዛዘ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ።

፻፹፬ በስ ፡ ፺ወ፯ቱ ፡ እመቦ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ዘይነሥእ ፡ ንዋየ ፡ እምነ ፡ ፩ዱ ፡ ዘይሠይሞ ፡ እንዘ ፡ ኢኮነ ፡ ድልወ ፡ ይትወገዝ ፡ ወለዝንቱ ፡ ሲሞን ፡ መሠርይ ፡ ዘዘከርዎ ፡ ሐዋርያት ፡ በቀኖናሆሙ ፡ ውእቱ ፡ ዘዘከሮ ፡ ሉቃስ ፡ በመጽሐፈ ፡ አብረ ክሲስ ፡ ወይቤ ፡ ወሶበ ፡ ርእየ ፡ ሲሞን ፡ ከመ ፡ በአንብሮ ፡ እደዊሆሙ ፡ ለሐዋርያት ፡ ይወ



ቆሞስ ፡ ነው ፡ ቆሞሱ ፡ ይሁን ፡ እንጂ ። ኤጲስቆጶሱ ፡ በአገር ፡ ያለ ፡ እንደሆነ ፡ ቆሞሱ ፡ ያለ ፡ ኤጲስቆጶሱ ፡ ፈቃድ ፡ በከተማ ፡ ወይም ፡ በገጠር ፡ ምንም ፡ አይሥራ ።

፻፸፱ ስምንተኛው ፡ ከነውር ፡ ወገን ፡ አንዲቱ ፡ ነውር በኤጲስቆጶስ ፡ ላይ ፡ ብትታወቅበት ፡ ከመዓርጉ ፡ የሚዋረድበትን ፡ ከሹመቱ ፡ የሚሻርበትን ፡ ምክንያት ፡ ይናገራል ። በዚህም ፡ አንቀጽ ፡ ውስጥ ፡ ቍጥራቸው ፡ ፳፰ ፡ ምክንያቶች፡ ናቸው ።

፻፹ መጀመሪያዋና ፡ ሁለተኛዋ ፡ ሦስተኛዋና ፡ አራተኛዋ ፡ ኤጲስቆጶስነትን ፡ በማማለጃ ፡ በጉልበት ፡ በተንኰል ፡ ስለ ፡ ተሾመው ፡ ወይም ፡ ማማለጃ ፡ ተቀብሎ ፡ ስለሾመው ፡ ነው ።

፻፹፩ ረስጠብ ፡ ፳ ። ኒቅያ ፡ ፶፫ ። በስ ፡ ፺፰ ። ይህችን ፡ ማዕርግ ፡ በማማለጃ ፡ የተሾመ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ወይም ፡ ቄስ ፡ ወይም ፡ ዲያቆን ፡ ይሻር ። የሾመውም ፡ ይሻር ። በእኔ ፡ በጴጥሮስ ፡ ዘንድ ፡ በመሠርዩ ፡ በሲሞን ፡ ላይ ፡ እንደተደረገው ፡ ፈጽመው ፡ አይገናኙት ።

፻፹፪ ረስጠብ ፡ ፳፩ ። በዚህ ፡ ዓለም ፡ መኳንንት ፡ ቢረዳ ፡ ከነርሱም ፡ ዘንድ ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ቢሾም ፡ ይሻር ። እርሱና ፡ ግብረ ፡ አበሮቹ ፡ ሁሉ ፡ ይለዩ ።

፻፹፫ ረስጠጅ ፡ ፳፰ ። ወይም ፡ እስኪሾም ፡ ድረስ ፡ መማለጃ ፡ እሰጣለሁ ፡ ብሎ ፡ የተሾመ ፡ ሹመቱን ፡ አይቀበሉት ። በተንኰል ፡ ቢያሸንፍም ፡ የተለየ ፡ ነው ። በእናንተም ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ አረማዊ ፡ ይሁን ። ከእግዚአብሔር ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንም ፡ ይለይ ። ከርሱ ፡ ጋር ፡ ከመነጋገርና ፡ ከመገናኘት ፡ ይራቁ ። እኔ ፡ ጴጥሮስ ፡ ከሲሞን ፡ መሠርይ ፡ ጋር ፡ ከመገናኘት ፡ እንደራቅሁ ። በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ትእዛዝ ፡ ከእግዚአብሔር ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እንደ ፡ ለየሁት ።

፻፹፬ በስ ፡ ፺፯ ። ሳይገባው ፡ ገንዘብ ፡ ተቀብሎ ፡ የሚሾም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ቢኖር ፡ ይለይ ። ሐዋርያት ፡ በመጽሐፋቸው ፡ የጻፉት ፡ ሉቃስም ፡ በግብረ ፡ ሐዋርያት ፡ የጻፈው ፡ ሲሞን ፡ መሠርይ ፡ ነው ። (የሐዋ ፡ ሥራ ፡ ፰ ፡ ፲፰ - ፲፱) ። ሲሞን ፡ ሐዋርያት ፡ እጃቸውን በጫኑበት ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሲወርድበት ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ መን

ርድ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ እምጽአ ፡ ሎሙ ፡ ንዋየ ፡ እንዘ ፡ ይብል ፡ ሀቡኒ ፡ ሊተኒ ፡ ዘንተ ፡ ሥልጣነ ፡ ከመ ፡ ሰበ ፡ አንበርኩ ፡ እደውየ ፡ ይረድ ፡ ላዕሌሁ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ። ወይቤሎ ፡ ስምዖን ፡ ብሩርከ ፡ ትሑር ፡ ምስሌከ ፡ ውስተ ፡ ኀጕል ፡ በእንተ ፡ ዘሐሰብከ ፡ አንተ ፡ ከመ ፡ ሀብተ ፡ እግዚአብሔር ፡ በረብሕ ፡ ዓለም ፡ ትጠረይ ፡ አልብከ ፡ ክፍል ፡ ወኢርስት ፡ ውስተ ፡ ዝንቱ ፡ ሃይማኖት ። እስመ ፡ ልብከ ፡ ኢኮነ ፡ ርቱዐ ፡ ቅድመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዳእሙ ፡ ተመየጥ ፡ እምዝንቱ ፡ እኪትከ ፡ ወስአል ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከመ ፡ ይሥረይ ፡ ለከ ፡ ውእቱ ፡ እከየ ፡ ልብከ ።

፪፻፷፭ ኃምስ ፡ ረስጠጅ ፡ ፳ወ፱ቱ ፡ እመቦ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ዘተማኅፀነ ፡ በእንተ ፡ ምግብናሁ ፡ ለሰብእ ፡ እፍኣ ፡ አው ፡ በመኳንንተ ፡ ዓለም ፡ ከመ ፡ ይርድእዎ ፡ በእንተ ፡ ሥርዓተ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እንዘ ፡ የኀሥሥ ፡ በዝንቱ ፡ አኀስሮቶሙ ፡ ለሕዝበ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወከመ ፡ ይትዐበይ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ በዘኢይደሉ ፡ አው ፡ ከመ ፡ ይማዕ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ካልእ ፡ ውጉዝ ፡ ውእቱ ፡ ወምቱር ፡ ወዘሎሙ ፡ እለ ፡ ይትራድእዎ ፡ በዝንቱ ፡ ግብር ።

፪፻፷፮ ሳድስ ፡ በስ ፡ ዘ፲ወ፰ቱ ፡ እመቦ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ዘይነሥእ ፡ ሕልያነ ፡ እምቀሳውስት ፡ ወዲያቆናት ፡ ወየኀድጎሙ ፡ ኀበ ፡ መዓርጊሆሙ ፡ እንዘ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ ፍትሕ ፡ ለይዓእ ።

፪፻፷፯ ሳብዕ ፡ ጽክ ፡ ዘ፲ወ፯ቱ ፡ እመቦ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ አው ፡ ጳጳስ ፡ አው ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ እስመ ፡ በእንቲአሆሙ ፡ ኢሐተ ፡ ፍኖት ፡ ዘአበየ ፡ እምቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እምድኅረ ፡ ሢመቱ ፡ ወተወክፎቱ ፡ እሎንተ ፡ መዓርጋተ ፡ ወለእመኒ ፡ ኢሐደ ፡ ዕለተ ፡ አው ፡ ኢሐተ ፡ ሰዓተ ፡ ወእምዝ ፡ ጎየ ፡ እምውእቱ ፡ መንበር ፡ ይትወቀሥ ፡ እምሰብአ ፡ ሀገሩ ፡ እስከ ፡ አሆ ፡ ይቤ ፡ ወይትመየጥ ፡ ኀበ ፡ መንበሩ ፡ ወእመ ፡ አኮ ፡ ይስደድ ፡ እምኔ ፡ መካን ፡ ዘፈተወ ፡ ይንበር ፡ ውስቴቱ ፡ ወእምተደምሮ ፡ ጉባኤ ። ወእመ ፡ ኢተመይጠ ፡ ድኅረ ፡ ስእልዎ ፡ ሰብአ ፡ ሀገሩ ፡ ኀርየት ፡ ሎሙ ፡ እመ ፡ ፈቀዱ ፡ ያንብርዎ ፡ ኀቤሆሙ ፡ ወይዝክሩ ፡ ስሞ ። ወለእመሰ ፡ ጸልእዎ ፡ ኢይዝክሩ ፡ ስሞ ፡ እስመ ፡ ይደሉ ፡ ይጸልዩ ፡ ላዕሌሁ ፡ በከመ ፡ ውእቱ ፡ ጸለየ ፡ ላዕሌሆሙ ።

ፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ያድርበት ፡ ዘንድ ፡ ይህን ፡ ሥልጣን ፡ ስጡኝ ፡ ብሎ ፡ ገንዘብ ፡ አመጣላቸው ። ስምዖንም ፡ አለው ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ጥቅም ፡ ሀብተ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ገንዘብ ፡ ታደርግ ፡ ዘንድ ፡ ስላሰብህ ፡ ብርህ ፡ ካንተ ፡ ጋር ፡ ለጥፋትህ ፡ ትሁን ። በዚህ ፡ ሃይማኖት ፡ ውስጥ ፡ ዕድል ፡ ፈንታ ፡ ርስትም ፡ የለህም ። ልብህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የቀና ፡ አይደለምና ፡ ከዚህ ፡ ክፋትህ ፡ ተመለስ ፡ እንጂ ፡ እርሱ ፡ የልብህን ፡ ክፋት ፡ ያስተሠርይልህ ፡ ዘንድ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለምን ።

፪፻፷፭ አምስተኛ ። ረስጠጅ ፡ ፳፱ ። እሾምሃለሁ ፡ ብሎ ፡ ከውጭ ፡ ሰዎች ፡ ጋር ፡ ወይም ፡ ከዓለም ፡ መኳንንት ፡ ጋር ፡ ስለቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሹመት ፡ ይረዱት ፡ ዘንድ ፡ የተማፀነ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ቢኖር ፡ በዚህ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሕዝብ ፡ ሊያዋርድ ፡ በማይገባ ፡ በላያቸው ፡ ሊታበይ ፡ ወይም ፡ የባልንጀራውን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሊወስድ ፡ ፈልጎ ፡ የተማፀነ ፡ ቢኖር ፡ ፈጽሞ ፡ የተወገዘ ፡ ነው ። በዚህ ፡ ሥራ ፡ የሚረዱትም ፡ ሁሉ ፡ ፈጽመው ፡ የተወገዙ ፡ ናቸው ።

፪፻፷፮ ስድስተኛ ። በስ ፡ ፲፰ ። ከቀሳውስትና ፡ ከዲያቆናት ፡ መማለጃ ፡ ተቀብሎ ፡ ፍርድ ፡ እያለባቸው ፡ በመዓርጋቸው ፡ የሚተዋቸው ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ቢኖር ፡ ይሻር ።

፪፻፷፯ ሰባተኛ ፡ ጽክ ፡ ፲፯ ። ሊቀ ፡ ጳጳሳት ፡ ወይም ፡ ጳጳስ ፡ ወይም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ቢሆን ፡ ስለነርሱ ፡ ሕግ ፡ አንዲት ፡ ፍትና ፡ ከተሾመና ፡ እነዚህን ፡ መዓርጋት ፡ ከተቀበለ ፡ በኋላ ፡ አንዲት ፡ ዕለት ፡ ወይም ፡ አንዲት ፡ ሰዓትም ፡ ቢሆን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡ ያላገለገለ ፡ ቀጥሎም ፡ የተሾመበትን ፡ አገር ፡ ጥሎ ፡ የሸሸ ፡ ቢኖር ፡ እሺ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ ቦታው ፡ እስኪመለስ ፡ ድረስ ፡ የአገሩ ፡ ሰዎች ፡ ይማልዱት ። አልመለስም ፡ ቢል ፡ ሊኖር ፡ ከሄደበት ፡ አገርና ፡ ከምእመናን ፡ ጉባኤ ፡ ይለይ ። የአገሩ ፡ ሰዎች ፡ ከለመኑት ፡ በኋላ ፡ ባይመለስ ፡ በእነርሱ ፡ ዘንድ ፡ እንዲኖር ፡ ስሙንም ፡ ሊጠሩት ፡ ቢወዱ ፡ ምርጫ ፡ አላቸው ። ቢጠሉት ፡ ግን ፡ ስሙን ፡ አይጥሩ ። እርሱ ፡ ለነርሱ ፡ እንደ ፡ ጸለየ ፡ እነርሱም ፡ ይጸልዩበት ፡ ዘንድ ፡ ይገባልና ።

፻፹፩ ሳምን ፡ ወታስዕ ፡ ረስጠብ ፡ ዘዓወዲቱ ፡ እመቦ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ አው ፡ ቀሲስ ፡ አው ፡ ዲያቆን ፡ ዘተሠይመ ፡ ፪ተ ፡ ጊዜ ፡ ይትመተር ፡ ውእቱኒ ፡ ወዘሤሞ ። እላ ፡ ለእመ ፡ አያቀ ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡ ዘተሠይመ ፡ እምኀበ ፡ ሐራ ፡ ጥቃ ። ረስጠ፰ ፡ ዘ፸ወ፪ቱ ፡ ወከማሁ ፡ ለእመ ፡ አውሰበ ፡ ፪ተ ፡ አንስተ ፡ እምቅድመ ፡ ሢመቱ ፡ ወተሠይመ ፡ ይትመተር ፡ ውእቱኒ ፡ ወዘሤሞ ፡ እላ ፡ ባሕቲቱ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ ውእቱ ፡ ዘኢይአምር ፡ ግብሩ ፡ ይትመተር ፡ ውእቱ ፡ ባሕቲቱ ።

፻፹፪ ዓሥር ፡ ዘኒቅያ ፡ ፴ወ፰ቱ ፡ እመቦ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ዘኮነ ፡ ተቀያሚ ፡ ፈድፋደ ፡ አው ፡ ዘያፈጥን ፡ ቀኖና ፡ እስከ ፡ ውእቱ ፡ የአምር ፡ ወያወግዝ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ፡ ወኢየኀድግ ፡ ዘንተ ፡ ወዘየፈቅር ፡ ክብረ ፡ ወኢየኀድግ ፡ ቂመ ፡ ከመ ፡ ያፍጥን ፡ ግዝተ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ፡ ይደቅ ፡ እመዓርጊሁ ፡ ወከማሁ ፡ ኵሎሙ ፡ እለ ፡ ይመስልዎ ፡ ይኩኑ ፡ ውጉዛነ ።

፻፹፫ ድስቅ ፡ ዘ፲ቱ ፡ ወኤጲስቆጶስ ፡ ዘድልው ፡ ለፍትሕ ፡ እመ ፡ ፈትሐ ፡ በዐመፃ ፡ ላዕለ ፡ ፩ዱሂ ፡ እስመ ፡ ፍትሕ ፡ ዘይወፅእ ፡ እምእፉሁ ፡ ላዕለ ፡ ነፍሱ ፡ ውእቱ ።

፻፹፬ ረስጠብ ፡ ዘ፷ወ፱ቱ ፡ ወይኩን ፡ ሊቅ ፡ ዘይኄሥዮሙ ፡ ለሕዝብ ፡ ወየአስሮሙ ፡ በመስቀል ፡ አኮ ፡ በግዘት ፡ ኢየአምር ፡ ወኢየውግዝ ፡ ዘእንበለ ፡ ርትዕ ። ወለእመሰ ፡ ውእቱ ፡ እሠረ ፡ ወአውገዘ ፡ ዘእንበለ ፡ ርትዕ ፡ እንዘ ፡ የኀሥሥ ፡ ከመ ፡ ያተክዞሙ ፡ ለሰብእ ፡ ወይፈቅድ ፡ ስሕተቶሙ ፡ ወተጋንዮቶሙ ፡ ሎቱ ፡ ይኩን ፡ ውእቱ ፡ እሡረ ፡ ወውጉዘ ፡ እምኀበ ፡ እግዚአብሔር ። ወይቁሙ ፡ ላዕሌሁ ፡ ካህናቲሁ ፡ በጽድቅ ፡ ዘይደሉ ።

፻፹፭ ወለእመ ፡ ጸንዐ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ ግብሩ ፡ ያጠይቁ ፡ ግብሮ ፡ ኀበ ፡ ጳጳስ ፡ አው ፡ ኀበ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳቲሁ ፡ ወይትነሥኡ ፡ ላዕሌሁ ፡ በጽድቅ ፡ ወኢይኅድግዎ ፡ ይትበየዉ ፡ ኀበ ፡ አባግዐ ፡ ክርስቶስ ፡ ዘተሣየጠሙ ፡ በደሙ ፡ ወኢያስተቀኑዎሙ ፡ ወኢያብጽሖሙ ፡ ኀበ ፡ ዕረፍት ፡ ላዕለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወከሃዲ ፡ ሕጉ ፡ ቅድስት ። ወኢይኅድግዎ ፡ ይንበር ፡ ላዕለ ፡ ፍትሕ ፡ ወኢየአግዝ ፡ በሢመቱ ፡ ወይኩን ፡ መሃይምነ ፡ እንዘ ፡ ይትዌከፍ ፡ ግፍዐ ፡ በሠናይ ፡ ከመ ፡ ዘይደሉ ፡ ላዕሌሁ ።



፻፹፩ ስምንተኛና ፡ ዘጠኛኛ ። ረስጠብ ፡ ፹፪ ። ሁለት ፡ ጊዜ ፡ የተሾመ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ወይም ፡ ቄስ ፡ ወይም ፡ ዲያቆን ፡ ቢኖር ፡ ይሻር ፡ ሿሚውም ፡ ይሻር ። ከሐራ ፡ ጥቃ ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ተሾመ ፡ ቢያስረዳ ፡ ግን ፡ አይሻርም ። ረስጠጅ ፡ ፸፪ ። እንደዚሁም ፡ ከሹመቱ ፡ በፊት ፡ ሁለት ፡ ሚስት ፡ አግብቶ ፡ የተሾመ ፡ ቢኖር ፡ እርሱም ፡ ሿሚውም ፡ ይሻር ። ሥራው ፡ የታወቀ ፡ ቢሆን ፡ ግን ፡ እርሱ ፡ ብቻ ፡ ይሻር ።

፻፹፪ አሥረኛ ፡ ኒቅያ ፡ ፴፰ ። ፈጽሞ ፡ ቂመኛ ፡ የሆነ ፡ ወይም ፡ በየጊዜው ፡ ሁሉን ፡ እስከ ፡ ማሠርና ፡ እስከ ፡ ማውገዝ ፡ ድረስ ፡ ፈጣኝ ፡ የሚቆጣ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ቢኖር ፡ ይህን ፡ ባይተው ፡ ክብርን ፡ የሚወድ ፡ ሁልጊዜ ፡ ፈጥኖ ፡ ለማውገዝ ፡ ቂሙን ፡ የማይረሳ ፡ ቢሆን ፡ ከሹመቱ ፡ ይሻር ። እርሱንም ፡ የሚመስሉት ፡ ሁሉ ፡ የተለዩ ፡ ይሁኑ ።

፻፹፫ ድስቅ ፡ ፲ ። ለፍርድ ፡ የተዘጋጀ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ በአንዱ ፡ ላይ ፡ ስንኳ ፡ በሐሰት ፡ ቢፈርድ ፡ በፈረደው ፡ ፍርድ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ይፈረድበታል ።

፻፹፬ ረስጠብ ፡ ፷፱ ። አለቃው ፡ ሕዝቡን ፡ የሚመክራቸው ፡ በውግዘት ፡ ያይደለ ፡ በመስቀል ፡ የሚያሥራቸው ፡ ይሁን ። በማይገባ ፡ እያውግዝ ። ሰዎችን ፡ ሊያሳዝናቸውና ፡ ፈርተው ፡ እንዲገዙለት ፡ ፈልጎ ፡ በማይገባ ፡ ቢያሥር ፡ ቢያወግዝ ፡ እርሱ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ የታሠረ ፡ የተወገዘ ፡ ይሁን ። ካህናትም ፡ በእውነት ፡ ይቃወሙት ።

፻፹፭ ግብሩ ፡ ቢጸናባቸው ፡ ግብሩን ፡ ወደ ፡ ጳጳሱ ፡ ወይም ፡ ወደ ፡ ሊቀ ፡ ጳጳሳቱ ፡ አቅርበው ፡ ያስረዱ ። በእውነት ፡ ይነሡበት ። ክርስቶስ ፡ በደሙ ፡ የዋጃቸውን ፡ ምእመናንን ፡ ይበድሳቸው ፡ ዘንድ ፡ አይተውት ። አያስቈጣቸው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ወደ ፡ መሳደብና ፡ ቅድስት ፡ ሕጉን ፡ ወደ ፡ መካድ ፡ እያደረሳቸው ። በሹመቱ ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ አይተዉት ። በሹመትም ፡ አይዘዝ ። ለርሱ ፡ እንደሚገባው ፡ በደሉን ፡ ተቀብሎ ፡ በሚገባ ፡ መሃይምን ፡ ይሁን ።

፪፻፹፮ ወይኩን ፡ ውእቱ ፡ ዘይትነሠሥ ፡ እግዚአብሔር፡ በግፍዐ ፡ ዚአሁ ። ወኢይኅድግዎ ፡ ሰብእ ፡ ፈታሕያን ከመ ፡ ይትመየጥ ፡ ኀበ ፡ ስሕተቱ ። ወሕዝብኒ ፡ ይኩኑ ፡ ተወካፍያነ ፡ አበሳሁ ፡ ለሠንዮቱ ፡ በከመ ፡ ግብር ፡ ዘድልው ፡ ሎቱ ፡ ውእቱኒ ፡ ይኩን ፡ አስተብቋዔ ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእንተ ፡ አበሳሁ ።

፪፻፹፯ ዓሥር ፡ ወ፩ዱ ፡ ረስጠጅ ፡ ዘ፶ወ፪ቱ ፡ ረስጠብ ፡ ፶ወ፩ ፡ ረስጠብ ፡ ዘ፰ወ፯ቱ ፡ ዘ፹ወ፰ቱ ፡ ኤጲስ ቆጶስ ፡ አው ፡ ቀሲስ ፡ አው ፡ ዲያቆን ፡ ዘይትህ ከይ ፡ እምትምህርተ ፡ ካህናቲሁ ፡ ወሕዝቡ ፡ ወተልእኮተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወፈሪሆቱ ፡ ይት ፈለጥ ፡ ወእመ ፡ አዝለፈ ፡ ነቢረ ፡ በሀኬቱ ፡ ይትመተር ።

፪፻፹፰ ጅ ፡ ፮ቱ ፡ ወከመዝ ፡ እግዚእነ ፡ አቅደመ ፡ ከመ፡ ይግበር ፡ ወይምህር ፡ ሉቃስ ፡ ይቤ ፡ እስመ ፡ ኩሎሙ ፡ ሐዋርያት ፡ ኮኑ ፡ ይፀመዱ ፡ ኵሎ ፡ ዕለተ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ወምኵራብ ፡ በእንተ ፡ ትምህርት ፡ ወበከመ ፡ አዘዘ ፡ ጳው ሎስ ፡ ለረድኡ ፡ ከመ ፡ ያዝልፍ ፡ በእንተ ፡ ትምህርት ።

፪፻፹፱ ዓሥር ፡ ወክልኤ ፡ ረስጠብ ፡ ፶ወ፱ቱ ፡ ረስጠብ ፡ ፵ ፡ እመቦ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ አው ፡ ቀሲስ ፡ ዘይት ኄየዮሙ ፡ ለካህናት ፡ ወለነዳያን ፡ ወኢይሁ ቦሙ ፡ በዘይትከሀሎ ፡ ይትፈለጥ ፡ ወለእመ ፡ አዝለፈ ፡ በተነይዮቱ ፡ ይትመተር ፡ ከመ ፡ ቀታሌ ፡ እኑሁ ።

፪፻፺ ዓሥር ፡ ወሣልስ ፡ ረስጠብ ፡ ፴ወ፰ቱ ፡ ረስጠጅ፡ ፵ወ፪ቱ ፡ እመቦ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ አው ፡ ቀሲስ ፡ ዘኢይትዌከፎ ፡ ለኀጥእ ፡ ሶበ ፡ ነስሐ ፡ ይትመ ተር ፡ እስመ ፡ ውእቱ ተሀየደ ፡ ዘይቤ ፡ እግዚ እነ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ይከውን ፡ በሰማያት ፡ ፍሥሐ ፡ ብዙኅ ፡ በእንተ ፡ ፩ዱ ፡ ኃጥእ ፡ ዘይኔ ስሕ ። ጅ ፡ ፯ቱ ፡ ወእግዚእነሰ ፡ ኢመጽአ ፡ ከመ ይጸውዕ ፡ ጻድቃነ ፡ አላ ፡ ኃጥአነ ፡ ለንስሓ ።

፪፻፺፩ ዓሥር ፡ ወራብዕ ፡ ረስጠብ ፡ ዘ፴ወ፩ዱ ፡ እመቦ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ አው ፡ ቀሲስ ፡ አው ፡ ዲያቆን ፡ ዘኮነ ፡ መዘለፈ ፡ ስካር ፡ ወእከይ ፡ ለንዲገ ፡ ሠሃ ይት ፡ ፴ወ፱ቱ ፡ አው ፡ ነሥአ ፡ እምነ ፡ ዘይፈ

፪፻፹፮ በበደሉ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚመረምረው ፡ ይሁን ። ወደ ፡ በደሉ ፡ ይመለስ ፡ ዘንድ ፡ ፈራ ጆች ፡ ሰዎች ፡ አይተውት ። ሕዝቡም ፡ ለርሱ ፡ እንደሚገባ ፡ ለበጎ ፡ ሥራ ፡ በደሉን ፡ ይቅር ፡ የሚሉት ይሁኑ ። እርሱም ፡ ስለ ፡ በደሉ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚማልድ ፡ ይሁን ።

፪፻፹፯ አሥራ ፡ አንደኛ ። ረስጠጅ ፡ ፶፪ ። ረስጠብ ፡ ፶፩ ። ረስጠብ ፡ ፹፯ ፡ ፹፰ ። እግዚአብሔርን ፡ ከማገልገልና ፡ ከመፍራት ፡ ሕዝቡንና ፡ ካህና ቱንም ፡ ከማስተማር ፡ ቸል ፡ የሚል ፡ ኤጲስ ቆጶስ ፡ ወይም ፡ ቄስ ፡ ወይም ፡ ዲያቆን ፡ በስን ፍናው ፡ ጸንቶ ፡ ቢኖር ፡ ይሻር ።

፪፻፹፰ ጅ ፡ ፮ ። እንደዚህም ፡ ጌታችን ፡ ሥራውን ፡ አስቀድሞ ፡ ሠርቶ ፡ ማስተማር ፡ ጀመረ ። (የሐ ዋ ፡ ፩ ፡ ፩-፪) ። ሉቃስም ፡ ሐዋርያት ፡ ሁሉ ፡ ለማስተማር ፡ ሁልጊዜ ፡ በምኵራብና ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡ ያገለግሉ ፡ ነበር ፡ አለ ። (የሐዋ ፡ ፲፫ ፡ ፩- ፪) ። ጳውሎስም ፡ ደቀመዝሙሩን ፡ ዘወ ትር ፡ ያስተምር ፡ ዘንድ ፡ እንዳዘዘው ። (፪ጢሞ ፡ ፬ ፡ ፩ -፪) ።

፪፻፹፱ አሥራ ፡ ሁለተኛ ። ረስጠብ ፡ ፶፱ ። ረስጠብ ፡ ፵ ። ድሆችንና ፡ ካህናትን ፡ ቸል ፡ የሚላቸው ፡ የሚቻለውንም ፡ የማይሰጣቸው ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ወይም ፡ ቄስ ፡ ቢኖር ፡ ይለይ ። ቸል ፡ በማለት ፡ ጸንቶ ፡ ቢኖርም ፡ ወንድሙን ፡ ገዳይ ፡ እንደመ ሆኑ ፡ ይሻር ።

፪፻፺ አሥራ ፡ ሦስተኛ ። ረስጠብ ፡ ፴፰ ። ረስጠጅ ፡ ፵፪ ። ንስሓ ፡ በገባ ፡ ጊዜ ፡ ኃጢአተኛውን ፡ የማ ይቀበል ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ወይም ፡ ቄስ ፡ ቢኖር ፡ ይሻር ፡ ንስሓ ፡ ስለሚገባ ፡ ስለ ፡ አንድ ፡ ኃጢ አተኛ ፡ በሰማይ ፡ ፍጹም ፡ ደስታ ፡ ይሆናል ፡ (ሉቃ ፡ ፲፭ ፡ ፯) ። ብሎ ፡ ጌታችን ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ የተናገረውን ፡ አፍርሷልና ። ጅ ፡ ፯። ጌታችን ፡ ግን ፡ ጻድቃንን ፡ ሊጠራ ፡ አልመጣም፡ ኃጥአንን ፡ ለንስሓ ፡ ሊጠራ ፡ መጣ ፡ እንጂ ። (ማቴ ፡ ፱ ፡ ፲፫) ።

፪፻፺፩ አሥራ ፡ አራተኛ ። ረስጠብ ፡ ፴፩ ። መልካምን ፡ ለመተው ፡ ስካርንና ፡ ክፋትን ፡ የሚያዘወትር ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ወይም ፡ ቄስ ፡ ወይም ፡ ዲያቆን ፡ ቢኖር ። ፴፱ ፡ ወይም ፡ ከአበደረው ፡ ሰው ፡

ሆሙ ፡ እምድኅረ ፡ ተዋሰቦሙ ፡ ወፈቀደ ፡ ፩ዱ ፡ ከመ ፡ ይትፈለጥ ፡ እምካልኡ ፡ ኢኮነ ፡ ዝንቱ ፡ ብጡሐ ፡ ሎቱ ።

፱፻፶፭ ወዳግማዊ ፡ መክ ፡ ፳ወ፫ቱ ፡ ወውእቱ ፡ ዘይደሉ ፡ ወዘእውሰበ ፡ ብእሲተ ፡ ወእምዝ ፡ ኮነ ፡ ባቲ ፡ ድኅረ ፡ ተዋስቦታ ፡ ውስተ ፡ ሥጋሃ ፡ ደዌ ፡ ዘከመ ፡ ዝልጋሴ ፡ ወለምጽ ፡ ወእመ ፡ ውእቱ ፡ ፈቀደ ፡ ተፈልጦታ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ የሀባ ፡ ኵሎ ፡ ትሎታ ፡ ወሕፃያ ። ወለእመ ፡ ኢፈቀደ ፡ ተፈልጦቶ ፡ ብጡሕ ፡ ሎቱ ፡ እንብሮታ ፡ በተሰናእዎ ፡ ከመ ፡ የሀባ ፡ ላቲ ፡ ሲሳየ ፡ በእምጣነ ፡ ክሂሎቱ ፡ እምንዋዩ ፡ እስመ ፡ ዘኮነ ፡ ላዕሌሃ ፡ ኢኮነ ፡ በፈቃዳ ፡ ወኢ ፡ በፈቃዱ ፡

፱፻፶፮ ጠስ ፡ ፲ወ፩ዱ ፡ ወንኤዝዝ ፡ እብዮሎቶ ፡ ተዋስቦ ፡ ለዘሀሎ ፡ ውስተ ፡ እሥረት ፡ ወባሕቱ ፡ እስከ ፡ ይትዐወቅ ፡ ብእሲ ፡ ወብእሲት ፡ የሀልዉ ፡ ወንሕነ ፡ ንኀድግ ፡ ተደምሮ ፡ እስከ ፡ ፍጻሜሃ ፡ ወኢይኩን ፡ ተዋስቦ ፡ ዳግማዊ ፡ ኢ ፡ ለእንስት ፡ ወኢ ፡ ለእደው ። ወእመ ፡ ተኀብሉ ፡ ይገሥጽ ፡ ምሙ ፡ ለብእሲኒ ፡ ይንሥኡ ፡ እምኔሁ ፡ እምኅ ፡ ዘእምቅድመ ፡ መርዓ ፡ ወለብእሲትኒ ፡ ይንሥኡ ፡ እምኔሃ ፡ ሕፃያ ፡ ወትሎታ ። ወእመሰ ፡ ኮነ ፡ በኀቡእ ፡ ለእመ ፡ ቦኑ ፡ ሀለወ ፡ ብእሲ ፡ በሕይወቱ ፡ ዘእኁዝ ፡ በእደ ፡ ጸላኢሁ ፡ አው ፡ አልቦ ፡ ይእቲ ፡ ጊዜ ፡ ይደልዎ ፡ ለብእሲ ፡ አው ፡ ለብእሲት ፡ ከመ ፡ ይትዓገሡ ፡ ፭ተ ፡ ዓመተ ። ወእምድኅረ ፡ ዝንቱ ፡ ለእመ ፡ ተጠየቀ ፡ ግብረ ሞቱ ፡ አው ፡ ርኅቀቱ ፡ ወተኀብአ ፡ ይደሉ ፡ እንከ ፡ እስተዋስቦ ፡ በእንበለ ፡ ፍርሃት ፡ ይትዐወቅ ፡ ድልው ፡ አውሰበ ፡ ለእመ ፡ አስተርአየ እምድኅረ ፡ ውእቱ ፡ ግብረ ፡ ተወፍዮት ፡ አው ፡ ተሰወረ ።

፱፻፶፯ ዘ፲ወ፰ቱ ፡ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ብእሲሁ ፡ እምሐራ ፡ ንጉሥ ፡ ንሕነ ፡ ንኤዝዝ ፡ ከመ ፡ ይጽንሑ ፡ መጠነ ፡ ፬ቱ ፡ ዓመታት ፡ ዘይከውን ፡ ባቲ ፡ ዘሚጥ ፡ ወይትዓገሥ ፡ እንስቲያሆሙ ፡ ወለእመ ፡ ኢመጽአ ፡ ኀቤሆን ፡ እምኀቤሆሙ ፡ ክታብ ፡ ወኢበጽሐ ፡ ኀቤሆን ፡ ዜና ። ወለእመ ሰምዐት ፡ አሐቲ ፡ እምኔሆን ፡ ከመ ፡ ሞተ ፡ ምቱ ፡ ኢይደልወን ፡ ናብሕ ፡ ላቲ ፡ ከመ ፡ ታውስብ ፡ በእንበለ ፡ ትጠይቅ ፡ ለሊሃ ፡ አው ፡ ወላዲ ፡ ያኒሃ ፡ አው ፡ ካልእኒሆሙ ፡ ኀበ ፡ መኳንንት ፡



ደዌ ፡ ሥጋ ፡ ቢያዘው ፡ እንዲ ፡ ከሁለተኛው ፡ ሊለይ ፡ ቢወድ ፡ ይህ ፡ ለእርሱ ፡ የተፈቀደ ፡ አይደለም ።

፱፻፶፭ ሁለተኛውም ፡ መክ ፡ ፳፫ ። ይህም ፡ የሚገባ ፡ ነው ። ሚስት ፡ ያገባ ፡ ሰው ፡ ከመጋባቱ ፡ በኋላ ፡ በሥጋዋ ፡ ውስጥ ፡ ደዌ ፡ ቢያድርባት ፡ ይኸውም ፡ እንደ ፡ ደዌ ፡ ሥጋ ፡ እንደ ፡ ለምጽ ፡ ያለ ፡ ነው ። እርሱ ፡ ሊፈታት ፡ ቢወድ ፡ ትልጡቷንና ፡ ማጫዋን ፡ ሁሉ ፡ ሊሰጣት ፡ ይገባዋል ። ሊለያት ፡ ባይወድም ፡ በተቻለው ፡ መጠን ፡ ምግቧን ፡ ከገንዘቡ ፡ እንዲሰጣት ፡ በመስማማት ፡ ሊያኖራት ፡ ይገባዋል ። በእርሷ ፡ ላይ ፡ የሆነው ፡ በፈቃዷ ፡ ወይም ፡ በፈቃዱ ፡ አልሆነምና ።

፱፻፶፮ ጠስ ፡ ፲፩ ። በእሥራት ፡ ላለ ፡ ሰው ፡ የጋብቻን ፡ መፍረስ ፡ እናዝዛለን ። ነገር ፡ ግን ፡ እስኪታወቅ ድረስ ፡ ባልና ፡ ሚስት ፡ ይኑሩ ። (ይጠብቁ) ፡ እስከ ፡ መጨረሻዋ ፡ ድረስ ፡ መገናኘትን ፡ እኛ ፡ እንከለክላለን ። ለሴቶችም ፡ ለወንዶችም ፡ ሁለተኛ ፡ ጋብቻ ፡ አይገባም ። ቢያፋልሱ ፡ ግን ፡ ይቅጧቸው ። ከወንዱ ፡ ከመርዓ ፡ አስቀድሞ ፡ የመጣውን ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ ይውሰዱ ። ከሴቷም ፡ ማጫዋንና ፡ ትልጡቷን ፡ ይውሰዱ ። በስውር ፡ ቢሆን ፡ በጠላቱ ፡ እጅ ፡ የተያዘው ሰው ፡ በሕይወቱ ፡ ቢኖር ፡ ወይም ፡ ያንጊዜ ባይኖር ፡ ለወንድ ፡ ወይም ፡ ለሴት ፡ አምስት ዓመት ፡ ሊታገሡ ፡ ይገባቸዋል ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የሞቱ ፡ ነገር ፡ (ዜና) ፡ ወይም ፡ ርቆ መሄዱ ፡ ቢታወቅም ፡ ባይታወቅም ፡ እንግዲህ ያለ ፡ ፍርሃት ፡ ማግባት ፡ ይገባል ። ከዚህ ከመቀበል ፡ ሥራ ፡ በኋላ ፡ ቢገለጽም ፡ ቢሠወርም ፡ ማግባት ፡ እንዲገባ ፡ ይታወቃል ።

፱፻፶፯ ፲፰ ። ሰውየው ፡ ከንጉሥ ፡ ጭፍራ ፡ ወገን ቢሆን ፡ ዘመቻ ፡ የሚሆንባትን ፡ ሁለት ፡ ዘመት ያህል ፡ ይጠብቁ ፡ ዘንድ ፡ እኛ ፡ እናዝዛለን ። ሚስቶቻቸውም ፡ ይታገሡ ። ከባሎቻቸው ዘንድ ፡ ወደእነርሱ ፡ ደብዳቤ ፡ ባይመጣ ፡ ወሬም ፡ ባይደርሳቸው ፡ ከእነርሱ ፡ አንዲቱ ፡ ባሏ ፡ እንደሞተ ፡ ብትሰማ ፡ እርሷ ፡ ሳትረዳ ፡ ወይም ፡ ወላጆቿ ፡ ወይም ፡ ለሌሎች ፡ ባላ ፡ ማገልገልን ፡ ከሚያገለግላቸው ፡ ከመኳንንቱ ፡ ዘንድ ፡ ስለ ፡ ወሬው ፡ እርግጠኛ ፡ ሳትጠይቅ ፡

አንቀጽ ፡ ፳፬ ።

መልእክተ ፡ እንተ ፡ ኮነ ፡ ይትለአኮሙ ፡ ምታ ፡ ወትስእሎሙ ፡ በእንተ ፡ ጥያቄ ፡ ዜናሁ ። ወእመ ፡ ሞተ ፡ ይኩን ፡ ወንጌል ፡ ቅዱስ ፡ በቅድሜሆሙ ፡ ኅቡረ ፡ ለስምዕ ፡ ወእምድኅረ ፡ ጸንዐ ፡ ጥያቄሁ ፡ ትንሣእ ፡ ብእሲት ፡ መጽሐፈ ፡ መባሕት ፡ በዘይትዐወቁ ፡ ቦቱ ፡ ስማዕታት ፡ ላቲ ፡ ወእምድኅረዝ ፡ ትትወሰብ ፡ ፩ደ ፡ ዓመተ ፡ ወእምዝ ፡ ይደልዋ ፡ ከመ ፡ ትትወሰብ ፡ ተዋስቦ ፡ ሕጋዌ ። ወእመሰ ፡ ተንበለት ፡ ወተወዶ ፡ ወት ፡ ዘንተ ፡ ይእቲኒ ፡ ወዘያወስባ ፡ ይትገሠጹ ፡ ከመ ፡ ተማኅጸ ፡ ዘማውያን ። ወሰማዕታተ ፡ ጥያቄ ፡ ለእመ ፡ ኮኑ ፡ ስምዐ ፡ በሐሰት ፡ ይደቁ ፡ እመዓርጊሆሙ ፡ ወየሀቡ ፡ ፲ተ ፡ ልጥረ ፡ ወርቅ ፡ ወይኩን ፡ ለዘሐሰዉ ፡ በእንቲአ ፡ ሞቱ ። ወእምዝ ፡ ይደልዎ ፡ ለውእቱ ፡ ብእሲ ፡ ከመ ፡ ይግበር ፡ ዘኀረየ ፡ እመ ፡ ይፈቅድ ፡ ትትመየጥ ፡ ኀቤሁ ፡ ይንሣእ ፡ ብእሲቶ ።

፱፻፶፬ ወሣልስኒ ፡ ይትከፈል ፡ ኀበ ፡ ፫ቱ ፡ ክፍላት ፡ ቀዳሚ ፡ በእንተ ፡ ዝሙታ ፡ ለብእሲት ። ጠስ ፡ ዘ፲ወ፩ዱ ፡ ወለእመ ፡ አእመረ ፡ ብእሲ ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡ ይትኬሀሎ ፡ ከመ ፡ ያቅም ፡ ስምዐ ፡ ጥያቄ ፡ ምስለ ፡ ብእሲቱ ፡ ከመ ፡ ይእቲ ፡ ዘመወት ፡ ይደልዎ ፡ ቅድመ ፡ ከመ ፡ ያቅም ፡ ዘንተ ፡ እሚሃ ፡ ይደልዎ ፡ ኀዲጎታ ። ወይንሣእ ፡ ብእሲ ሕዜሃ ፡ መጠነ ፡ ካዕበት ፡ ምስለ ፡ አምኃ ፡ ዘቀደመ ፡ ለመርዓ ። ወለእመ ፡ አልቦቱ ፡ ውሉድ ፡ ይንሣእ ፡ እምንዋየ ፡ ብእሲት ፡ መጠነ ፡ ፫ቱ ፡ እድ ፡ እምትሎታ ። ወለእመሰ ፡ ቦቱ ፡ ውሉድ ፡ እምኔሃ ፡ ለይኩን ፡ ትሎታ ፡ ወዘተርፈ ፡ ንዋያ ፡ ዕቁበ ፡ ለውሉዳ ። ወእምድኅረዝ ፡ ሶበ ፡ ተከሥተ ፡ ግብረ ፡ ዝሙት ፡ በላዕሌሃ ፡ ይትኩነኑ ፡ ውእቱ ፡ ወይእቲ ፡ ኅቡረ ። ወለዘማዊኒ ፡ ዘዘመወ ፡ በብእሲቱ ፡ ይንሥኡ ፡ እምኔሁ ፡ መጠነ ትሎት ፡ ዘወሀባ ፡ ተዳሚ ፡ በጊዜ ፡ መርዓ ። ወለእመ ፡ ቦቱ ፡ ካዕበ ፡ ብእሲት ፡ ለዘማዊ ፡ ለትንሣእ ፡ ሕፄሃ ፡ ምስለ ፡ አምኃ ፡ ዘእምቅድመ ፡ መርዓ ፡ ወእመሰ ፡ ዘየ ፡ ሀለዉ ፡ ውሉድ ፡ ኢይኩን ፡ ለብእሲ ፡ ዘእንበለ ፡ ተማባረ ፡ ዚአሁ ፡ ወንዋዩሰ ፡ የሀሉ ፡ በተዐቅቦ ፡ ለውሉዱሙ ። ወዘሀሎ ፡ ለብእሲ ፡ እምድኅረ ፡ ዝንቱ ፡ እምነ ፡ ጥሪት ፡ ንሕነ ፡ ንሁቦሙ ፡ ለውሉድ ፡ ወእምኃስ ፡ ዘእምቅድመ ፡ መርዓ ፡ ንኤዝዝ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ለብእሲት ፡ ለእመ ፡ ኢሀለዉ ፡ ውሉድ ፡ ወተረፈ ፡ ጥሪቱ ፡ ይኩን ፡ በማእከል ።

ስለ ፡ ጋብቻ ።

እንድታገባ ፡ ልናስናብታት ፡ አይገባንም ። ቢሞትም ፡ ቅዱስ ፡ ወንጌል ፡ ለምስክርነት ፡ በፊታቸው ፡ ይኑር ። እርግጠኛነቱ ፡ ከታወቀ ፡ በኋላ ፡ ሴትዮዋ ፡ ለእርሷ ፡ የመሰከሩላት ፡ ምስክሮች ፡ በሚታወቁበት ፡ ግንዘብ ፡ የስንብት ፡ ደብዳቤ ፡ ትቀበል ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ ትታገሥ ። ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ሕጋዊ ፡ ጋብቻ ፡ ልታገባ ፡ ይገባታል ። ይህን ፡ ብትደፋፈርና ፡ ብትተላለፍ ፡ ግን ፡ እርሷም ፡ የሚያገባትም ፡ እንደ ፡ ዘማውያን ፡ ቅጣት ፡ ይቀጡ ። ያስረዱትም ፡ ምስክሮች ፡ በሐሰት ፡ የመሰከሩ ፡ ቢሆኑ ፡ ከመዓርጋቸው ፡ ይዋረዱ ። ፲ ፡ ወቄት ፡ ወርቅ ፡ ይስጡ ። በሞቱ ፡ ምክንያት ፡ ለዋሹበት ፡ ሰው ፡ ይሁን ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ለዚያ ፡ ሰው ፡ የመረጠውን ፡ ሊያደርግ ፡ ይገባዋል ። ወደእርሱ ፡ ልትመለስ ፡ ቢወድ ፡ ሚስቱን ፡ ይውሰድ ።

፱፻፶፬ ፫ኛውም ፡ ከሦስት ፡ ክፍል ፡ ይከፈላል ። መጀመሪያው ፡ ስለሴት ፡ ዝሙት ፡ ይናገራል ። ጠስ ፡ ፲፩ ። እርሷ ፡ እንደሰሰነች ፡ ከሚስቱ ፡ ጋራ ፡ የማስረጃ ፡ ምስክር ፡ ያቆም ፡ ዘንድ ፡ እንደሚቻለው ፡ ቢያውቅ ፡ አስቀድሞ ፡ ይህን ፡ ሊወስን ፡ ይገባዋል ። ያንጊዜ ፡ ሊፈታት ፡ ይገባዋል ። ባል ፡ ማጫዋን ፡ ለሠርግ ፡ ከቀደመው ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ ጋራ ፡ በእጠፉታ ፡ ይውሰድ ። ልጅ ፡ ባይኖረው ፡ ከሴት ፡ ገንዘብ ፡ ወገን ፡ ከትል ወቷ ፡ ፫ ፡ እጅ ፡ ያህል ፡ ይውሰድ ። ከእርሷ ፡ ልጆች ፡ ቢኖሩት ፡ ግን ፡ ትልወቷና ፡ የቀረ ፡ ገንዘቧ ፡ ለልጆቿ ፡ የተጠበቀ ፡ ይሁን ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በእርሷ ፡ ላይ ፡ የዝሙት ፡ ሥራ ፡ ቢገለጥ ፡ እርሱም ፡ እርሷም ፡ በአንድነት ፡ ይቀጡ ። በፊታት ፡ ሚስቱ ፡ ሲሰስን ፡ የተገኘ ፡ አመንዝራም ፡ በሠርግ ፡ ጊዜ ፡ አስቀድሞ ፡ በሰጣት ፡ ትልወት ፡ ልክ ፡ ከእርሱ ፡ ይውሰዱ ። ዳግመኛም ፡ ለአመንዝራው ፡ ሰው ፡ ሚስት ፡ ብትኖረው ፡ ከሠርግ ፡ በፊት ፡ ከተሰጠው ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ ጋራ ፡ ማጫዋን ፡ ትውሰድ ፡ ከዚያ ፡ ልጆች ፡ ቢኖሩት ፡ ከሥራው ፡ (ሠርቶ ፡ ካገኘው) በቀር ፡ ለእርሱ ፡ አይሁን ። ገንዘቡ ፡ ግን ፡ ለልጆች ፡ ተጠብቆ ፡ ይኑር ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ለሰውየው ፡ ከገንዘብ ፡ ወገን ፡ ያለውን ፡ እኛ ፡ ለልጆች ፡ እንሰጣለን ። ከሠርግ ፡ የቀደመው ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ ግን ፡ ልጆች ፡ ከሌሉ ፡ ለሴቷ ፡ እንዲ

፱፻፺፭ ወዳግምስ ፡ ዘይደሉ ፡ በእንተ ፡ ዘማዊት ፡ ብእሲት ። ጠስ ፡ ፲ወ፩ዱ ፡ ወከማሁ ፡ ለእመ ፡ ስትየት ፡ ብእሲት ፡ ዘእንበለ ፡ ምክረ ፡ ምታ ፡ ምስለ ፡ ብእሲ ፡ ካልእ ፡ አው ፡ ተሐፅበት ፡ አው ፡ ስሐቀት ፡ አው ፡ ሖረት ፡ ኀበ ፡ መካነ ፡ አሥግሮ ፡ ወጉባኤ ፡ እንዘ ፡ ኢሀሎ ፡ ምታ ፡ እምነ ፡ ዝንቱ ። አው ፡ ኀደረት ፡ አፍአ ፡ እምቤታ ፡ ኀበ ፡ ካልእ ፡ ቤት ፡ ለእመ ፡ ኢኮነ ፡ በይቶታ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ አቡሃ ፡ ወለእመኒ ፡ አልባቲ ፡ አብ ፡ ወኮነ ፡ ዝንቱ ፡ ምክንያተ ፡ ኀዲሮታ ፡ በአፍአ ። ወበዘይከውን ፡ ከዋኔ ፡ ዝንቱ ፡ ሥርዓተ ፡ ተዋስቦታት ፡ አለ ፡ ውጉዛት ፡ ውስተ ፡ አከፋል ፡ ቀዳማውያን ። ረስጣ ፡ ፲ወ፱ቱ ፡ ዘእንበለ ፡ ፰ቱ ፡ ወ፺ቱ ፡ ወናሁ ፡ ሀሎ ፡ ውስተ ፡ ካልእ ፡ እምውእቱ ፡ ጉልቈ ፡ ቀኖና ፡ ወይእቲ ፡ ረስጣ ፡ ዘ፲ወ፺ቱ ፡ ቀጠጅ ፡ ዘ፪ቱ ፡ በስ ፡ ፳ወ፳ቱ ፡ ዘ፵ወ፬ቱ ፡ ወዘተርፈ ፡ ዘተአምረ ፡ በዘከሮ ፡ በተባዕት ፡ ይትጐሰቆ ፡ ላዕለ ፡ ዘተዐውቀ ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ዘከማሁ ።

፱፻፺፮ ወኀልስ ፡ በእንተ ፡ ሰበ ፡ ፈተደ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ እማስኖተ ፡ ሕይወት ፡ ካልኡ ፡ ወእማስኖተ ፡ ንጽሐ ፡ ለብእሲት ። ጠስ ፡ ፲ወ፩ዱ ፡ ወእመ ፡ ብእሲት ፡ መከረት ፡ ለአኅጕሎ ፡ ሕይወተ ፡ ምታ ፡ በምንትኒ ፡ ኀጸ ፡ እምኀጸት ፡ አው ፡ አአመረት ፡ ከመ ፡ ካልኣን ፡ ይጽሕቁ ፡ በዝንቱ ፡ ወኢከሠተት ፡ ሎቱ ። ኒቅያ ፡ ፶ወ፰ቱ ፡ ወዘአውሰበ ፡ ብእሲተ ፡ ወኮነ ፡ ማእከሌሆሙ ፡ መማእከለ ፡ ብእሲቱ ፡ እከይ ፡ አው ፡ ምክንያት ፡ እምክንያታት ፡ ወኮነት ፡ ይእቲ ፡ ሀማዪተ ፡ ሎቱ ፡ ይትሀገሦ ፡ ኪያሃ ፡ ወይምሕካ ፡ ላቲ ፡ እስከ ፡ ትትመየጥ ፡ እምግብራ ፡ ኀበ ፡ ሠናያት ። ወለእመ ፡ ኢተከሀለ ፡ በዝንቱ ፡ ወተወስከ ፡ ግብራ ፡ ላዕሌሁ ፡ ያብጽሓ ፡ ኀበ ፡ ቀሲስ ፡ ዐቢይ ፡ እምቀሲሳን ፡ ወይኅሡን ፡ ሀራቂ ፡ ማእከሌሆሙ ፡ ወለእመ ፡ እበየት ፡ ኪያሁ ፡ ሰይፍታሕ ፡ ማእከሌሆሙ ፡ ኤጲስቆጶስ ። ወለእመ ፡ ኢተአዘዘት ፡ ሎቱኒ ፡ ወኀየየት ፡ እምታ ፡ ወሶማ ብእ ፡ ካዕበ ፡ ወእመስ ፡ ጸንዐት ፡ ወኢሰምዐት ፡ ቃሎ ፡ ለገቢእ ፡ ወይንግፍ ፡ እግእዚኡ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ወጸበለ ፡ እገሪሁ ፡ ውስተ ፡ ይዲያሃ ። ወብውሕ ፡ ለብእሲሃ ፡ ከመ ፡ ይግበር ፡ ዘአፍ



ሆን ፡ እናዝዛለን ። የገንዘቡ ፡ ትርፍም ፡ በመካከል ፡ ይሁን ።

፱፻፺፭ ሁለተኛውም ፡ ስለአመንዝራይቱ ፡ ሴት ፡ የሚገባውን ፡ ይናገራል ። ጠስ ፡ ፲፩ ። እንደዚሁም ፡ ሴት ፡ ያለባልዋ ፡ ፈቃድ ፡ ከሌላ ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ ብትጠጣ ፡ ወይም ፡ ፍል ፡ ውሀ ፡ ብትታጠብ ፡ ወይም ፡ ብትስቅ ፡ ወይም ፡ ወደማጥመጃያና ፡ ወደስብሰባ ፡ ቦታ ፡ ከዚያ ፡ ባሏ ፡ ሳይኖር ፡ ብትሄድ ፡ ወይም ፡ ከቤቷ ፡ ውጭ ፡ በሌላ ፡ ቤት ፡ ብታድር ፡ ማደሯም ፡ በአባቷ ፡ ቤት ፡ ባይሆን ፡ አባት ፡ ባይኖራትም ፡ በውጭ ፡ የማደሯ ፡ ምክንያት ፡ ይህ ፡ ቢሆን ፡ የዚህ ፡ ሁኔታ ፡ በመጀመሪያዎቹ ፡ ክፍሎች ፡ ውስጥ ፡ በተከለከሉት ፡ የጋብቻዎች ፡ ሥርዐት ፡ በሚሆን ፡ ገንዘብ ፡ ነው ። ረስጣ ፡ ፲፱ ። ከ፰ኛውና ፡ ከ፺ኛው ፡ በቀር ፡ እነሆ ፡ ከዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ ወጥቶ ፡ በሌላ ፡ ውስጥ ፡ አለ ። ይህችውም ፡ ረስጣ ፡ ፲፺ ፡ ቀጠጅ ፡ ፪ ። በስ ፡ ፳፰ ። ፵፬ ፡ ነው ። በወንድ ፡ ላይ ፡ በመነገር ፡ ታውቆ ፡ የቀረውም ፡ በታወቀው ፡ ላይ ፡ ይቆጠራል ። እርሱ ፡ እንደ ፡ እርሱ ፡ ነውና ።

፱፻፺፮ ፫ኛውም ፡ ከእነርሱ ፡ አንዱ ፡ ያንዱን ፡ ሕይወት ፡ ሊያጠፋ ፡ የሚስቱንም ፡ ንጽሕና ፡ ሊያሳድፍ ፡ በወደደ ፡ ጊዜ ፡ ስለሚሆነው ፡ ይናገራል ። ጠስ ፡ ፲፩ ። ሚስት ፡ ከሥራ ፡ በማናቸውም ፡ ሥራ ፡ የባሏን ፡ ሕይወት ፡ ለማጥፋት ፡ ብትመክር ፡ ወይም ፡ ሌሎች ፡ ሲመክሩ ፡ አውቃ ፡ ባትገልጽለት ፡ ነው ። ኒቅያ ፡ ፶፰ ። ሚስት ፡ ያገባ ፡ ሰው ፡ በእርሱና ፡ በሚስቱ ፡ መካከል ፡ ፀብ ፡ ክርክር ፡ ቢኖር ፡ ወይም ፡ ከምክንያቶች ፡ ወገን ፡ ምክንያት ፡ ቢኖር ፡ እርሱን ፡ የምትበድል ፡ ሰው ፡ ብትሆን ፡ ከክፉ ፡ ሥራዋ ፡ ወደበጎ ፡ ሥራ ፡ እስክትመለስ ፡ ድረስ ፡ ይታገሣት ፡ ይራራላት ። በዚህ ፡ ባይቻል ፡ ክፋቷ ፡ በዚያው ፡ ላይ ፡ ቢጨመር ፡ ከቀሳውስት ፡ ወገን ፡ ወደ ፡ ትልቁ ፡ ቄስ ፡ ያድርሳት ። በመካከላቸውም ፡ አስታራቂ ፡ ይሁን ። እርሱን ፡ እንቢ ፡ ብትል ፡ ኤጲስቆጶሱ ፡ በመካከላቸው ፡ ይፍረድ ። ለእርሱም ፡ ባትታዘዝ ፡ ከባሏም ፡ ብትሸሽ ፡ ዳግመኛ ፡ ይመልሳት ። ብትሆን ፡ ግን ፡ ለመመለስም ፡ ቃሉን ፡ ባትሰማ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ከይጅዋ ፡ ሒማውንና ፡ የእግሩን ፡ ትቢያ ፡ ያራግፍ ። ለባሏ ፡ የወደደውን ፡ ሊያደርግ ፡ ሥልጣን ፡ አለው ።

አንቀጽ ፡ ፳፰ ።

ውዴት ፡ ዘይከውን ፡ አሙነ ፡ ወኢይጸንዕ ፡ ጥያቄሁ ። ዝንቱኒ ፡ ወዘይመስሎ ፡ ይደሉ ፡ ከመ ፡ የሀቡ ፡ በእንቲአሁ ፡ ዙንጌ ፡ ንስሓ ፡ እስ ፡ ቦሙ ፡ ሥልጣን ፡ ሳዕለ ፡ ሥርየተ ፡ ኃጢአት ፡ ወእኮ ፡ ከመ ፡ ይፍጽሙ ፡ ብእሲተ ፡ እም ብእሲሃ ።

ዕቁባትን ፡ ስለመከልከል ።

እውነት ፡ የሚሆንና ፡ እርግጠኛነቱ ፡ የማይፀና ፡ አለና ፡ በዚህና ፡ በመሰለው ፡ ሴትን ፡ ከባልዋ ፡ ስመለየት ፡ ያይደለ ፡ ኃጢአትን ፡ ለማስተሥረይ ሥልጣን ፡ ያላቸው ፡ ስለእርሱ ፡ የንስሐ ፡ ቅጣት ሊሰጡ ፡ ይገባል ።

---

## አንቀጽ ፡ ፳ወ፫ቱ ።

በእንተ ፡ አኀርሞተ ፡ ዕቁባት ፡ ወግብረ ፡ ዕቁ ባት ፡ ወብእሲት ፡ ዘእስርት ፡ በሕግ ።

፲፻፹፬ ንሕነ ፡ ዕቅብትሰ ፡ በውስተ ፡ ሕግነ ፡ ቅድስት ፡ ሕሩም ፡ ውእቱ ፡ እስመ ፡ ውፁእ ፡ ውእቱ ፡ እም አውስቦ ፡ ዘብዉሕ ፡ እምቀዳሚ፡ ዘተጠየቀ ፡ ውእቱኒ ፡ ዝሙት ፡ ዘዘልፍ።

፲፻፹፭ ረስጠብ ፡ ፳ወ፩ቱ ፡ እመቦ ፡ ዘቦቱ ፡ ዕቅብት ፡ እመ ፡ ኮነት ፡ አመተ ፡ ዚአሁ ፡ ለይኅድግ ፡ ወያ ውስብ ፡ በከመ ፡ ሕግ ፡ ወእመሰ ፡ ኮነት ፡ አግዓ ዚተ ፡ ለያውስባ ፡ በከመ ፡ ሕግ ። ወለእመ ፡ ኢፈ ቀደ ፡ ከመ ፡ ይግበር ፡ ዘንተ ፡ ይሰደድ ።

፲፻፹፮ ጠስ ፡ ፬ቱ ፡ ወኢይኩን ፡ ለፈዱሂ ፡ መባሕት ፡ ከመ ፡ ይንበር ፡ ምስለ ፡ ዕቅብት ፡ ውስተ ፡ ማኅ ደሩ ፡ ወአልቦኬ ፡ ፍልጠት ፡ ማእከሌሁ ፡ ወማ እከለ ፡ ዘማውያን ፡ ወእመ ፡ ፈቀደ ፡ ተሳትፎታ ለያውስባ ፡ በሥርዓተ ፡ ስብሳብ ፡ ዘሕግ ። ወለእ መሰ ፡ ይሬኢ ፡ ከመ ፡ ይእቲ ፡ ኢኮነት ፡ ድሉተ ከመ ፡ ትሰመይ ፡ ሎቱ ፡ ብእሲተ ፡ ሕግ ፡ ለይስ ድዳ ፡ ወይንሣእ ፡ ዘየንቲሃ ፡ ዘትኀሥሥ ፡ ወለ እመኒ ፡ ፈቀደ ፡ ለይንበር ፡ በንጽሕ ።

፲፻፹፯ ዘ፴ወ፱ቱ ፡ ወዘሎቱ ፡ ብእሲት ፡ ወዘያወስብ ፡ አመተ ፡ ዚአሁ ፡ ይትገሠጽ ፡ ወይደልዎ ፡ ለሊቅ ፡ ከመ ፡ ይሢጥ ፡ ኪያሃ ፡ ውስተ ፡ ካልእ ፡ ብሔር ፡ ርኁቅ ።

፲፻፹፰ ረስጠብ ፡ ፳ወ፱ቱ ፡ ፳ወ፬ቱ ፡ ወዕቅብቱ ፡ ዘኢ ማእምንት ፡ ለዘኢየአምን ፡ ወሶበ ፡ ኮነት አመተ ፡ ዚአሁ ፡ ዘኢረከበት ፡ ምስለ ፡ ካልእ ፡ ወእልኀተት ፡ ውሉዳ ፡ ለትባእ ፡ ወእመሰ ረከበት ፡ ምስለ ፡ ካልእን ለትስደድ ።

፲፻፹፱ በስ ፡ ፷ቱ ፡ ወኢይደልዎ ፡ ለብእሲ ፡ ከመ ፡ ያን ብር ፡ ሎቱ ፡ ዕቅብተ ፡ እምድኅሬ ፡ እስመ ፡ እግ ዚእነ ፡ ክርስቶስ ፡ ሠርዐ ፡ ሕገ ፡ ግዕዛን ።

## አንቀጽ ፡ ፳፫ ።

ዕቁባት ፡ ማኖርን ፡ ስለመከልከል ፡ ስለዕቁባት፡ ሥራ ፡ በሕግ ፡ ስለታሠረችም ፡ ሴት ፡ ይናገ ራል ።

፲፻፹፬ ዕቁባት ፡ ማኖርስ ፡ በተቀደሰች ፡ ሕጋችን ፡ ውስጥ ፡ የተከለከለ ፡ ነው ። ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ ከተረዳው ፡ ከሚገባው ፡ ጋብቻ ፡ የወጣ ፡ ነውና። ይኸውም ፡ የዘወትር ፡ ዝሙት ፡ ነው ።

፲፻፹፭ ረስጠብ ፡ ፳፩ ። ዕቁባት ፡ ያለችው ፡ ሰው ፡ ቢኖ ር ፡ አገልጋዩ ፡ ብትሆን ፡ ይተውና ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፡ ያግባ ። ነፃ ፡ የወጣች ፡ ብትሆን ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፡ ያግባት ። ይህን ፡ ሊያደርግ ፡ ባይ ወድ ፡ ይለይ ።

፲፻፹፮ ጠስ ፡ ፬ ። አንድ ፡ ሰውስ ፡ እንኳ ፡ በቤቱ ፡ ከዕ ቁባት ፡ ጋራ ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ ሥልጣን ፡ አይኑ ረው ። በእርሱና ፡ በዘማውያን ፡ መካከል ፡ ልዩ ነት ፡ የለም ። ሊያገባት ፡ ቢወድ ፡ በሕግ ፡ ጋብቻ ፡ ሥርዓት ፡ ያግባት ። ለእርሱ ፡ የሕግ ፡ ሚስት ፡ ለመባል ፡ የተገባች ፡ እንዳልሆነች ፡ ቢያውቅ ፡ ግን ፡ ይፍታት ፡ በእርሷ ፡ ፈንታ ፡ የተሻለችውን ፡ ያግባ ። ቢወድም ፡ በንጽሕና ፡ ይኑር ።

፲፻፹፯ ፴፱ ። ሚስት ፡ እያለችው ፡ ከአገልጋዩ ፡ የሚ ደርስ ፡ ይቀጣ ። ለዳኛ ፡ ወደሌላ ፡ ሩቅ ፡ ሀገር ፡ እርሷን ፡ ሊሸጥ ፡ ይገባዋል ።

፲፻፹፰ ረስጠብ ፡ ፳፱ ። ፳፬ ። ላላመነው ፡ ያላመነች ፡ ዕቁባት ፡ ከሌላ ፡ ጋር ፡ ያልረከሰች ፡ አገልጋዩ ፡ ብትሆን ፡ ልጆቿንም ፡ ያሳደገች ፡ ከሆነች ፡ ትግባ ፡ (ትጠመቅ) ፡ ከሌሎች ፡ ጋራ ፡ የረከሰች፡ ብትሆን ፡ ግን ፡ ትለይ ።

፲፻፹፱ በስ ፡ ፷ ። ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ ዕቁባት ፡ ሊያኖር ፡ ለሰው ፡ አይገባውም ። ጌታችን ፡ ክርስቶስ ፡ የነፃነት ፡ ሕግ ፡ ሠርቷልና ። ለዳዊት ፡ ለሰሎሞ

አንቀጽ ፡ ፳፮ ።

ወእመ ትቤ ፡ ከመ ፡ ለዳዊት ፡ ወለሰሎሞን ወለካልእን ፡ ከና ፡ ሎሙ ፡ ዕቅብታት ፡ እመሰ ፈቀድከ ፡ ከመ ፡ ታእምር በማዕከ ፡ አሰመ ፡ በውእቱ ፡ ዘመን ፡ ኮኑ ፡ ሰብእ ፡ ሙኑዳነ ፡ በዲበ ፡ ምድር ። በእንተ ፡ ዝንቱ ፡ ተበውሐ ፡ ሎሙ ፡ ከመ ፡ ያውስቡ ፡ ወያንብሩ ፡ ሎሙ ፡ ዕቅብታት ፡ ከመ ይብዝኁ ፡ ሰብእ ፡ በዲበ ምድር ። ወሶበ ፡ ርእየ ፡ ከመ ፡ ምድር ፡ መልአት ፡ ከልአ ፡ ሕግ ፡ እምኑኅ ፡ ዕቅብት ፡ ወአ ንበረ ፡ ሕገ ፡ እሙስቦ ።

ስለ ፡ ስጦታ ። (ሁብት)

ን ፡ ለሌሎችም ፡ ዕቁባት ፡ ነበሩቸውሳ ፡ ብትል ፡ ልታውቅ ፡ ከወደድኽ ፡ ስማ ! በዚያ ፡ ዘመን ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ሰዎች ፡ ጥቂቶች ፡ ስለነበሩ ፡ ሰዎች ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ይበዙ ፡ ዘንድ ፡ ስለዚህ ፡ ሚስት ፡ እንዲያገቡ ፡ ዕቁባት ፡ እንዲኖሩ ፡ ተፈቀደላቸው ። ምድር ፡ እንደመላች ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ዕቁባትን ፡ ከማኖር ፡ ከልክሎ ፡ ሚስት ፡ የማግባትን ፡ ሕግ ፡ ሠራ ።

## አንቀጽ ፡ ፳ወ፯ቱ ።

### በእንተ ፡ ሀብት ።

፪፻፸ ወመብዝኀተኒ ፡ እመጽሐፈ ፡ ጠስ ፡ ፲ወ፪ቱ ፡ ፲ወ፫ቱ ፡ በእንተ ፡ ሀብታት ፡ ወከዋን ፡ ሀብታት ፡ ውእቱ ፡ ይከውን ፡ እምጽንዕ ፡ ገጻት ። ወውእቱ ፡ ሀብት ፡ ወወሀቢ ፡ መዘይሁብዎ ፡ ሎቱ ፡ ወንዋይኒ ፡ ዘያሁቡ ፡ ኪያሁ ፡ ወተረፈ ፡ ትእዛዝት ።

፪፻፸፩ ሀብትሰ ፡ ይደሉ ፡ ከመ ፡ የሀብዎሙ ፡ ለእለ ፡ ኢኮኑ ፡ ድልዋነ ፡ ለመጽጠውቶ ፡ ወምጽዋትኒ ፡ ትከውን ፡ ለዘይደልዎ ። ወሀብትሰ ፡ ምግባረ ፡ ትሩፋት ፡ ይእቲ ፡ ዘይደሉ ፡ ውሂቦታ ፡ እምድኅረ ፡ ምጽዋት ። ወእምከመ ፡ ወሀበ ፡ ወሃቢ ፡ ኪያሃ ፡ ወተወከፈ ፡ ዘይሁብዎ ፡ ሎቱ ፡ ንዋየ ፡ ዘትትወሀብ ፡ ወእምዝ ፡ ይደሉ ፡ ሎቱ ፡ ሥልጣን ፡ ላዕሌሁ ፡ ወይሥረቅ ፡ ቦቱ ፡ ከመ ፡ ወሀቢ ።

፪፻፸፪ ወለወሀቢኒ ፡ ኢትከውን ፡ እማን ፡ እምኔሁ ፡ ሀብት ፡ ለእመ ፡ ኢኮነ ፡ ብጹሐ ፡ እምዓን ፡ ወማእምረ ፡ ወእግዚኡ ፡ ውንሩየ ፡ በአልቦቱ ፡ ፍርሃት ፡ እምዝወሀበ ። ወእመሰ ፡ ዘይፈርሆ ፡ እምዘ ፡ ወሀበ ፡ ኢይትፌጸም ፡ ሎቱ ፡ ወእመኒ ፡ ሞተ ፡ ወሀቢሁ ፡ ኢይማባእ ፡ እምኔሃ ፡ በስምዕ ውኩፍ ፡ ኢበጎቡእ ፡ ወኢ ፡ በከሙት ።

፪፻፸፫ ወለወሀቢሰ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ የሀብ ፡ በሕይወቱ ፡ እመ ፡ ፈቀደ ፡ በጊዜሁ ፡ ዘእንበለ ፡ ውሳኔ ሰደሚ ። ወለእመ ፡ ፈቀደ ፡ እምድኅሬሁ ፡ በትእዛዝ ፡ ወበጊዜ ፡ እሙር ፡ ዘይመጽእ ፡ ወሎቱ ፡ ድልው ፡ ከመ ፡ ይግበር ፡ በጊዜ ፡ ሞቱ ፡ ተፍጻሚተ ፡ እምድኅረ ፡ ዕረፍቱ ።

## አንቀጽ ፡ ፳፯ ።

### ስለ ፡ ስጦታ ፡ ይናገራል ።

፪፻፸ አብዛኛውም ፡ ከጠስ ፡ መጽሐፍ ፡ የተገኘ ፡ ነው ። ጠስ ፡ ፲፪ ፡ ፲፫ ። ስለስጦታዎች ፡ ይናገራል ። የስጦታ ፡ ሁኔታ ፡ ከ፫ ፡ ወገን ፡ ነው ። እነዚህም ፡ ስጦታ ፡ ሰጪ ፡ ለእርሱ ፡ የሚሰጡት ሰው እርሱን የሚሰጡት ፡ ገንዘብ ፡ ከትእዛዝ ፡ የቀረውም ናቸው ።

፪፻፸፩ ስጦታስ ፡ ምጽዋት ፡ ለመስጠት ፡ ለማይችሉት ፡ ሰዎች ፡ ሊሰጡአቸው ፡ ይገባል ። ምጽዋትም ፡ ለሚገባው ፡ ትሆናለች ። ስጦታስ ፡ ከምጽዋት ፡ ቀጥሎ ፡ ሊሰጧት ፡ የሚገባ ፡ የትሩፋት ፡ ሥራ ፡ ናት ። ሰጪ ፡ እርሷን ፡ ከሰጠ ፡ የምትሰጠዋንም ገንዘብ ፡ የሚሰጡት ፡ ሰው ፡ ከተቀበለ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እንደሰጪው ፡ ይሠራበት ፡ ዘንድ ፡ በገንዘቡ ፡ ላይ ፡ ሥልጣን ፡ ሊኖረው ፡ ይገባል ።

፪፻፸፪ ሰጪውም ፡ እካለ ፡ መጠን ፡ ያደረሰ ፡ አዋቂ ፡ ራሱን ፡ የቻለ ፡ የተመረጠ ፡ ከሰጠው ፡ ገንዘብ ፡ የተነሣ ፡ ፍርሃት ፡ የሌለበት ፡ ካልሆነ ፡ ስጦታው ፡ የታመነች ፡ አትሆንም ። ከሰጠ ፡ በኋላ ፡ የሚፈራ ፡ ቢሆን ፡ ግን ፡ አይጸናለትም ። ሰጪው ቢሞትም ፡ በስውርም ፡ ቢሆን ፡ በግልጽ ፡ ስጦታው ፡ ተቀባዩንት ፡ ባለው ፡ ምስክር ፡ ከተረጋገጠ ፡ አይመለስ ።

፪፻፸፫ ለሰጪ ፡ ግን ፡ በሕይወት ፡ ሳለ ፡ ዘመን ፡ ሳይወስን ፡ በጊዜው ፡ ሊሰጥ ፡ ቢወድ ፡ መስጠት ፡ ይገባዋል ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በማዘዝና ፡ በሚመጣው በታወቀ ፡ ጊዜ ፡ ቢወድ ፡ ፍጻሜዋን ፡ በሞቱ ፡ ጊዜ ፡ ሊያደርግ ፡ ይገባዋል ።

### አንቀጽ ፡ ፳፮ ።

ወእመ ፡ ትቤ ፡ ከመ ፡ ለዳዊት ፡ ወለሰሎሞን ፡ ወለካልኣን ፡ ከና ፡ ሎሙ ፡ ዕቅብታት ፡ እመሰ ፡ ፈቀድከ ፡ ከመ ፡ ታእምር ፡ ስማዕኬ ፡ እስመ ፡ በውእቱ ፡ ዘመን ፡ ኮኑ ፡ ሰብእ ፡ ውኁዳን ፡ በዲበ ፡ ምድር ። በእንተ ፡ ዝንቱ ፡ ተበውሐ ፡ ሎሙ ፡ ከመ ፡ ያውስቡ ፡ ወያንብሩ ፡ ሎሙ ፡ ዕቅብታተ ፡ ከመ ፡ ይብዝኁ ፡ ሰብእ ፡ በዲበ ፡ ምድር ። ወሶበ ፡ በጽሐ ፡ ከመ ፡ ምድር ፡ መልእት ፡ ከልአ ፡ ሕግ ፡ እምነሢአ ፡ ዕቅብት ፡ ወአንበረ ፡ ሕገ ፡ አውስቦ ።

### ስለ ፡ ስጦታ ። (ሀብት)

ን ፡ ለሌሎችም ፡ ዕቁባት ፡ ነበሩባቸውላ ፡ ብትል ፡ ልታውቅ ፡ ከወደድኽ ፡ ስማ ! በዚያ ፡ ዘመን ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ሰዎች ፡ ጥቂቶች ፡ ስለነበሩ ፡ ሰዎች ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ ይበዙ ፡ ዘንድ ፡ ስለዚህ ፡ ሚስት ፡ እንዲያገቡ ፡ ዕቁባት ፡ እንዲኖሩ ፡ ተፈቀደላቸው ። ምድር ፡ እንደመላች ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ዕቁባትን ፡ ከማኖር ፡ ከልክሎ ፡ ሚስት ፡ የማግባትን ፡ ሕግ ፡ ሠራ ።

---

## አንቀጽ ፳ወ፯ቱ ።

### በእንተ ፡ ሀብት ።

፱፻፸ ወመብዝኅንቱኒ ፡ እመጽሐፈ ፡ ጠስ ፡ ፲ወ፪ቱ ፡ ፲ወ፫ቱ ፡ በእንተ ፡ ሀብታት ፡ ወከዊን ፡ ሀብታት ፡ ውእቱ ፡ ይከውን ፡ እምኔቱ ፡ ገጻት ። ወውእቱ ፡ ሀብት ፡ ወወሀቢ ፡ ወዘይትወሀብ ፡ ሎቱ ፡ ወንዋይኒ ፡ ዘይሁቡ ፡ ኪያሁ ፡ ወተረፈ ፡ ትእዛዝ ።

፱፻፸፩ ሀብትሰ ፡ ይደሉ ፡ ከመ ፡ የሀብዎሙ ፡ ለእለ ፡ ኢኮኑ ፡ ድልዋነ ፡ ለመጽውቶ ፡ ወምጽዋትኒ ፡ ትከውን ፡ ለዘይደልዎ ። ወሀብትሰ ፡ ምግባረ ፡ ትሩፋት ፡ ይእቲ ፡ ዘይደሉ ፡ ውሂቦታ ፡ እምድኅረ ፡ ምጽዋት ። ወእምከመ ፡ ወሀበ ፡ ወሃቢ ፡ ኪያሃ ፡ ወተወክፈ ፡ ዘይሁብዎ ፡ ሎቱ ፡ ንዋየ ፡ ዘትትወሀብ ፡ ወእምዝ ፡ ይደሉ ፡ ሎቱ ፡ ይኩልዎን ፡ ዓዕሲሁ ፡ ወይትረሐቅ ፡ ቦቱ ፡ ከመ ፡ ወሀቢሁ ።

፱፻፸፪ ወለወሀቢኒ ፡ ኢትከውን ፡ እማን ፡ እምኔሁ ፡ ሀብት ፡ ለእመ ፡ ኢኮነ ፡ ብጹሐ ፡ እምዓመ ፡ ወማእምረ ፡ ወእግዓዜ ፡ ወንዋየ ፡ በአልቦቱ ፡ ፍርሃት ፡ እምዘወሀበ ። ወእመሰ ፡ ዘይፈርህ ፡ እምዘ ፡ ወሀበ ፡ ኢይትፈጸም ፡ ሎቱ ፡ ወእመኒ ፡ ሞተ ፡ ወሀቢሁ ፡ ኢያግብእ ፡ እምኔሃ ፡ በሰምዕ ፡ ውኩፍ ፡ ኢበጎቡእ ፡ ወኢ ፡ በከሡት ።

፱፻፸፫ ወለወሀቢሰ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ የሀብ ፡ በሕይወቱ ፡ እመ ፡ ፈቀደ ፡ በጊዜሁ ፡ ዘእንበለ ፡ ውስኔ ፡ ዕድሜ ። ወለእመ ፡ ፈቀደ ፡ እምድኅሬሁ ፡ በትእዛዝ ፡ ወበጊዜ ፡ እሙር ፡ ዘይመጽእ ፡ ወሎቱ ፡ ይደልው ፡ ከመ ፡ ይግበር ፡ በጊዜ ፡ ሞቱ ፡ ተናጽሚተ ፡ እምድኅረ ፡ ዕረፍቱ ።

## አንቀጽ ፡ ፳፯ ።

### ስለ ፡ ስጦታ ፡ ይናገራል ።

፱፻፸ አብዛኛውም ፡ ከጠስ ፡ መጽሐፍ ፡ የተገኘ ፡ ነው ። ጠስ ፡ ፲፪ ፡ ፲፫ ። ስለስጦታዎች ፡ ይናገራል ። የስጦታ ፡ ሁኔታ ፡ ከ፫ ፡ ወገን ፡ ነው ። እነዚህም ፡ ስጦታ ፡ ሰጪ ፡ ለእርሱ ፡ የሚሰጡት ፡ ሰው ፡ እርሱን ፡ የሚሰጡት ፡ ገንዘብ ፡ ከትእዛዝ ፡ የቀረውም ፡ ናቸው ።

፱፻፸፩ ስጦታስ ፡ ምጽዋት ፡ ለመስጠት ፡ ለማይችሉት ፡ ሰዎች ፡ ሊሰጡአቸው ፡ ይገባል ። ምጽዋትም ፡ ለሚገባው ፡ ትሆናለች ። ስጦታስ ፡ ከምጽዋት ፡ ቀጥሎ ፡ ሊሰጧት ፡ የሚገባ ፡ የትሩፋት ፡ ሥራ ፡ ናት ። ሰጪ ፡ እርሷን ፡ ከሰጠ ፡ የምትሰጠዋንም ፡ ገንዘብ ፡ የሚሰጡት ፡ ሰው ፡ ከተቀበለ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እንደሰጪው ፡ ይሠራበት ፡ ዘንድ ፡ በገንዘቡ ፡ ላይ ፡ ሥልጣን ፡ ሊኖረው ፡ ይገባል ።

፱፻፸፪ ሰጪውም ፡ እካለ ፡ መጠን ፡ ያደረሰ ፡ እዋቂ ፡ ራሱን ፡ የቻለ ፡ የተመረጠ ፡ ከሰጠው ፡ ገንዘብ ፡ የተነሣ ፡ ፍርሀት ፡ የሌለበት ፡ ካልሆነ ፡ ስጦታው ፡ የታመነች ፡ አትሆንም ። ከሰጠ ፡ በኋላ ፡ የሚፈራ ፡ ቢሆን ፡ ግን ፡ አይጸናለትም ። ሰጪው ፡ ቢሞትም ፡ በሰውርም ፡ ቢሆን ፡ በግልጽ ፡ ስጦታው ፡ ተቀባዩንት ፡ ባለው ፡ ምስክር ፡ ከተረጋገጠ ፡ አይመለስ ።

፱፻፸፫ ለሰጪ ፡ ግን ፡ በሕይወት ፡ ሳለ ፡ ዘመን ፡ ሳይወስን ፡ በጊዜው ፡ ሊሰጥ ፡ ቢወድ ፡ መስጠት ፡ ይገባዋል ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በማዘዝና ፡ በሚመጣው ፡ በታወቀ ፡ ጊዜ ፡ ቢወድ ፡ ፍጻሜዋን ፡ በሞቱ ፡ ጊዜ ፡ ሊያደርግ ፡ ይገባዋል ።

አንቀጽ ፡ ፳፪ ።

ስለ ፡ ስጦታ ። (ሀብት)

፪፻፹፬ ወነገሩ ፡ እምኔሆሙ ፡ ዘኢየአኩት ፡ ወሃቢሁ ፡ አላ ፡ የሐውር ፡ ኀበ ፡ እደ ፡ ገጽ ፡ እምገጸ ፡ ሕሠም ፡ ወእንዘ ፡ እዴሁ ፡ ላዕሌሁ ፡ በኀመቅ ፡ ወእከይ ፡ ወጕሕሉት ፡ ወእንጕሉ ፡ ኀጕለ ፡ ሀቢየ ፡ እምእስተዋድዮቱ ፡ ለንዋእ ፡ ንዋዩ ፡ እሙ ፡ ገብረ ፡ በዘያማስን ፡ ሕይወቶ ፡ እው ፡ ኀደገ ፡ እምዘ ፡ ኮነ ፡ ተሰናእዎቶሙ ፡ ላዕሌሁ ፡ በትድኅሙ ፡ ስማዕት ፡ በምንትኒ ፡ እምነሉ ፡ ዘወሀበ ፡ ሎቱ ፡ ወእምከመ ፡ ተዐውቀ ፡ ከሙቱ ፡ በመንበረ ፡ ፍትሕ ፡ ወተጠየቀ ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡ ገብረ ፡ እሐተ ፡ እምነ ፡ እሉ ፡ ምግባራት ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ የግብእ ፡ ሀብቶቱ ፡ ዘእንበለ ፡ ተውላጥ ፡ ለእመ ፡ ሀለዋ ፡ እው ፡ ሤጠ ፡ ዚአሆን ፡ ለእመ ፡ ኢሀለዋ ፡ ወለእመ ፡ ኢነበሩ ፡ በምሳሌ ፡ ሤጥ ፡ ይኩን ፡ በከመ ፡ ቃሉ ፡ ለዘወሀቦ ፡ ሎቱ ፡ ለእመ ፡ ኢተንሥአ ፡ ቃለ ፡ ስምዕ ፡ ላዕሌሁ ፡ ዘያበጥል ፡ ቃሎ ።

፪፻፹፬ ከእነርሱም ፡ ወገን ፡ ሰጭውን ፡ የሚያመሰግን ፡ ሁሉ ፡ ከክፋት ፡ ወገን ፡ ወደማናቸውም ፡ የክፋት ፡ ወገን ፡ የሚሄድ ፡ በበደል ፡ በክፋቱ ፡ በተንኮል ፡ እጁን ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ የእንግ ፡ ገንዘቡን ፡ ለመውሰድ ፡ አንገር ፡ ሥራው ፡ የተነሣ ፡ ታላቅ ፡ ጥፋት ፡ ያጠፋው ፡ ወይም ፡ ሕይወቱ ፡ የሚጠፋበትን ፡ ሥራ ፡ ቢሠራ ፡ ወይም ፡ ከሰጠው ፡ ገንዘብ ፡ ሁሉ ፡ በማናቸውም ፡ ነገር ፡ በምስክሮች ፡ ፊት ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ የሆነውን ፡ ስምምነት ፡ የተወ ፡ (ያፈረሰ) ፡ በፍርድ ፡ አደባባይ ፡ በግልጽ ፡ ከታወቀ ፡ ከእነዚህም ፡ ሥራዎች ፡ አንዱቱን ፡ መሥራቱ ፡ ከተረጋገጠ ፡ ቢኖሩ ፡ ያለ ፡ ለውጥ ፡ ስጦታዎቹን ፡ ወይም ፡ ባይኖሩ ፡ ዋጋቸውን ፡ ይመልስለት ፡ ዘንድ ፡ ይገባዋል ። በዋጋው ፡ እምሳይ ፡ ባይስማሙ ፡ ቃሉን ፡ የሚያፈርስበት ፡ የምስክር ፡ ቃል ፡ ካልተነሣበት ፡ በቀር ፡ እንደሰጪው ፡ ቃል ፡ ይሁን ።

፪፻፹፭ ወለእመኒ ፡ ይቤ ፡ ዘወሀብዎ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ጽኑስ ፡ ውእቱ ፡ እልቦ ፡ ዘያክልእ ፡ ኀሠሣሁ ፡ ዘእንበለ ፡ በስምዕ ፡ ዘያፀርዕ ፡ ኀሠሣሁ ።

፪፻፹፭ የሰጡት ፡ ሰው ፡ ችጋረኛ ፡ እንደሆነ ፡ ቢናገርም ፡ ፍላጎቱን ፡ ከሚያስቀር ፡ ምስክር ፡ በቀር ፡ ፍላጎቱን ፡ የሚከለክል ፡ የለም ።

፪፻፹፮ ወኢይቀውም ፡ ሀብት ፡ ለዘይሁብዎ ፡ ዘእንበለ ፡ ለዘቦቱ ፡ ጥሪት ፡ ወኢትትፈጸም ፡ ዘእንበለ ፡ ሶበ ፡ ይትዌከፉ ። ወንዋይኒ ፡ ዘይትወሀብ ፡ ኢይደሉ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ዘኢይትዐወቅ ፡ ወኢእምዘ ፡ ኢይከውና ፡ ለወሃቢ ፡ ምልክናሁ ።

፪፻፹፮ ስጦታ ፡ ለሚሰጡት ፡ ሰው ፡ ገንዘብ ፡ ላለው ፡ ሰው ፡ ካልሆነ ፡ አይጸናም ። በሚቀበላትም ፡ ጊዜ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ አትፈጸምም ። የሚሰጠውም ፡ ገንዘብ ፡ ያልታወቀ ፡ ሊሆን ፡ አይገባም ። ለሰጪ ፡ ከማያዝዝበትም ፡ ወገን ፡ ሊሆን ፡ አይገባም ።

፪፻፹፯ ወኢይኩን ፡ እንከ ፡ እምነ ፡ ዘተመውዐ ፡ ቦቱ ፡ ሕሊናሁ ፡ እስመ ፡ ዘይሁብዎ ፡ ኪያሁ ፡ ይበውእ ፡ ውስተ ፡ ልቡ ፡ ፍቅረ ፡ ንዋይ ፡ ወእመ ፡ አኮ ፡ ያደውዮ ፡ በውእቱ ፡ ጊዜ ፡ ከመ ፡ ዘይሁብ ፡ ሰይፈ ፡ ለዘእኀዞ ፡ ጋኔን ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ከመ ፡ ቦ ፡ ዘይቀትል ፡ ቦቱ ፡ ነፍሶ ፡ እው ፡ ነፍሰ ፡ ካልኡ ።

፪፻፹፯ እንግዲህ ፡ ልቡናው ፡ ድል ፡ ከሚነሣበት ፡ ወገን ፡ አይሁን ፡ እርሱን ፡ የሚሰጡት ፡ ሰው ፡ በልቡ ፡ ፍቅረ ፡ ንዋይ ፡ ያድርበታልና ። ይህም ፡ ባይሆን ፡ ወዲያው ፡ ያስምመዋል ። ጋኔን ፡ ለያዘው ፡ ሰው ፡ ሰይፍ ፡ እንደመስጠት ፡ ነው ። ነፍሱን ፡ ወይም ፡ የሌላውን ፡ ነፍስ ፡ እንደሚገድል ፡ ያለ ፡ ነውና ።

፪፻፹፰ ወእመሰ ፡ ኮነ ፡ ንዋይ ፡ ዘተውህበ ፡ ኢይትፈለጥ ፡ ለተፈቅዶ ፡ ወኢበውሂብ ፡ ከመ ፡ ዘዲናራት ፡ ወጠፋልሐ ፡ ብሩር ፡ ኢይትፈቀድ ፡ ኀበ ፡ ጽሒፍ ፡ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ እሙረ ፡ ለዝንቱስ ፡ ይኩን ፡ ጽሒፈተ ፡ ዚአሁ ። ወበእንቲአሁ ፡ ይደሉ ፡ ጽሒፈተ ፡ ስማዕት ፡ ዘያዜክሩ ፡ ባቲ ፡ ፍቅደ ፡ ንዋይ ፡ ዘይትወሀብ ፡ ወከዋኔ ፡ እርእያሁ ፡ ወያቱ ፡ ትእዛዛቲሁ ፡ ለወሃቢ ፡ በእንቲአሁ ወከመ ፡ ውእቱ ፡ ኢይገብእ ፡ እምዘወሀበ ፡ ይደልው ፡ ከመ ፡ ይጽሐፍ ፡ ትእዛዘ ፡ በእንቲአሁ ።

፪፻፹፰ የተሰጠው ፡ ገንዘብ ፡ በቍጥር ፡ የማይለይ ፡ ወይም ፡ በመስጠት ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ዲናርና ፡ እንደተመዘነ ፡ ብር ፡ ያለ ፡ ቢሆን ፡ ሊጽፍ ፡ አያስፈልግም ። የታወቀ ፡ ቢሆን ፡ ይህንስ ፡ ሊጽፉት ፡ ይገባል ። የሚሰጠውን ፡ የገንዘብ ፡ ቍጥር ፡ የመልኩን ፡ ሁኔታ ፡ ስለእርሱም ፡ የሰጪን ፡ የትእዛዝ ፡ ስልት ፡ እርሱን ፡ የሚያስረዱ ፡ ምስክሮችን ፡ ስለእርሱ ፡ መጻፍ ፡ ይገባል ። እርሱም ከሰጠ ፡ በኋላ ፡ እንዳይመለስ ፡ ስለእርሱ ፡ ትእዛዙን ፡ ይጽፍ ፡ ዘንድ ፡ ይገባዋል ።

፱፻፹፭ ወለእመ ፡ ኮነት ፡ ዘተውህበት ፡ ሀገር ፡ ይእቲ ፡ ወእክል ፡ ዘትትጋባእ ፡ እምኔሃ ፡ ይእቲ ፡ ትደሉ ፡ ለዘውሁብ ፡ሎቱ ፡ እምእመ ፡ ተጽሕፈ ፡ ሎቱ ፡ መጽሐፍ ፡ ወተመጠወ ፡ ኪያሁ ፡ ለእመ ፡ ኢተእዘዘ ፡ ላዕሌሁ ፡ ካልእ ፡ እምዘ ፡ ተጽሕፈ ። ወእመሰ ፡ ተእዘዘ ፡ እክል ፡ ዘሀለወት ፡ ኢትኩን ፡ ሎቱ ፡ እላ ፡ ይሰደድ ፡ እምፍጻሜ ፡ ሀብት ፡ ወእመ ፡ ተወክፈ ፡ ውእቱ ፡ ዘውሁብ ፡ ሎቱ ፡ ይኩውን ፡ ግብር ፡ ከመዝ ። ወተረፈ ፡ ትእዛዛትሂ ፡ እስመ ፡ ኢይትኤዘዝ ፡ ዘይትዐደው ፡ ፍጻሜ ፡ ሀብት ።

፱፻፹፮ ወእመ ፡ ወሀበ ፡ ፩ዱ ፡ ለመኑሂ ፡ ምንተኒ ፡ ንዋየ ፡ መዋተ ፡ እምቅድመ ፡ ብጽሐቱ ፡ ኀቤሁ ፡ ኢይደልዎሙ ፡ ለወራስያኒሁ ፡ ከመ ፡ ይሰድዎ ።

፱፻፹፯ ወለእመኒ ፡ ወሀበ ፡ ዘሀሎ ፡ ታሕተ ፡ ሐፃኒት ፡ በትእዛዘ ፡ እቡሁ ፡ እው ፡ በትእዛዘ ፡ ርእሱ ፡ መጠነ ፡ ውእቱ ፡ ሀብት ፡ ይኩን ፡ ለአብ ። ወዘ ወሀበሂ ፡ ለብእሲ ፡ ንዋየ ፡ በፈቃዱ ፡ በዓለ ፡ ንዋይ ፡ ውእቱ ፡ ወሃቢሁ ።

ስለ ፡ ብድር ።

፱፻፹፭ የተሰጠችው ፡ ሀገር ፡ (መሬት) ፡ ብትሆን ፡ እሀልም ፡ ከእርሷ ፡ የሚገኝባት ፡ ብትሆን ፡ ደብዳቤ ፡ ከተጻፈለትና ፡ እርሱን ፡ ከተቀበለበት ፡ ጊዜ ፡ ጀምሮ ፡ ለተሰጠው ፡ ሰው ፡ ትገባለች ። ከተጻፈው ፡ ሌላ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ካልታዘዘ ፡ ያለችው ፡ እህል ፡ ብትታዘዝለት ፡ ግን ፡ (መሬቱ) ፡ ለእርሱ ፡ አትሁን ። ከፍጹም ፡ ስጦታ ፡ ይለይ ፡ እንጂ ። እርሱ ፡ የተሰጠውን ፡ ቢቀበል ፡ ግድ ፡ እንደዚሁ ፡ ይሆናል ። ከትእዛዛት ፡ የቀረውም ፡ የስጦታን ፡ ፍጻሜ ፡ የሚተላለፍ ፡ አይታዘዝምና ።

፱፻፹፮ አንዱ ፡ ሰው ፡ ለማንም ፡ ማናቸውንም ፡ ገንዘብ ፡ ቢሰጥ ፡ ወደ ፡ እርሱም ፡ ከመድረሱ ፡ በፊት ፡ ቢሞት ፡ ወራሾቹ ፡ ሊመልሱት ፡ አይገባቸውም።

፱፻፹፯ በሞግዚት ፡ ስር ፡ ያለ ፡ በአባቱ ፡ ትእዛዝ ፡ ወይም ፡ በራሱ ፡ ትእዛዝ ፡ ገንዘብ ፡ ቢሰጥ ፡ ስጦታውን ፡ መመጠን ፡ ለአባት ፡ ይሁን ። በፈቃዱ ለሰው ፡ ገንዘብን ፡ የሰጠ ፡ ሰው ፡ ሰጪው ፡ ባለ ገንዘቡ ፡ ነው ።

## አንቀጽ ፴ወ፰ቱ ።

በእንተ ፡ ሊቃሕ ፡ ወእጎዝ ፡ ወተሐብዮ ፡ ወምግብና ።

፱፻፹፰ ሊቃሕሰ ፡ ሀብት ፡ ይእቲ ፡ እምእዝማዲሃ ፡ ለምጽዋት ፡ ዘእዘዘ ፡ ባቲ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወከልእ ፡ ከመ ፡ ኢይእበዩ ፡ ኪያሃ ፡ በቃሉ ፡ ዘውስተ ፡ ወንጌል ፡ ዘይቤ ፡ ለቅሉ ፡ ወኢትምትሩ ፡ ተሰፋሁ ፡ ለ፩ዱሂ ፡ ወብሂሎቱኒ ፡ ለዘፈቀዶ ፡ ይትሊቃሕ ፡ እምኔከ ፡ ኢትክልኦ ።

፱፻፹፱ ወእስተሐምሞሂ ፡ በእንተ ፡ ፈድዮ ፡ ሊቃሕ ፡ ድልው ፡ ውእቱ ፡ ወፈድዮቱኒ ፡ በጊዜ ፡ ዘይትከሀሎ ፡ ሕግ ፡ ውእቱ ፡ በከመ ፡ ይቤ ፡ ዳዊት ነቢይ ፡ "ይትሊቃሕ ፡ ኃጥእ ፡ ወኢይፈዲ ፡ ጻድቅሰ ፡ ይምሕር ፡ ወይሁብ" ። ወተዓግሦ ላዕለ ፡ ተሊቃሒ ፡ እስከ ፡ ይረክብ ፡ ዘይፈድዮ ፡ ድልው ፡ ውእቱ ፡ ሎቱ ፡ በከመ ፡ ይቤ ፡ እግዚአብሔር ፡ ኢትትኀወሥ ፡ እምዘ ፡ ይነሥእ ፡ ንዋየከ ፡ ወኢታግብር ፡ በእንተ ፡ ግብረ ፡ ተጽናሱ ። ወእንበረ ፡ በእንቲአሁ ፡ ምሳሌ ፡ እግዚእነ ፡ በገብር ፡ ዘአገበሮ ፡ ለበዓለ ፡ ዕዳሁ ።

## አንቀጽ ፡ ፴፰ ።

ስለ ፡ ብድር ፡ ስለ ፡ መያዣ ፡ ስለ ፡ ዋስትና ፡ ስለ ፡ አስተዳዳሪነት ፡ ይናገራል ።

፱፻፹፰ ብድርስ ፡ እግዚአብሔር ፡ እርሷን ፡ ከዘዛት ፡ ከምጽዋት ፡ ወገን ፡ የምትሆን ፡ ስጦታ ፡ ናት ። አበድሩ ፡ የእንዱንስ ፡ እንኳ ፡ ተስፋ ፡ አትቍረጡ ፡ ብሎ ፡ በወንጌል ፡ በተናገረው ፡ ቃሉ ፡ እርሷን ፡ እንቢ ፡ እንዳይል ፡ ከለከለ ። ከእንተ ፡ ሊበደር ፡ የሚሻውንም ፡ አትከልክለው ፡ በማለቱ ። (ማቴ ፡ ፭ ፡ ፵፪) ።

፱፻፹፱ ብድርንም ፡ ስለመክፈል ፡ መትጋት ፡ ተገቢ ፡ ነው ። በሚቻልበትም ፡ ጊዜ ፡ መክፈል ፡ ሕግ ፡ ነው ። ኃጥእ ፡ ተበድሮ ፡ አይከፍልም ። ጻድቅ ፡ ግን ፡ ይራራል ፡ ይሰጣልም ፡ ብሎ ፡ ነቢይ ፡ ዳዊት ፡ እንደተናገረ ። (መዝ ፡ ፴፮ ፡ ፳፩) ፡ የሚከፍለው ፡ እስኪያገኝ ፡ ድረስ ፡ በተበዳሪ ፡ ላይ ፡ መታገሥ ፡ ለአበዳሪ ፡ ይገባዋል ። ገንዘብህን ፡ ከወሰደ ፡ ሰው ፡ አትፈላግ ፡ ስለችግሩም ፡ አታስገድደው ፡ ብሎ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደተናገረ ። (ዘዳ ፡ ፲፭ ፡ ፪) ። ስለዚህም ፡ ጌታችን ፡ ባለዕዳውን ፡ ባስገደደው ፡ ባሪያ ፡ ምሳሌ ፡ ተናገረ ። (ማቴ ፡ ፲፰ ፡ ፳፫ - ፴፭) ።

## እንቀጽ ፡ ፵፮ ።

፱፻፶ ወሊቃሕስ ፡ ይደሉ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ በእኅዝ ፡ እው ፡ በትሕቢት ፡ እው ፡ በመድኀን ፡ እው ፡ በመጽሐፍ ፡ እንተ ፡ ውስቴታ ፡ ሰማዕት ። ወሶቤሁ ፡ ያብቍዕ ፡ በእንቲአሃ ፡ ጽሕፈተ ፡ እደዊሁ ፡ ለዘተለቅሐ ፡ እው ፡ በዘይቀውም ፡ ላዕለ ፡ እሚኖቱ ፡ ባሕቲቱ ፡ ወሰማዕታት ፡ ድልው ፡ በጽሕፈት ። ወይኩን ፡ ፍጡነ ፡ እው ፡ በሰድሚ ፡ ወፈድዮ ፡ ሊቃሕስ ፡ ይደሉ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ በጊዜሁ ፡ እመ ፡ ተኀሥሠ ፡ ወይደሉ ፡ ዓዲ ፡ ቅድመ ፡ ተኀሥሠ ፡ ጊዜ ፡ ተከህሎ ።

፱፻፶፩ ወይኩን ፡ እምንዋዩ ፡ ሊቃሕ ፡ እው ፡ እምኀጢ ፡ በጊዜ ፡ ፈድዮ ፡ ዘተክህሎ ፡ እምአሐዱ ፡ እምተ ለቅሖት ፡ እው ፡ እምግብር ፡ ካልእ ፡ ኅጡ ፡ ዚአሁ ፡ ጊዜ ፡ ፈድዮ ፡ መጠነ ፡ ሊቃሕ ። ወለ እመ ፡ ተገብረ ፡ በበይነ ፡ ዝንቱ ፡ ትእዛዝ ፡ ይትገበር ፡ ከማሁ ። ወለእመ ፡ ይቤ ፡ ተለቃሒ ፡ ኀጣእኩ ፡ ክሂለ ፡ በእንተ ፡ ፈድዮ ፡ ዕዳ ፡ ይደሉ ፡ ለለቃሒ ፡ ከመ ፡ ይንሣእ ፡ እምዘ ፡ ረከበ ፡ እምንዋዩ ፡ በትእዛዘ ፡ ፈታሒ ፡ ወበዘሠርዑ ፡ ውእቱ ፡ ሰብእ ፡ ምእመናን ፡ በፍትሕ ፡ ወበሐሳብ ፡ ለእመ ፡ ኀረየ ፡ ዝንቱ ፡ ተለቃሒ ፡ ወእመኒ ፡ ኢኀረየ ፡ ወለእመ ፡ ክሕደ ፡ ተለቃሒ ፡ ዘቦ ፡ ላዕሌሁ ፡ ዕዳ ፡ ውተከሥተ ፡ እምድኅረ ፡ ዝንቱ ፡ መጽሐፈ ፡ ሰምዐ ፡ ዘያርር ፡ ኢይደሉ ፡ ይትኄለቁ ፡ ሎቱ ፡ ከዊኖ ፡ አላ ፡ ይንሥእ ፡ ኵሎ ፡ እምኔሁ ።

፱፻፶፪ ወዘሂ ፡ ክሕዶ ፡ ለበዓለ ፡ ዕዳሁ ፡ በዘዐለወ ፡ ላዕሌሁ ፡ ወመሐለ ፡ ሎቱ ፡ ወእመ ፡ ቆመ ፡ ሰማዕ ታት ፡ ላዕሌሁ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይፍዲ ፡ ህየ ንተ ፡ ዝንቱ ፡ ምክዕቢተ ። ወእመሰ ፡ እምነ ፡ በጊዜ ፡ መሐላ ፡ እምድኅረ ፡ ክሕደ ፡ ድኅነ ፡ እምተኀሥሦተ ፡ ምክዕቢት ። ወዘሂኒ ፡ በነ ሢአ ፡ አኀዘ ፡ ሰበ ፡ ኮነ ፡ እምዘ ፡ ቦቱ ፡ ዓስብ ፡ ወፃዕረ ፡ ሆሎ ፡ ዘበጽሐ ፡ ኀበ ፡ እደዊሁ ፡ ለለ ቃሒ ፡ በእንተ ፡ ዝንቱ ፡ ይደሉ ፡ ይትኌለቍ ፡ ላዕሌሁ ፡ በእምነት ፡ ዕዳሁ ።

፱፻፶፫ ወበእንተ ፡ ርሁስ ፡ ይደልወነ ፡ ከመ ፡ ንርኅቅ ፡ እምኔሁ ፡ እስመ ፡ ሕግ ፡ እምላከነ ፡ ናሁ ፡ ከልአ ፡ እምኔሁ ፡ ወለእመ ፡ ነሥአ ፡ ፩ዱሂ ፡ ንዋየ ፡ በምንትኒ ፡ ግብር ፡ እምግብራት ፡ ወው እቱ ፡ ይከውን ፡ እምነ ፡ ሊቃሕ ፡ ወለእመ ፡ ተፈድየ ፡ እምበዓለ ፡ ዕዳሁ ፡ ይደልዎ ፡ እግብ አተ ፡ አኀዘ ፡ ኀበ ፡ በዓለ ፡ ዚአሁ ። ወለእመ ፡

## ስለ ፡ ብድር ።

፱፻፶ ብድርስ ፡ በመያዣ ፡ ወይም ፡ በዋስትና ፡ ወይም ፡ በመድኅን ፡ ወይም ፡ ምስክሮች ፡ ባሉበት ፡ ጽሑፍ ፡ ሊሆን ፡ ይገባል ። የተበዳሪ ፡ የእጅ ፡ ጽሕፈት ፡ እነዚ ፡ ስለእርሱ ፡ ይጠቅማል ። ወይም ፡ በመተማመን ፡ ብቻ ፡ በሚጸና ፡ ገን ዘብ ፡ ነው ። ምስክሮችም ፡ ሊጻፉ ፡ ይገባል ። ፈጥኖ ፡ ወይም ፡ በቀጠሮ ፡ ይሁን ፡ ብድር ፡ መክፈልስ ፡ በተፈለገ ፡ ጊዜ ፡ ሊሆን ፡ ይገባል ። ዳግመኛም ፡ በተቻለው ፡ ጊዜ ፡ ከፍላጎቱ ፡ አስ ቀድሞ ፡ መክፈል ፡ ይገባል ።

፱፻፶፩ ከብድር ፡ ገንዘብ ፡ ወይም ፡ ከእንርሱ ፡ ወገን ፡ ከብድር ፡ የተቻለውን ፡ በመክፈል ፡ ጊዜ ፡ ከዋ ጋው ፡ ወይም ፡ በብድሩ ፡ ልክ ፡ በሚከፍል በት ፡ ጊዜ ፡ ከሌላው ፡ ሥራ ፡ ከዋጋው ፡ ይሁን ። ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ውል ፡ ቢደረግ ፡ እንደዚሁ ፡ ይሁን ። ተበዳሪ ፡ ብድሩን ፡ ስለመክፈል ፡ ችሎታ ፡ አጣሁ ፡ ቢል ፡ በዳኛ ፡ ትእዛዝ ፡ ምእ መናን ፡ ሰዎችም ፡ በፍርድና ፡ በግምት ፡ በወ ሰኑ ፡ ገንዘብ ፡ ተበዳሪ ፡ ቢወድም ፡ ባይወ ድም ፡ ካገኘው ፡ ከገንዘቡ ፡ ይቀበል ፡ ዘንድ ፡ ለአበዳሪ ፡ ይገባዋል ። ተበዳሪ ፡ ያለበትን ፡ ዕዳ ፡ ቢክድ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የያዘው ፡ የምስ ክር ፡ ደብዳቤ ፡ ቢመሰክርበት ፡ እርሱን ፡ ከቁ ጥር ፡ ሊያገቡለት ፡ አይገባም ። ሁሉን ፡ ከእርሱ ፡ ይውሰዱ ፡ እንጂ ።

፱፻፶፪ ስለ ፡ እለበት ፡ ዕዳ ፡ ባለዕዳውን ፡ የካደ ፡ ቢም ልለትም ፡ ምስክሮች ፡ ቢመሰክሩበትም ፡ ስለ ዚህ ፡ ባጠፋው ፡ ሊከፍል ፡ ይገባዋል ። ከካደ ፡ በኋላ ፡ በመሐላ ፡ ጊዜ ፡ ቢያምን ፡ ግን ፡ እጠ ፊው ፡ ከመክፈል ፡ ዳነ ። መያዣ ፡ በመያዝ ፡ የሆነውም ፡ ዋጋና ፡ ፍሬ ፡ ካለው ፡ ወገን ፡ ቢሆን ፡ በአበዳሪ ፡ እጅ ፡ የደረሰው ፡ ሁሉ ፡ ስለ ዚህ ፡ በዕዳው ፡ ሊቆጠር ፡ ይገባል ።

፱፻፶፫ ስለ ፡ አራጣ ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡ ልንርቅ ፡ ይገ ባናል ። አምላካዊ ፡ ሕግ ፡ ከእርሱ ፡ ከልክሎ ልና ፡ እንድ ፡ ሰው ፡ እንኳ ፡ ከሥራ ፡ በማናቸውም ፡ ሥራ ፡ ገንዘብ ፡ ቢቀበል ፡ እርሱ ፡ ከብድሩ ፡ ወገን ፡ ይሆናል ። ከበዓለ ፡ ዕዳው ፡ ቢቀበል ፡ መያ ዣውን ፡ ለባለቤቱ ፡ መመለስ ፡ ይገባዋል ። በብድሩ ፡ ላይ ፡ ቢጨምርም ፡ ጭማሪውን ፡

ጐለቶ ፡ ይለወ ፡ ከመ ፡ የሀብ ፡ ዘየንቲሁ ፡ ሚጠ
ዚአሁ ፡ አው ፡ ፈድየ ፡ ለቃሕ ፡ ወለእመ ፡ ኮነ ፡
ዕሉስ ፡ ዘኢይትከሀሎ ፡ ፈድዮ ፡ ግዕዛን ፡ ወኢ ፡
ዘምጽዋት ፡ ወኢ ፡ ዘጐልት ፡ ዘእንበለ ፡ እምድ
ኅረ ፡ ፈድየ ፡ ለቃሕ ፡ ኢይደሉ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡
ይሥራዕ ፡ ዓዕለ ፡ አኀዝ ፡ በዘይበቍዕ ፡ በቍዔተ
ለቃሒ ፡ በጊዜሁ ፡ ዘከመ ፡ ሚጥ ፡ ወሀብት ፡
ወእመ ፡ አኮ ፡ በዘየሐጽጽ ፡ አኀዝ ፡ ከመ ፡
ንግሥት ፡ ሐበር ፡ ወይደሉ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ይር
ከብ ፡ በቍዔተ ፡ ቦቱ ፡ በዘኢይረከቦ ፡ ሕሠም ፡
ለአኀዝ ፡ ዘከመ ፡ ፍሬያቲሁ ፡ ወተዋልዶቱ ፡
ወተዓስቦት ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ ተዓስቦቱ ፡ ካልእ ፡
እምነ ፡ ዕድሜሁ ፡ ለለቃሕ ፡ ዘእንበለ ፡ እመ ፡
ተወሰነ ፡ ዝንቱ ።



ተው ፡ ወይም ፡ ቢጐልተው ፡ ስለእርሱ ፡ ፈንታ፡
ዋጋውን ፡ ሊሰጥ ፡ ወይም ፡ ብድሩን ፡ መክፈል ፡
ይገባዋል ። ነፃ ፡ የወጣውን ፡ የተመጸወተው
ንም ፡ የተጐለተውንም ፡ ብድርን ፡ ከመክፈል ፡
በኋላ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ መክፈል ፡ የማይቻለው
ድን ፡ ቢሆን ፡ በጊዜው ፡ ያበዳሪ ፡ ጥቅም ፡ ስለ
ሚጠፋ ፡ በመያዣው ፡ ሊሠራበት ፡ አይገባ
ውም ። ይኸውም ፡ እንደዋጋ ፡ እንደ ፡ ስጦታ ፡
ያለ ፡ ነው ። ያም ፡ ባይሆን ፡ መያዣ ፡ በሚጐ
ድል ፡ ገንዘብ ፡ እጥርን ፡ እንደማፍረስ ፡ ነው ።
መያዣውን ፡ ጉዳት ፡ በማያገኘው ፡ ገንዘብ ፡
በእርሱ ፡ ጥቅም ፡ ያገኝበት ፡ ዘንድ ፡ ይገባ
ዋል ። ይኸውም ፡ እንደፍሬው ፡ እንደመ
ዋለዱ ፡ እንደ ፡ ኪራዩ ፡ ነው ። ኪራዩ ፡ ከብድሩ፡
ጊዜ ፡ ሌላ ፡ ቢሆን ፡ ይዞ ፡ በተወሰነበት ፡ ጊዜ ፡
ነው ፡ እንጂ ።

፱፻፺፱ ወኢይደሉ ፡ ከመ ፡ ይረስዮ ፡ አኀዝ ፡ ዘኢይትሜጣ
ሜጠ ፡ ዘከመ ፡ ግብር ፡ ግዑዝ ፡ ወከመ ፡ ቤት ፡
ዘጐለቶ ፡ ኪያሁ ፡ ለካልእ ፡ መዘፍጠኑ ፡ ይማስን
እምቅድመ ፡ ዕድሜሁ ፡ ለፈድየ ፡ ለቃሕ ።
ወእመ ፡ ተሣአሉ ፡ ክልኤሆሙ ፡ በእንተ ፡ ተወ
ልጦተ ፡ አኀዝ ፡ ይኩን ፡ በከመ ፡ ቃሉ ፡ ለእ
ኀዚ ፡ ምስለ ፡ መሐላሁ ። ወለእመ ፡ ይቤ ፡ ከመ፡
ውእቱ ፡ አግብአ ፡ ኀበ ፡ እግዚኡ ፡ ኢይትወ
ከፉ ፡ ቃሉ ፡ ወእመኒ ፡ ፈድፈደ ፡ ንዋየ ፡ አኀዝ፡
እምድኅረ ፡ አኀዘ ፡ ኢይኅሥእ ፡ እምአዴሁ ፡ ለዘ
አኀዘ ። እመኒ ፡ ኮሎንታሁ ፡ ወኢመንፈቁ ።
ወለእመ ፡ ተሰነአወ ፡ ከመ ፡ የሀሉ ፡ ውስተ ፡
እደ ፡ ዘአኀዘዎ ፡ አው ፡ ውስተ ፡ ፩ዱ ፡ ምእ
መን ፡ ይደሉ ፡ ላዕሌሁ ፡ ከመ ፡ ይግበር ፡ ቦቱ ፡
በከመ ፡ ፈጸሙ ፡ ተሰናእዎ ፡ ዓዕለ ፡ ዘተወሰነ።
ወኢይደሉ ፡ ከመ ፡ ይኩኑ ፡ ለቃሒ ፡ ወተለቃሒ
ወዘተአመንዎሙ ፡ ሥሉጣነ ፡ ዓዕለ ፡ አኀዝ ፡ ዘእ
ንበለ ፡ ዘከመ ፡ ይደሉ ፡ ሥርዓቱ ። ወፍትሐ ፡
ወራሲሁ ፡ ለእኂዜ ፡ አኀዝ ፡ ወለዘሂ ፡ ተለቅሐ ፡
እምድኅረ ፡ ሞቶሙ ፡ ውእቱ ፡ ወከማሁ ፡ እለ ፡
ጸሐፉ ፡ ሎሙ ፡ በኀሒፈ ፡ ትእዛዝ ፡ በእንተ ፡
አኀዝ ፡ ወእለሂ ፡ አኮንንዎሙ ፡ በአኂዝ ፡ ዕዳ ፡
በውስተ ፡ ፍትሕ ። ወከማሁ ፡ ለእለ ፡ ሀለዉ ፡
ታሕተ ፡ ሕፅንኒ ፡ በሕይወቶሙ ፡ ወእምድኅረ ፡
ሞቶሙ ። ወከማሁ ፡ ለፈታሒኒ ፡ እምድኅረ ፡
ተኀጥአቶሙ ፡ ለገበሬን ።

፱፻፺፱ ዋጋው ፡ ጥሩ ፡ ያይደለውን ፡ መያዣ ፡ ሊያደ
ርጉ ፡ አይገባም ። ይኸውም ፡ ነፃ ፡ እንደወጣ ፡
ባሪያ ፡ እርሱን ፡ ለሌላ ፡ እንደጐለቱት ፡ ቤት ፡
ብድሩ ፡ ከሚከፈልበት ፡ ጊዜ ፡ አስቀድሞ ፡
ፈጥኖ ፡ እንደሚጠፋ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ ነው ። ስለመ
ያዣው ፡ መለወጥ ፡ ሁለቱ ፡ ቢጣሉ ፡ ከመሐላ
ው ፡ ጋር ፡ እንደያዡ ፡ ቃል ፡ ይሁን ። እርሱ ፡
ወደጌታው ፡ እንደመለሰ ፡ ቢናገር ፡ ቃሉን ፡ አይ
ቀበሉት ። ከያዘው ፡ በኋላ ፡ የመያዣው ፡ ገን
ዘብ ፡ ቢበዛ ፡ መላውም ፡ ቢሆን ፡ እኩሌታውም
ቢሆን ፡ ከያዥ ፡ እጅ ፡ አይውጣ ። ባስያዙት ፡
ሰው ፡ እጅ ፡ ወይም ፡ ከምእመናን ፡ በአንዱ ፡
እጅ ፡ እንዲኖር ፡ ቢስማሙ ፡ በተወሰነው ፡ ሳይ ፡
ስምምነትን ፡ እንዳደረጉ ፡ ሊያደርግ ፡ ይገባል ።
አበዳሪና ፡ ተበዳሪ ፡ አማኙም ፡ ሥራቱ ፡ እንደ
ሚገባ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ በመያዣው ፡ ሊሰለጥ
ኑበት ፡ አይገባም ። ከሞቱ ፡ በኋላ ፡ መያዣውን
የያዘና ፡ የተበዳሪ ፡ የወራሽ ፡ ፍርድ ፡ ይሆ ፡
ነው ። ስለመያዣ ፡ የትእዛዝ ፡ ደብዳቤ ፡ የጻ
ፈላቸውና ፡ ዕዳውን ፡ በመያዝ ፡ የሾማቸው ፡
በፍርድ ፡ ጊዜ ፡ እንደዚሁ ፡ ነው ። በሕይወታቸ
ውና ፡ ከሞታቸው ፡ በኋላ ፡ በሞግዚት ፡ ስር ፡
ላሉ ፡ እንዲሁ ፡ ነው ። እኒህ ፡ የተጠሩት ፡
(የተጠቀሱት) ፡ ከመታጣታቸው ፡ በኋላ ፡ ለዳ
ኞውም ፡ እንዲሁ ፡ ነው ።

፩ሺ. መኮ ፡ ፃወጅቱ ፡ ወዘሎቱ ፡ ንዋይ ፡ ኀበ ፡

፩ሺ. መከ ፡ ፃጅ ። ከሌላ ፡ ዘንድ ፡ ገንዘብ ፡ ያለው ፡

አንቀጽ ፡ ፵፯ ።

ካልእ ፡ ወኢኀሠሦ ፡ እስከ ፡ ፴ ፡ ዓመት ፡ ኢይደልዎ ፡ እምድኅረ ፡ ዝንቱ ፡ ተመይጦ ፡ ከመ ፡ ይኅሥሦ ፡ ኪያሁ ፡ ውእቱ ፡ ወኢ ፡ ወልዱ ፡ ወከማሁ ፡ ይደሉ ፡ በግብረ ፡ ምግባሪ ። ወለእመ ፡ ሀሎ ፡ በእደ ፡ ሰብእ ፡ እንግዳ ፡ ወኢወፅአ ፡ እምእዴሁ ፡ ኀበ ፡ ትንየተ ፡ ካልእ ፡ ሎቱ ፡ ይደሉ ፡ ከመ ፡ ይኅሥሥ ፡ ንዋዮ ፡ እሙ ፡ ከመ ፡ ይንሣእ ፡ እንዘ ፡ ዘእኀዘ ፡ ወእመ ፡ ወፅአ ፡ እንግዳ ፡ እምእዴሁ ፡ ኀበ ፡ ካልኡ ፡ ኢይደሉ ። ወከመዝ ፡ ነገር ፡ ይደሉ ፡ ለኵሉ ፡ ተኅሥሦተ ፡ ሰዳ ፡ ወርስታት ፡ ወቍንጳያት ፡ ወሕገጋት ፡ ወተሳትፎታት ፡ ወትዕግልታት ፡ ወውሳንያተ ፡ ምድር ፡ ወግዘቶት ፡ ወመሐዘ ፡ ማይ ፡ በውስተ ፡ ቤት ፡ ወዘገር ፡ ወገነጋት ፡ ወዘይመስሎ ፡ ለዝንቱ ፡ ኢይደልዎ ፡ ለበዓል ፡ ከመ ፡ ይትኀሠሥ ፡ እምድኅረ ፡ ፴ ፡ ዓመት ፡ ወእመኒ ፡ ፈቀደ ፡ ተኀሥሦ ፡ ኢይፈትሕዎ ፡ ሎቱ ፡ በዝንቱ ።

፩ሺ.፩ መከ ፡ ፻ወ፵ቱ ፡ ወእብኒ ፡ ኢይትእኀዝ ፡ በሰዳ ፡ ሊቀሉ ፡ ወልዱ ፡ ለእመ ፡ ኢኮነ ፡ ዘተሰትሐ ፡ በትእዛዘ ፡ ዚአሁ ። ወኢይትእኀዝ ፡ ብእሲ ፡ በሊቀሉ ፡ ንዋየ ፡ እሙ ፡ ወእኁሁ ፡ በእኁሁ ፡ ወኢ ፡ በአበ ፡ ብእሲቱ ፡ ዳእሙ ፡ እመ ፡ ተሐበ ዮሙ ፡ ይፍዲ ።

፩ሺ.፪ ወበእንተ ፡ ሕቢትሰ ፡ ወእደ፡ጎኖ ፡ ለሙ ፡ ፅቱ ፡ ፍናዋት ፡ እደ፡ጎኖስ ፡ ዘነፍስ ፡ ውእቱ ፡ ወተሐብዮ ፡ ዘንዋይ ። ወተሐብዮስ ፡ ዘንዋይ ፡ ለዘተጠየቀ ፡ ንዋዩ ፡ ወሥርዓቱ ፡ ለዘከመዝ ፡ ይትጋኤ ፡ ትሕቢቱ ። ወእመ ፡ ኮነ ፡ ዘተሐበዮ ፡ ሎቱ ፡ ማእምረ ፡ እሙ ፡ በብዩ ፡ ይደሉ ፡ እንከ ፡ ተሐብዮ ፡ በትእዛዘ ፡ ዚአሁ ፡ ለዘተሐበይዎ ፡ ወለእመኒ ፡ ኮነ ፡ ዘእንበለ ፡ ትእዛዙ ። ወለእመ ፡ ተሐበዮ ፡ በትእዛዙ ፡ ይደሉ ፡ ተኀሥሦ ፡ እምኔሁ ፡ በኵሉ ፡ ዘፈደየ ፡ በእንቲአሁ ፡ ወለእመሰ ፡ ተሐበዮ ፡ ዘእንበለ ፡ ትእዛዙ ፡ ኢይደሉ ፡ ተኀሥሦ ፡ እምኔሁ ፡ ዘእንበለ ፡ በዘፈደየ ፡ በእንቲአሁ ።

፩ሺ.፫ ወነገረ ፡ ተሐብዮሰ ፡ ከመዝ ፡ ውእቱ ፡ ከመ ፡ ይበል ፡ ተሐበይኩክዎ ፡ አነ ፡ እገሌ ፡ ለእገሌ ፡ በዘከመዝ ፡ ወዘከመዝ ። ወለእመ ፡ ይቤ ፡ ተሐበይኩ ፡ ለእገሌ ፡ በእንተ ፡ እገሌ ፡ ወለእመ ፡ ቆመ ፡ ላዕሌሁ ፡ ስምዕ ፡ ይደሉ ፡ ቦቱ ፡ በውእቱ ፡ ጊዜ ፡ ዘኮነ ፡ ተሐብዮ ፡ ወእኮ ፡ በዘእምነ ፡ ቦቱ ፡ ዘተሐበዮ ፡ ዘእንበለ ፡ ሰማዕት ። ወለእመ ፡ ይቤ ፡ ዘተሐበየ ፡ ተሐበይኩ ፡ ውዕገ ፡

ስለ ፡ ብድር ።

ሰው ፡ እስከ ፡ ፴ ፡ ዓመት ፡ ባይፈልገው ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እርሱም ፡ ቢሆን ፡ ልጁም ፡ ቢሆን ፡ ተመልሶ ፡ ሊጠይቅ ፡ አይገባውም ። በአስተዳዳሪነትም ፡ ሥራ ፡ እንደዚሁ ፡ ይገባል ። በከላሽ ፡ እጅ ፡ መያዣ ፡ ቢኖር ፡ ከእጁ ፡ ወደሌላው ፡ እጅነት ፡ ባይወጣ ፡ ለእርሱ ፡ ገንዘቡን ፡ ሊጠይቅ ፡ ወይም የያዘውን ፡ መያዣ ፡ ሊይዝ ፡ ይገባዋል ። መያዣው ፡ ከእጁ ፡ ወደሌላው ፡ ቢወጣ ፡ ሊጠይቅ ፡ አይገባም ። ዕዳን ፡ ስመፈላሰግ ፡ ሁሉ ፡ እንደዚህ ፡ ነገር ፡ ይገባል ። የርስትና ፡ የዳኝነት ፡ የሕግና ፡ የአንድነት ፡ ንግድ ፡ የቅሚያ ፡ የምድር ፡ ድንበር ፡ የጕድጓድ ፡ በቤትና ፡ በሀገር ፡ በተክልም ፡ በታ ፡ ያለ ፡ የውሀ ፡ በይ ፡ ይህን ፡ የመስለውም ፡ ለአንድ ፡ ሰው ፡ ከ፴ ፡ ዓመት ፡ በኋላ ፡ ሊጠይቅ ፡ አይገባውም ። ሊከራከር ፡ ቢወድም ፡ በዚህ ፡ አይፍረዱለት ።

፩ሺ.፩ መከ ፡ ፻፵ ። አባት ፡ በልጁ ፡ ብድር ፡ ዕዳ ፡ አይያዝ ። በእርሱ ፡ ትእዛዝ ፡ የተበደረ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ። ሰው ፡ በእናቱ ፡ ገንዘብ ፡ ብድር ፡ አይያዝ ፡ ወንድም ፡ በወንድሙ ፡ በሚስቱም ፡ አባት ፡ አይያዝ ። ነገር ፡ ግን ፡ ቢዋሳቸው ፡ ይከፈል ።

፩ሺ.፪ ስለዋስትናና ፡ ስለመድን ፡ ግን ፡ ሁለት ፡ መንገዶች ፡ አሏቸው ። መድን ፡ የነፍስ ፡ ነው ። ዋስትናም ፡ የገንዘብ ፡ ነው ። የገንዘብ ፡ ዋስትና ፡ ግን ፡ ገንዘቡና ፡ ውሳኔው ፡ ሊተረጋገጠ ፡ ለእንደዚህ ፡ ላለው ፡ ዋስትናው ፡ ያምራል ። ለእርሱ ፡ የተዋሰው ፡ ሰው ፡ አዋቂ ፡ ወይም ፡ አላዋቂ ፡ ቢሆን ፡ በሚዋሱት ፡ ሰው ፡ ትእዛዝ ፡ ያለ ፡ ትእዛዙም ፡ ቢሆን ፡ እንግዲህ ፡ መዋስ ፡ ይገባል ። በትእዛዙ ፡ ቢዋሰው ፡ ስለእርሱ ፡ በከፈለው ፡ ሁሉ ፡ ከእርሱ ፡ መጠየቅ ፡ ይገባል ። ያለትእዛዙ ፡ ቢዋሰው ፡ ግን ፡ ከከፈለው ፡ በቀር ፡ ከእርሱ ፡ ዕዳ ፡ መፈለግ ፡ አይገባም ።

፩ሺ.፫ የመዋስም ፡ ነገር ፡ እንዲህ ፡ ነው ። እኔ ፡ እገሌ ፡ ለእገሌ ፡ እንደዚህና ፡ እንደዚህ ፡ ባለ ፡ ነገር ፡ ተውሸዋለሁ ፡ ይል ፡ ዘንድ ፡ ነው ። ስለ ፡ እገሌ ፡ ለእገሌ ፡ ተውሸዋለሁ ፡ ቢል ፡ ምስክርም ፡ ቢመሰክርበት ፡ ዋስ ፡ የሆነው ፡ ሰው ፡ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ መክፈል ፡ ይገባዋል ። ያለምስክር ፡ ዋሱ ፡ ባመነበት ፡ አይደለም ። የተዋሰው ፡ ሰው ፡ ተውሼያለሁና ፡ ገንዘብህን ፡ ከባሕር ፡ ወይም ፡ ልብ

አንቀጽ ፡ ፳፮ ።

ንዋየከ ፡ ውስተ ፡ ባሕር ፡ እው ፡ እልባሲከ ፡ ውስተ ፡ እሳት ፡ እይማኒ ፡ ተሐብዮቱ ፡ ለዘከነ ፡ ውስተ ፡ ዝንቱ ፡ እርእያ ።

፩ሺ.፬ ወዘይደልዎሙ ፡ ለሊቃሒ ፡ ከመ ፡ ይትኃሠሥ ፡ ቅድመ ፡ ለተሊቃሒ ፡ ወለእመ ፡ እፈደየ ፡ ይሕተ ፡ ወይትኃሠሥ ፡ ለዘተሐበየ ። ወለእመ ፡ ርኅቀ ፡ ተሊቃሒ ፡ የሀብ ፡ ፈታሒ ፡ ለተሐባዪ ፡ ሰደሚ ፡ ወለእመ ፡ እረከበ ፡ በውእቱ ፡ ሰደሚ ፡ እሚሃ ፡ ይስፋሕ ፡ እደዊሁ ፡ ለነሢእ ፡ ንዋዩ ፡ ለዘተሐበየ ፡ ተሊቃሒ ፡ በእምግባረ ፡ ሊቃሕ ፡ ለእመ ፡ ፈደየ ። ወእመ ፡ አኮሰ ፡ ይስፋሕ ፡ እደዊሁ ፡ ለቃሒ ፡ ኅበ ፡ ጥሪቱ ፡ ለተሐባዪ ፡ በእምግባረ ፡ ሊቃሕ ።

፩ሺ.፭ ወይደልዎ ፡ ለሊቃሒ ፡ ተኃሥሦቶሙ ፡ ለተሊቃሒ ፡ ወተሐባዪ ። ወለተሐባዪኒ ፡ ለእመ ፡ ተሐበየ ፡ ካልዕ ፡ ይደልዎ ፡ ሎቱ ፡ ተኃሥሦቶ ፡ ዘሎሙ ፡ ወለእመ ፡ ሞተ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ይደሉ ፡ ቦቱ ፡ ከመ ፡ ይትኃሠሥዎ ፡ እለ ፡ ተርፉ ፡ ወለእመ ፡ መሐረ ፡ በኩሉ ፡ እምኔሆሙ ፡ ወአስተደኃረ ፡ ኀሠሣሁ ፡ ይድኅን ፡ ተሐባዪ ፡ ወትደኃር ፡ ኀሠሣሁ ፡ ወኢይትኃሠሥዎ ። ወእመ ፡ ቦ ፡ ዘተፈደየ ፡ እምኔሁ ፡ ውእተ ፡ ሊቃሐ ፡ ተዐርዐ ፡ ተኃሥሦቶሙ ፡ በእንቲአሁ ፡ ለእለ ፡ ተርፉ ።

፩ሺ.፮ ወለእመ ፡ ኮኑ ፡ እለ ፡ ተሐበዩ ፡ ብዙኃነ ፡ ወለለ፩ዱ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ያስተቃልሉ ፡ ተዋሕሶቶ ፡ ይደልዎ ፡ ለዘነሥአ ፡ ሕበይቶሙ ፡ ከመ ፡ ይትኀሠሥ ፡ እምነ ፡ ኵሎሙ ፡ ኵሎ ፡ ንዋዮ ። ወዘሂ ፡ ነሥአ ፡ እም፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ይደልዎ ፡ ለገቢኡ ፡ ፩ዱ ፡ ከመ ፡ ይትኀሠሦሙ ፡ ለለ፩ዱ ፡ እምእለ ፡ ተርፉ ፡ ዘወሀበ ፡ ለሊሁ ፡ ፈድፋዴ ፡ እምነ ፡ ዘይደሉ ፡ ላዕሌሁ ፡ መንፈቀ ፡ ወራብዕተ ፡ እድ ፡ በእምሳል ፡ ለእመ ፡ ኮኑ ፡ ፬ተ ፡ ወኢኮነ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ዘያስተቃልል ፡ እላ ፡ ኵሎሙ ፡ ኅቡረ ፡ ኢይደልዎሙ ፡ ለተሐባይያን ፡ ከመ ፡ ይትኀሠሥዎ ፡ ኵሎ ፡ ለለ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ዘእንበለ ፡ በዘይደልዎ ፡ ውሂበ ፡ ራብዕተ ፡ እድ ፡ ለእመ ፡ ኮኑ ፡ ፬ተ ።

፩ሺ.፯ ወለእመ ፡ ገብረ ፡ ሰርቀ ፡ ንግሥ ፡ ዋሕስ ፡ ምስለ ፡ በዓለ ፡ ንዋይ ፡ ዘተሐበየ ፡ ሎቱ ፡ በእንተ ፡ ፩ዱ ፡ እምንዋይ ፡ ድኅነ ፡ ተሐባዪ ፡ ወዘተሐበዮሙ ፡ ሎሙ ፡ እምተኃሥሦተ ፡ በዓለ ፡ ዕዳ ፡ ወይከውን ፡ ተሐባዪ ፡ ተኃሣሢ ፡ ለዘተሠ

ስለ ፡ ብድር ።

ስህን ፡ ከእሳት ፡ ጣል ፡ ቢል ፡ በዚህ ፡ ዓይነት ፡ የሆነው ፡ ሰው ፡ ዋስትና ፡ መልካም ፡ አይደ ለም ።

፩ሺ.፬ ላበዳሪም ፡ የሚገባው ፡ አስቀድሞ ፡ ተበዳሪን ፡ መጠየቅ ፡ ነው ። ባይከፍል ፡ ሂዶ ፡ ዋሱን ፡ ይጠ ይቀው ። ተበዳሪ ፡ ቢርቅ ፡ ዳኛ ፡ ለዋሱ ፡ ቀን ፡ (ቀጠሮ) ፡ ይስጠው ። በዚያ ፡ ቀጠሮ ፡ ባያገኘው ከከፈለ ፡ ዋስ ፡ የሆነውን ፡ የተበዳሪ ፡ ገንዘብ ፡ በብድሩ ፡ ልክ ፡ ለመውሰድ ፡ ያንጊዜ ፡ እጁን ፡ ይዘርጋ ። ይህም ፡ ባይሆን ፡ ግን ፡ አበዳሪ ፡ በብ ድሩ ፡ ልክ ፡ ወደዋሱ ፡ ገንዘብ ፡ እጁን ፡ ይዘ ርጋ ።

፩ሺ.፭ ለአበዳሪ ፡ ዋሱንም ፡ ተበዳሪውንም ፡ መያዝ ፡ ይገባዋል ። ሌላ ፡ ቢዋሰው ፡ (የጠለፋ ፡ ዋስ ፡ ቢኖረው) ፡ ሁሎቹንም ፡ መያዝ ፡ ይገባዋል ። ከእነርሱ ፡ አንዱ ፡ ቢሞት ፡ የቀሩት ፡ በዕዳው ፡ ሊጠየቁት ፡ ይገባል ። ከእነርሱ ፡ በሁሉ ፡ ቢም ረው ፡ መፈለጉንም ፡ ቢያቆይ ፡ ዋሱ ፡ ይዳን ። መያዙም ፡ ትቆይ ። አይፈላለጉት ። ከእርሱ ፡ ያን ፡ ብድር ፡ የተከፈለ ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡ ስለእ ርሱ ፡ የቀሩት ፡ ሰዎች ፡ ክርክር ፡ ተቋረጠ ።

፩ሺ.፮ ዋሶች ፡ ብዙዎች ፡ ቢሆኑ ፡ ለእያንዳንዳቸው ፡ ዋስነታቸውን ፡ ያስወርዱ ። ዋስነታቸውን ፡ ለተቀበለ ፡ ሰው ፡ ገንዘቡን ፡ ሁሉ ፡ ከሁላቸው ፡ ሊቀበል ፡ ይገባዋል ። ከእነርሱ ፡ ወገን ፡ ከአ ንዱ ፡ የወሰደም ፡ ለእርሱ ፡ ከሚገባው ፡ አብ ልጦ ፡ እርሱ ፡ የሰጠውን ፡ እኩሌታውንና ፡ አራት ፡ እጁን ፡ ከቀሩት ፡ ሰዎች ፡ እያንዳንዱን ፡ ሊጠይቃቸው ፡ ስለዚያ ፡ ለአንዱ ፡ ሰው ፡ ይገባ ዋል ። ለምሳሌ ፡ አራት ፡ ቢሆኑ ፡ ሁሉም ፡ በአ ንድነት ፡ እንጂ ፡ ከእነርሱ ፡ ፩ዱ ፡ የሚከፍል ፡ አይደለም ። አራት ፡ ቢሆኑ ፡ ከእነርሱ ፡ እያንዳን ዱ ፡ አራተኛውን ፡ እጅ ፡ መስጠት ፡ በሚገባው ፡ ገንዘብ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ ሁሉን ፡ ይከፍሉ ፡ ዘንድ ፡ ለዋሶች ፡ አይገባቸውም ።

፩ሺ.፯ ዋስ ፡ የጠራ ፡ ከገንዘብ ፡ ወገን ፡ ስለአንዱ ፡ ከተ ዋሰው ፡ ባለገንዘብ ፡ ጋራ ፡ ዕርቅ ፡ ቢያደርግ ፡ ዋሱ ፡ ዳነ ። ለእነርሱም ፡ የተዋሳቸው ፡ ከባለ ዕዳው ፡ መፈላለግ ፡ ዳነ ። ዋሱ ፡ በታረቀበት ፡ ልክ ፡ ለተዋሰው ፡ ሰው ፡ ተያዥ ፡ ይሆናል ።

እንቀጽ ፡ ፳፯ ።

ሕስ ፡ ሎቱ ፡ በእምጣን ፡ ዘተዓረቀ ፡ ቦቱ ።

፩ሺ.፰ ወይደሉ ፡ ሥርዓተ ፡ ሕቢት ፡ በነቢረ ፡ ውሳኔ ፡ ወይበል ፡ ተሐባዪ ፡ አነ ፡ ተሐበይኩክሙ ፡ ለእገሌ ፡ ከመዝ ፡ እስከ ፡ ኀበዝ ። ወማእዜኒ ፡ ይደልዎ ፡ ለተሐባዪ ፡ በንዋይ ፡ ከመ ፡ የሀብ ፡ ለዘተሐበዮ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ይደኅን ፡ እምዕዳ ።

፩ሺ.፱ ወእመሰ ፡ ተሰነአወ ፡ ተሐባዪ ፡ ወነሣኢ ፡ ዋሕስ ፡ ሳሰለ ፡ ንዋይ ፡ ይደልዎ ፡ ይፍዲ ፡ ተሐባዪ ፡ ንዋየ ፡ ነሣኤ ፡ ዋሕስ ፡ ወይደልዎ ፡ ቀዊም ፡ ሳሰለ ፡ ንዋይ ፡ እስከ ፡ ይትኀሠሥ ፡ ነሣኢ ፡ እምኔሁ ። ወለእመ ፡ ረከቦ ፡ ቦቱ፡ ተሐባዪ ፡ በዘንሥአ ፡ እው ፡ ኀጎለ ፡ ዘንቱ ፡ ይደሉ ፡ ሎቱ ። ወኢይደልዎ ፡ ለመኑሂ ፡ በዓለ ፡ ዕዳ ፡ ከመ ፡ ይትከላእ ፡ እምተመጥዎቱ ፡ ዘወሀበ ፡ ሎቱ ፡ ተለቃሒ ፡ በጊዜ ፡ ወሀበ ፡ ወበኵሉ ፡ ንዋይ ፡ ኢይደሉ ፡ ተራድኦቱ ፡ እምተሐባዪ ፡ ለእመ ፡ ኢኮነ ፡ አማን ፡ ተሐብዮቱ ፡ በከመ ፡ ፍትሐ ፡ ሕግ ።

፩ሺ.፲ ወለእመ ፡ ሞተ ፡ ዘተሐበዮ ፡ ይደልዎ ፡ ለተሐባዪ ፡ ተኀሥሦ ፡ እምወራስያኒሁ ፡ በዘተሐበየ ፡ ኪያሁ ፡ ለእመ ፡ ቦቱ ፡ ጥሪት ። ወለእመኒ ፡ ሞተ ፡ ተሐባዪ ፡ ይደልዎ ፡ ተኀሥሦ ፡ ለነሣኢ ፡ ዋሕስ ፡ እምእደ ፡ ወራሲያኒሁ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ ሎቱ ፡ ንዋይ ። ወለእመ ፡ አልቦቱ ፡ ንዋይ ፡ ኢይትኀሠሥ ፡ እምዝ ፡ ኢኮነ ፡ ሎቱ ፡ ዋሕስ ።

፩ሺ.፲፩ ወመድኅን ፡ ነፍስኒ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ ያምጽእ ፡ ዘተድኅነ ፡ ወይኩን ፡ ቃለ ፡ ዘተ ፡ ተድኅኖ ፡ ከመ ፡ ይበል ፡ ተድኅንኩ ፡ ለአብጽሖቱ ፡ እገሌ፡ ለእገሌ ፡ እው ፡ ተድኅንኩ ፡ ለእገሌ ፡ ገጸ ፡ እገሌ ፡ እው ፡ ላዕሌየ ፡ ተድኅኖተ ፡ እገሌ ። ወለእመ ፡ ሠርዐ ፡ ለድኅኔ ፡ እሙረ ፡ በአይኒ ፡ ጊዜ ፡ ይትኀሠሥዎ ፡ ኅሠሣ ፡ ለዘተድኅነ ፡ አመ ብጽሐ ፡ ለድኅኔ ፡ ወበጊዜ ፡ የኀሥሥ ፡ እምኔሁ ፡ ዘኮነ ፡ ሎቱ ፡ መድኅን ። ወለእመ ፡ አብጽሐ ፡ እምቅድመ ፡ ውእቱ ፡ ጊዜ ፡ አመ ፡ ይትከሀሎ ፡ እኂዞቱ ፡ ለበዓለ ፡ ዕዳሁ ፡ ድኅነ ፡ እምኔሁ ፡ ወከማሁ ፡ ለእመ ፡ አግብአ ፡ ነፍሶ ፡ ለበዓለ ፡ ዕዳሁ ። ወእመኒ ፡ ኢተረክበ ፡ እምድኅረ ፡ ለድኅኔ ፡ ዘተሠርዐ ፡ የሀብ ፡ ፈታሒ ፡ ለድኅኔ ፡ መዋዕለ ፡ እስከ ፡ ያመጽእ ። ወለእመ ፡ ኢያምጽኦ ፡ እምድኅረ ፡ ለድኅኔሁ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ ዘተሐበየ ፡ ሎቱ ፡ ገጸ ፡ ባሕቲቱ ፡ ተእኀዘ ፡ በአብጽሖቱ ፡ ባሕቲቱ ። ወእመኒ ፡

ስለ ፡ ብድር ።

፩ሺ.፰ የዋሰንት ፡ ሥራት ፡ ውሳኔ ፡ እንዲኖረው ፡ ይገባል ። ዋሱ ፡ እኔ ፡ ለእገሌ ፡ ከዚህ ፡ እስከ ፡ ዚህ ፡ ተውሼዋለሁ ፡ ይበል ። መቸውንም ፡ ከሰዳው ፡ ይድን ፡ ዘንድ ፡ ለተዋሰው ፡ ሰው ፡ ሊሰጥ ፡ ገንዘብ ፡ ዋስ ፡ ለሆነ ፡ ይገባዋል ።

፩ሺ.፱ ዋሱና ፡ ዋስ ፡ የጠራው ፡ በገንዘቡ ፡ ቢስማሙ ፡ ዋስ ፡ የጠራ ፡ ገንዘቡን ፡ ሊከፍል ፡ ይገባዋል ። ተቀባይ ፡ ከእርሱ ፡ እስኪፈልገው ፡ ድረስ ፡ በገንዘቡ ፡ ማዘዝ ፡ ይገባዋል ። ዋሱ ፡ በተቀበለው ፡ ገንዘብ ፡ ቢጠቀምበት ፡ ወይም ፡ ቢጠፋበት ፡ ይህ ፡ ለእርሱ ፡ ይገባል ። ለማንም ፡ ባለዕዳ ፡ ተበዳሪ ፡ በሰጠው ፡ ጊዜ ፡ የሰጠውን ፡ ከመቀበል ፡ ሊከለከል ፡ አይገባውም ። እንደ ፡ ሕግ ፡ ፍርድ ፡ ዋሰንቱ ፡ እውነተኛ ፡ ካልሆነ ገንዘቡን ፡ ሁሉ ፡ ከዋሱ ፡ መክፈል ፡ አይገባም ።

፩ሺ.፲ ዋስ ፡ የሆኑት ፡ ሰው ፡ ቢሞት ፡ ገንዘብ ፡ ካለው ፡ እርሱን ፡ በተዋሰበት ፡ ከወራሾቹ ፡ መጠየቅ ፡ ለዋሱ ፡ ይገባዋል ። ዋሱ ፡ ቢሞትም ፡ ገንዘብ ፡ ያለው ፡ ከሆነ ፡ ለዋስ ፡ እነቹ ፡ ከወራሾቹ ፡ መጠየቅ ፡ ይገባዋል ። ገንዘብ ፡ ባይኖረው ፡ ግን ፡ ዋስ ፡ ካልሆነው ፡ አይፈልግ ።

፩ሺ.፲፩ የነፍስ ፡ መድኅንም ፡ መድን ፡ የሆነበትን ፡ ያመጣ ፡ ዘንድ ፡ ይገባዋል ፡ የይህች ፡ መድኅንነት ነገርም ፡ እገሌን ፡ ለእገሌ ፡ ለማድረስ ፡ ወይም ፡ በእገሌ ፡ ፊት ፡ ለእገሌ ፡ መድን ፡ ሁኛለሁ ። ወይም ፡ የእገሌ ፡ መድኅንነት ፡ በእኔ ፡ ላይ ፡ ነው ፡ እንዲል ፡ ይሁን ፡ በማናቸውም ፡ ጊዜ ፡ የታወቀ ፡ ቀጠሮ ፡ ቢወስን ፡ ቀጠሮው ፡ በደረስ ጊዜና ፡ መድን ፡ የሆነለትን ፡ ከእርሱ ፡ በሚፈልግበት ፡ ጊዜ ፡ መድን ፡ የሆነውን ፡ በማናቸውም ጊዜ ፡ ፍሊጋን ፡ ይፈላለጉት ። ቀጠሮው ፡ ሳይደርስ ፡ በዓለ ፡ ዕዳዉን ፡ መያዝ ፡ በተቻለው ፡ ጊዜ ቢያቀርበው ፡ ከዕዳዉ ፡ ዳነ ። ራሱንም ፡ ለባለዕዳዉ ፡ ቢያሳልፍ ፡ እንደዚሁ ፡ ነው ። ከተወሰነው ፡ ቀጠሮ ፡ በኋላ ፡ ባይገኝም ፡ እስኪያመጣው ፡ ድረስ ፡ ዳኛ ፡ የቀን ፡ ቀጠሮ ፡ ይስጠው ። ከቀጠሮውም ፡ በኋላ ፡ ባያመጣው ፡ ፊቱን ፡ ለማቅረብ ፡ ብቻ ፡ የተዋሰው ፡ ከሆነ ፡ እርሱን ፡ በማድረስ ፡ ብቻ ፡ ይያዛል ። እርሱ ፡ እንደሆን ፡ ቢስ

ተሰናአወ ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡ ወውእቱ ፡ እመ ፡ ኢያብጽሐ ፡ በጊዜ ፡ ኀሠሣሁ ፡ ውእቱ ፡ ተሐበየ ሰዳ ፡ ዘላስሌሁ ፡ ወከዋኒሁ ፡ ከመዝ ፡ ወከመዝ ፡ ይከውን ፡ እምውእቱ ፡ ጊዜ ፡ ተሐባዪ ፡ ዘን ዋይ ፡፡

ማማ ፡ በተፈለገም ፡ ጊዜ ፡ ባያቀርብ ፡ ሰዳጨን ፡ የራሱ ፡ አድርጎ ፡ ተዋስ ፡፡ ሁኔታውም ፡ የገን ዘብ ፡ ዋስ ፡ ከሆነበት ፡ ጊዜ ፡ ጀምሮ ፡ እንደዚሁ ፡ ይሆናል ፡፡

፩ሺ.፲፮ ወለእመ ፡ ኢተረክበ ፡ መደኅን ፡ ወተደኅኖ ፡ ለዘተደኅነ ፡ ካልእ ፡ መደኅን ፡ ወለዘሰ ፡ ዘቦቱ ፡ መደኅን ፡ ይደሉ ፡ ተኀሥሥዎ ፡ በእንቲአሁ ፡ ወኢይደሉ ፡ ተደኅኖቱ ፡ ለዘይደሉ ፡ ላዕሌሁ ፡ ቀትል ፡ ወለእመ ፡ ሞተ ፡ ዘተደኅንዎ ፡ ይትኀሠሡ ፡ አደኅኖቶ ፡ እመደኅን ፡ ወዘይደሉሰ ፡ ከመ ፡ ይኀሥሥ ፡ ቅድመ ፡ ለበዓለ ፡ ሰዳሁ ፡ ወለእመ ፡ ኢረከበ ፡ ይኀሥሥ ፡ ለመደኅን ፡፡

መድኑ ፡ ባይገኝ ፡ ለመድኑ ፡ ሌላ ፡ መድን ፡ ሊሆነው ፡ መድን ፡ ላለው ፡ ሁሉ ፡ ስለእርሱ ፡ መፈላለግ ፡ ይገባል ፡፡ ሞት ፡ ለሚገባው ፡ መድን መሆን ፡ አይገባም ፡፡ መድን ፡ የሆኑት ፡ ሰው ፡ ቢሞት ፡ ከመድኑ ፡ እርሱን ፡ ማዳን ፡ ይፈልጉ ፡ አስቀድሞ ፡ ሊፈልግ ፡ የሚገባውስ ፡ ባለሰዳ ውን ፡ ነው ፡፡ ባያገኘው ፡ መድኑን ፡ ይፈልገው ፡፡

፩ሺ.፲፯ ረስጠጅ ፡ ዘ፲ወ፱ቱ ፡ ወኢይደልዎ ፡ ለካህን ፡ ከመ ፡ ይትወሐስ ፡ ፩ደዪ ፡ ወየኀዝ ፡ ንዋየ ፡፡ ዘኒቅያ ፡ ፲ወ፰ቱ ፡ ወለብእሲትኒ ፡ ኢይትወከፋ ፡ እምኔሃ ፡ መደኅን ፡ ወኢተሐብዮ ፡፡

ረስጠጅ ፡ ፲፱ ፡፡ ካህን ፡ ለአንድ ፡ ሰውስ ፡ እንኳ ፡ ሊዋስ ፡ የእደራ ፡ ገንዘብም ፡ ሊይዝ ፡ አይገባ ውም ፡፡ ኒቅያ ፡ ፲፰ ፡፡ ሴትንም ፡ በመድንነትና ፡ በዋስትና ፡ አይቀበሉ ፡፡

፩ሺ.፲፰ ወዘሰ ፡ ይከውን ፡ በጽሕፈት ፡ አው ፡ በተአምኖ ባሕቲቱ ፡ ወእመ ፡ ይከሕድ ፡ ተለቃሒ ፡ ዘተለ ቅሐ ፡ ይትኀሠሥዎ ፡ በመሐላ ፡፡ ወለእመ ፡ መሐለ ፡ ወቆመ ፡ ቦቱ ፡ ሰማዕት ፡ እምድኅረ ዝንቱ ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡ መጽሐፍ ፡ መጽሐፈ ፡ ዚአሁ ፡ ውእቱ ፡ ይኩን ፡ ፍትሑ ፡ ፍትሐ ፡ ዘክሕደ ፡ በዓለ ፡ ሰዳሁ ፡ ወመሐለ ፡ ሎቱ ፡ ወባሕቱ ፡ እቅደምነ ፡ በዋንተ ፡ አንቀጽ ፡ ቀዳማዊ ፡፡ ወእመሰ ፡ ኢመሐለ ፡ ይሰጠ ፡ ላዕ ሌሁ ፡ ዘተነግረ ፡ በጽሕፈቱ ፡ ወለእመ ፡ ኢኮነ ፡ ጽሕፈቱ ፡ እዴሁ ፡ ወትሕዚቱ ፡ ይጹውዎ ፡ ለተለቃሒ ፡፡

በጽሕፈት ፡ ወይም ፡ በእምነት ፡ ብቻ ፡ የሚ ሆን ፡ ግን ፡ ተበዳሪ ፡ የተበደረውን ፡ ቢክድ ፡ በመሐላ ፡ ይፈላለጉት ፡፡ ቢምል ፡ ከእዚህ ፡ በኋላ ፡ ጽሕፈቱ ፡ የእርሱ ፡ ጽሕፈት ፡ እንደ ሆነ ፡ ምስክሮች ፡ ቢመሰክሩበት ፡ ፍርዱ ፡ ባለ ሰዳጨን ፡ ክዶ ፡ እንደማለ ፡ ሰው ፡ ፍርድ ፡ ይ ሁን ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ከመጀመሪያው ፡ አንቀጽ ፡ አስቀድመን ፡ ተናግረናል ፡፡ ባይምል ፡ ግን ፡ በደብዳቤው ፡ የተነገረው ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ተገባ ፡፡ የእጁ ፡ ጽሕፈት ፡ ዋስትናውም ፡ ባይ ሆን ፡ ተበዳሪውን ፡ ይጥሩት ፡፡

፩ሺ.፲፱ ወአእምር ፡ ከመ ፡ እግዚአብሔር ፡ አስተዓ ቀበ ፡ እምበዓለ ፡ ሰዳ ፡ ከመ ፡ ኢያሕምሞ ፡ ለበ ዓለ ፡ ሰዳሁ ፡ ሶበ ፡ ኀየአ ፡ በከሊኦቱ ፡ ልብሰ ፡ ዚአሁ ፡ ዘእኅዘ ፡ በከመ ፡ ተብህለ ፡ በኦሪት ፡፡ ወክልአ ፡ እምተኀሥሦቱ ፡ ኪያሁ ፡ ወነሢአ ፡ ኢየአኀዞ ፡ ወኢያሕምሞ ፡ ላዕሌሁ ፡ በከመ ፡ ተነግረ ፡ በወንጌል ፡ በዋንተ ፡ አንቀጽ ፡ ወበእ ንተ ፡ ዝንቱ ፡ ኢይደሉ ፡ አሕምሞ ፡ ላዕለ ፡ ጽኑስ ፡፡ ወባሕቱ ፡ ለዘሀለወ ፡ ላዕሌሁ ፡ ልቃሕ ፡ በከዊኖ ፡ ሰድማ ፡ ኢይትኀሠሥዎ ፡ በእንቲ አሃ ፡ ዘእንበለ ፡ በጊዜ ፡ ዘይደሉ ፡፡ ወለእመ ፡ ፈርሆ ፡ በእንቲአሁ ፡ የሀብዎ ፡ ዋሕስ ፡ በትእ ዛዘ ፡ ፈታሒ ፡፡

በኦሪት ፡ እንደተነገረ ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ ያሲያዘውን ፡ ልብሱን ፡ በመከልከል ፡ ተበዳሪን ፡ እንዳያስጨ ንቀው ፡ እግዚአብሔር ፡ ባለሰዳን ፡ እንዳስጠ በቀ ፡ እወቅ ፡፡ (ዘጸ ፡ ፳፪ ፡ ፲ - ፲፯) ፡፡ እርሱንም ፡ ከመያዝ ፡ ከለከለው ፡፡ እንዳይዘው ፡ ክፉም ፡ እንዳያደርግበት ፡ ነሣው ፡፡ በወንጌል ፡ በመጀ መሪያው ፡ አንቀጽ ፡ እንደተነገረ ፡፡ (ማቴ ፡ ፲፰ ፡ ፳፪) ፡፡ ስለዚህ ፡ በችግረኛ ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ መሥ ራት ፡ አይገባም ፡፡ ነገር ፡ ግን ፡ ጊዜን ፡ በመጠ ሰን ፡ ብድር ፡ ያለበትን ፡ ሰው ፡ በሚገባው ፡ ጊዜ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ ስለእርሱዋ ፡ አይፈላለ ጉት ፡፡ ስለእርሱ ፡ ቢፈሩ ፡ በዳኛ ፡ ትእዛዝ ፡ ዋስ ፡ ያስጠሩት ፡፡

፩ሺ.፳ ወለእመ ፡ ቦ ፡ ምንትኒ ፡ ዘይትኀሠሥዎ ፡ ባቲ ፡

፩ሺ.፳ በእርሷ ፡ የሚፈላለጉት ፡ አንዳች ፡ ነገር ፡ ቢኖር ፡

ወሰአልዎ ፡ ለመኰንን ፡ ሰብአ ፡ ዕዳሁ ፡ ከመ ፡ ይወስን ፡ ላዕሌሁ ፡ ለይ.ወስን ፡ ወለእመኒ ፡ ሤጠ ይሚጥ ፡ በእደ ፡ ዘየአምኖ ፡ ዘተረክበ ፡ እምጥሪቱ ፡ በቅድሜሁ ፡ ወበቅድመ ፡ ሰብአ ፡ ዕዳሁ ። አው ፡ በቅድመ ፡ መድኅኑ ፡ ወመድኅኖሙ ፡ ሤጠ ፡ በሰናይ ፡ በጽሕቅ ። ወያቅድሙ ፡ ሠይጠቶ ፡ ለዘይማስን ፡ ፍጡነ ፡ ወእምዝ ፡ በእንስሳ ፡ አው ፡ በአብያት ፡ ሰለኵሉ ፡ ግብር ፡ ውስተ ፡ ምሥያጥ ፡ በቅድመ ፡ ሰብእ ።

፩ሺ.፲፯ ወኢይፍዲ ፡ ዘእንበለ ፡ ዘተበውቀ ፡ ጥያቄሁ ፡ በሰማዕታት ፡ ወኢያብጽሕ ፡ በነገረ ፡ ሰዳውያን ፡ ባሕቲቶሙ ፡ እስከ ፡ ይከውን ፡ ተዓቅቦቱ ፡ እምተኀይሎቶሙ ፡ ወኢይበቍዕ ፡ ተአምኖቱ ፡ ዘለቅሕም ፡ ባሕቲቱ ፡ ወይፍርሁ ፡ እምተኀይሎ ፡ ወይፍልጡ ፡ ቦቱ ፡ ዘይከውኖ ፡ ለመፍቅድ ፡ ዘከማሁ ። ለእመ ፡ ኢፈጸመ ፡ ንዋዩ ፡ ፈድየ ፡ ልቃሑ ፡ ይክፍልዎሙ ፡ በአምጣነ ፡ ንዋዩ ።

፩ሺ.፲፰ ወሰዘሂ ፡ ተረክበ ፡ ሐሳበ ፡ ንዋዩ ፡ በአምጣነ ፡ ሤጡ ፡ የሀብዎ ፡ እንተ ፡ ባቲ ፡ ሤጠ ፡ ኪያሁ ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ሤጡ ፡ በውእቱ ፡ ጊዜ ፡ ብዙኅ ፡ የሀብዎ ፡ ዘይበዝኅ ። ወሰእመ ፡ ኢተረክበ ፡ ሎቱ ፡ ንዋይ ፡ ወነገረ ፡ ተጽናሰ ፡ ዚአሁ ፡ ወአጠየቀ ፡ ሰብአ ፡ ዕዳሁ ፡ በእፈ ፡ እሰ ፡ የአምሩ ፡ ህላዌሁ ፡ ከመ ፡ በሐሰት ፡ ተናገረ ፡ ይሞቅሕ ፡ ሎሙ ፡ እስከ ፡ ይፈድዮሙ ። ወለእመ ፡ ፈቀዱ ፡ እምሕሎቶ ፡ ያምሕልዎ ፡ ወያኅድግዎ ። ወሰእመ ፡ ተጠየቀ ፡ ተጽናሱ ፡ በጀቱ ፡ ሰማዕት ፡ ዘየአምሩ ፡ ግብሮ ፡ ይጽንሕዎ ፡ እስከ ፡ የኀልፍ ፡ ተጽናሱ ። ወለእመ ፡ ኮነት ፡ ሎቱ ፡ ዓስብ ፡ ይሥርዑ ፡ ላዕሌሁ ፡ ምጣኔ ፡ ዚአሁ ፡ እምድኅረ ፡ ነሢእ ፡ ዘየእክሎ ። ወለእመ ፡ ኢተጠየቀ ፡ ተጽናሰ ፡ ዚአሁ ይደኅር ፡ እኅድኅቱ ።



ባለዕዳዎችም ፡ በእርሱ ፡ ይወስን ፡ ዘንድ ፡ ዳኛውን ፡ ቢጠይቁት ፡ ይወስን ። ቢሸጥም ፡ ከገንዘቡ ፡ የተገኘውን ፡ በእርሱና ፡ በባለዕዳዎቹ ፡ ፊት ፡ ወይም ፡ በመድኑና ፡ በመድናቸው ፡ ፊት ፡ በሚያምነው ፡ ሰው ፡ እጅ ፡ ይሸጥ ። ሺያጩም ፡ በትክክል ፡ በትጋት ፡ ይሁን ። ፈጥኖ ፡ የሚበላሸውን ፡ ሺያጭ ፡ ያስቀድሙ ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እንስሳውን ፡ ወይም ፡ ቤቱን ፡ ለየሥራው ፡ ሁሉ ፡ በገበያ ፡ በሰዎች ፡ ፊት ፡ ይሁን ።

፩ሺ.፲፯ እርግጡ ፡ በምስክር ፡ ካልታወቀ ፡ በቀር ፡ አይክፈል ። ከተንኮላቸው ፡ መጠበቅ ፡ እስከሚሆንበት ድረስ ፡ በባለዕዳዎቹ ፡ ቃል ፡ አያቅርብ ። ያበደሩትን ፡ ሰው ፡ ብቻ ፡ ማመን ፡ አይጠቅምም ። ከቅሚያም ፡ ወገን ፡ ይፍሩ ። እንደዚሁም ፡ ለመፍቅድ ፡ የሚሆነውን ፡ ለእርሱ ፡ ይለዩ ። ገንዘቡ ፡ ብድሩን ፡ ሊከፍል ፡ ባይችል ፡ እንደ ፡ ገንዘቡ ፡ መጠን ፡ ያካፍልዋቸው ።

፩ሺ.፲፰ የገንዘቡ ፡ ሂሳብ ፡ በዋጋው ፡ ልክ ፡ ለተገኘለት ፡ ሰው ፡ እርሱን ፡ የሸጠባትን ፡ ይሰጡት ። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ዋጋው ፡ ብዙ ፡ ቢሆን ፡ የሚበዛውን ፡ ይስጡት ፡ ገንዘብ ፡ ባይገኝለት ፡ ችግሩንም ፡ ቢናገር ፡ ባለዕዳዎቹ ፡ በሐሰት ፡ እንደተናገረ ፡ ኑሮውን ፡ በሚያውቁ ፡ አፍ ፡ ቢያስመሰክሩ ፡ እስኪከፍላቸው ፡ ድረስ ፡ ይሠሩላቸው ። ሊያምሉት ፡ ቢወዱም ፡ አምለው ፡ ይተዉት ። ችግሩ ፡ ኑሮውን ፡ በሚያውቁ ፡ በሁለት ፡ ምስክሮች ፡ ቢረጋገጥ ፡ ችግሩ ፡ እስኪያልፍ ፡ ድረስ ፡ ይጠብቁት ። ደመወዝ ፡ ብትኖረው ፡ የሚበቃውን ፡ ከተቀበለ ፡ በኋላ ፡ በእርሱ ፡ ላይ ፡ ልኩን ፡ ይወስኑ ። ችግሩ ፡ ባይረጋገጥ ፡ መለቀቁ ፡ ይቀራል ።

## አንቀጽ ፳ወ፱ቱ ።

በእንተ ፡ ሕስት ።

፩ሺ.፲፱ ሕስትሰ ፡ ነሢእ ፡ በቀኖት ፡ ውእቱ ፡ ዘእንበለ ፡ ቤዛ ፡ በገጸ ፡ እሙር ። መጽ ፡ ዘ፳ወ፬ቱ ፡ ትቢ ፡ ዘ፲ወ፩ዱ ፡ ወለእመ ፡ ቦ ፡ ዘተወሐሰ ፡ እንስሳ ፡ እስከ ፡ መካን ፡ ውሱን ፡ ወተዓደወ ፡ ኪያሁ ፡

## አንቀጽ ፡ ፳፱ ።

ስለትውስት ፡ ይናገራል ።

፩ሺ.፲፱ ትውሰትስ ፡ በታወቀ ፡ ቦታ ፡ ያለዋጋ ፡ ጥቅም ፡ ማግኘት ፡ ነው ። መጽ ፡ ፳፬ ። ትቢ ፡ ፲፩ ። እስከ ፡ ተወሰነ ፡ ቦታ ፡ ከብት ፡ የተዋሰ ፡ ቢኖር ፡ የተወሰነውን ፡ ቢያልፍ ፡ ከጕዳት ፡ ወገን ፡ ያገ

አንቀጽ ፡ ፹፫ ።

፩ሺ.፬፻፲፪ ወሚመተ ፡ ፈታሒስ ፡ ድልው ፡ ውእቱ ፡ በፍጽሚ ፡ ሕግ ፡ ወፍጥረት ። ወዘይቀድምስ ፡ በከመ ፡ ይቤ ፡ እግዚአብሔር ፡ ልዑል ፡ በአሪት ፡ ውስተ ፡ መጽሐፍ ፡ ኃምስ ፡ ሢሙ ፡ ለክሙ ፡ ፈታሕተ ፡ በኵሉ ፡ አህጉሪክሙ ፡ እንተ ፡ ይሁበክሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክክሙ ፡ ከመ ፡ ይፍትሑ ፡ ማእከለ ፡ ሰብእ ፡ ፍትሐ ፡ ርቱዐ ፡ ዘኢያጸንኑ ፡ በጊዜ ፡ ፍትሕ ፡ ወኢይነሥኡ ፡ ገጸ ወኢሕልያነ ፡ እስመ ፡ ሕልያን ፡ ያዐውር ፡ አዕይንተ ፡ ጠቢባን ፡ ከመ ፡ ኢይርእዩ ፡ ጽድቀ ፡ ወይዌልጥ ፡ ቃለ ፡ ርቱዐ ።

፩ሺ.፬፻፲፫ ወዳግማዊኒ ፡ እስመ ፡ ተጋብእ ፡ ህገራዊ ፡ ኢይትገደግ ፡ ዘእንበለ ፡ ትኩን ፡ ተጋእዞ ፡ በቱ ፡ እምነ ፡ ግብረት ፡ ወኢይትፈጸምኬ ፡ በሠናይ ፡ ዘእንበለ ፡ ፈታሒ ፡ ዘይፈትሕ ፡ ማእከለ ፡ ተጋእዝያን ፡ ለጽኑዕ ፡ ወለድኩም ፡ ለለባዊ ፡ ወለዐብድ ፡ በከመ ፡ ይደሉ ፡ ለገቢረ ፡ ርትዕ ።

፩ሺ.፬፻፲፬ ወዘሂ ፡ ጸነ ፡ እምትእዛዘ ፡ ፈታሒ ፡ ይኤምር ፡ ካዕበ ፡ ከመ ፡ ይደሉ ፡ አቅሞቱ ፡ ወሥርዓተ ፡ አቅሞቱኒ ፡ ናሁ ፡ ይነብር ፡ እምትእዛዘ ፡ ፍትሕ ። ወይመርሕ ፡ ካዕበ ፡ ኀበ ፡ ያሊወ ፡ ሢመት ፡ እስመ ፡ ትእዛዘ ፡ ሢመትኒ ፡ ናሁ ፡ ቀደመ ፡ ተነግሮ ፡ በቀኖናት ፡ እምትእዛዘ ፡ ሢመት ፡ ዘካህናት ፡ ወሊቃነ ፡ ካህናት ፡ ወይደሉ ፡ ከመ ፡ ነአዝዝ ፡ በዝየኒ ፡ ትእዛዘ ፡ ሢመተ ፡ ፍትሕ ፡ እምነበ ፡ ውእቱ ፡ ፈታሒ ፡ እንተ ፡ ባቲ ፡ ይክውን ፡ ሢመቱ ፡ ሠናየ ፡ ወትቀውም ፡ ፍትሐ ፡ ዚአሁ ። ወጕላቄሆን ፡ ፲ወ፫ቱ ፡ ትእዛዛት ።

፩ሺ.፬፻፲፭ ቀዳሚሆን ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ብእሲ ፡ ወዝንቱ ፡ ዘያስተጋብእ ፡ እብጽሖተ ፡ መጠን ፡ ዘብእሲ ፡ ወብጽሖትስ ፡ ብጹሐ ፡ እምባን ፡ ዘፈጸመ ፡ ሕገ ፡ ውርዛዌ ። ወዘእንበሌሁሰ ፡ ኢይትፌጸም ፡ ልቡና ፡ ወኢይበቍዕ ፡ ለሢመት ፡ ከመ ፡ ይፍታሕ ፡ ማእከለ ፡ ዐቢያን ፡ ወልኁቃን ፡ ወዘይመስሎሙ ፡ ወኢይሜኒ ፡ ከመ ፡ የሀልዉ ፡ ዘእምሳለ ፡ እሉ ፡ ቅድሜሁ ፡ ለዘኢበጽሐ ፡ ኀበ ፡ መጠን ፡ ከመ ፡ ይፍታሕ ፡ ሎሙ ። ወበላሰሌሆሙ ፡ ሎሙ ፡ ብሂል ፡ ለእለ ፡ ይመውዑ ፡ ወበላዕሌሆሙ ፡ ሎሙ ፡ ብሂል ፡ ለእለ ፡ ይትመወዑ ።

፩ሺ.፬፻፲፮ ወበእንተ ፡ ተባዕትኒ ፡ እስመ ፡ ብእሲ ፡ ርእሳ ፡

ስለ ፡ ዳኛ ።

፩ሺ.፬፻፲፪ የዳኛ ፡ መሾምስ ፡ በሕግና ፡ በፍጥረት ፡ ፍጹሜ የተገባ ፡ ነው ። የሚቀድመው ፡ ግን ፡ ልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡ በኦሪት ፡ በአምስተኛው ፡ መጽሐፍ ፡ ፈጣሪያችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሚሰጣችሁ ፡ አገሮቻችሁ ፡ ሁሉ ፡ በሰዎች ፡ መካከል ፡ የቀና ፡ ፍርድ ፡ ይፈርዱ ፡ ዘንድ ፡ ለራሳችሁ ፡ ዳኞችን ፡ ሹሙ ። በፍርድ ፡ ጊዜ ፡ የማያደሉ ፡ ፊት ፡ አይተው ፡ መማለጃ ፡ (ጉቦ) ፡ የማይቀበሉ ፡ መማለጃ ፡ (ጉቦ) ፡ እውነትን ፡ እንዳያዩ ፡ የብልሆችን ፡ ዓይን ፡ ያሳውራልና ። የቀናውንም ፡ ፍርድ ፡ ይለውጣልና ፡ ብሎ ፡ እንደተናገረ ። (ዘዳግ ፡ ፲፮ ፡ ፲፰ - ፳) ።

፩ሺ.፬፻፲፫ ሁለተኛውም ፡ በህገር ፡ የምትደረግ ፡ ስብሰባ ፡ ከሥራ ፡ ወገን ፡ ክርክር ፡ ሳይሆንባት ፡ አትፈታምና ። በተጣሉት ፡ ሰዎች ፡ መካከል ፡ ለብርቱና ለደካማ ፡ ለዐዋቂና ፡ ላለዐዋቂም ፡ ቅን ፡ ለመሥራት ፡ እንደሚገባ ፡ የሚፈርድ ፡ ዳኛ ፡ ከሌለ ፡ በመልካም ፡ አይፈጸምምና ።

፩ሺ.፬፻፲፬ ከዳኛ ፡ ትእዛዝ ፡ የጸነነውንም ፡ (የተሰወረውንም) ፡ ሁለተኛ ፡ መቅጠር ፡ እንደሚገባ ፡ ያመለክታል ። የቀጠሮው ፡ ሥርዓትም ፡ ከፍርድ ፡ ትእዛዝ ፡ የተነሣ ፡ እነሆ ፡ ይወሰናል ። ዳግመኛም ፡ ለሹመት ፡ ወደመገባት ፡ ይመራል ። እነሆ ፡ የሹመት ፡ ትእዛዝ ፡ ከካህናትና ፡ ከሊቃነ ፡ ካህናት ፡ ሹመት ፡ ትእዛዝ ፡ የተነሣ ፡ አስቀድሞ ፡ በመጻሕፍት ፡ ተነግሯልና ፡ በዚህም ፡ ሹመቱ ፡ መልካም ፡ የምትሆንበትንና ፡ ፍርዱ ፡ የምትጸናበትን ፡ የፍርድ ፡ ትእዛዝ ፡ ከዚህ ፡ ዳኛ ፡ ዘንድ ፡ ልናዝዝ ፡ ይገባል ። ቁጥራቸውም ፡ ፲፫ ፡ ትእዛዛት ፡ ናቸው ።

፩ሺ.፬፻፲፭ መጀመሪያቸው ፡ ወንድ ፡ እንዲሆን ፡ ነው ። ይህም ፡ የወንድ ፡ አካለ ፡ መጠን ፡ መድረስን ፡ የፈጸመ ፡ ነው ። አካለ ፡ መጠን ፡ ማድረስም ፡ የጉልምስናን ፡ ሕግ ፡ የፈጸመ ፡ ነው ። ያለዚያስ ፡ አእምሮ ፡ አይደላደልም ። በተላላቆችና ፡ በሽማግሌዎች ፡ በመሰሎቻቸውም ፡ ይፈርድ ፡ ዘንድ ፡ ለሹመት ፡ አያበቃም ። እነዚህን ፡ የመሰሉ ፡ ሰዎች ፡ አካለ ፡ መጠን ፡ ባላደረሰው ፡ ዳኛ ፡ ፊት ፡ ይፈርድላቸው ፡ ዘንድ ፡ ሊቆሙ ፡ አይገባም ። በሚረቱት ፡ ላይ ፡ ነገር ፡ አለ ። በሚረቱት ፡ ላይም ፡ ነገር ፡ አለ ።

፩ሺ.፬፻፲፮ ስለ ፡ ወንዶችም ፡ ወንድ ፡ ለሴት ፡ ገዥዋ ፡

ለብእሲት ፡ በከመ ፡ ይቤ ፡ ሐዋርያ ፡ ወፍትሕኒ ፡ ይደሉ ፡ ለርእሰ ፡ እምትሕተነ ፡ እስመ ፡ ብእሲ ፡ ክቡድ ፡ ልቡና ፡ ውእቱ ፡ ወሎቱ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይፍታሕ ፡ በከመ ፡ ተነግረ ፡ ውስተ ፡ ቀኖናት ፡ ከመ ፡ ብእሲት ፡ ኢትምሀር ፡ ወኢትኩን ፡ እምኁልቈ ፡ ክህናት ፡ ወፈታሕኒ ፡ ኢይኩን ፡ ዘእንበለ ፡ ካህን ።

፩ሺ፩፻፲፯ ወዳግማዊ ፡ ልብ ፡ ምስለ ፡ አእምሮታቲሁ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ጠባይዕ ፡ እንስሳዊ ፡ ወካልኡኒ ፡ ረባናዊ ፡ ወሳልስ ፡ ዘይበቍዖ ፡ እንዘ ፡ የኀሥሥ ፡ ወኢየአክሎ ፡ ውስቴቱ ፡ በዘይስቀል ፡ በአንብሮ ፡ ወውእቱ ፡ ከሀሊ ፡ ተላዊ ፡ ለረኪበ ፡ ጸሕፈት ፡ እላ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ዘይፈሊይት ፡ ፍልጠተ ፡ አበይት ፡ ወውሉደ ፡ አእምሮ ፡ ርትዕ ፡ ዐሪት ፡ ዘይበጽሕ ፡ በትምህርት ፡ ልቡናሁ ፡ ኀበ ፡ ከሚተ ፡ ፍትሕ ፡ ዘኀጸበ ፡ ወፈጸሚ ፡ ዘተኰነበ ፡ እስመ ፡ በከመዝ ፡ ውእቱ ፡ ይፈትሕ ፡ ማእከለ ፡ ማእምራን ፡ ወእኩያን ፡ ወኢይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ዘየሐጽጽ ፡ እምኔሆሙ ፡ ልበ ፡ ወኢ ፡ ዘይውኅድ ፡ አእምሮ ።

፩ሺ፩፻፲፰ ሣልስ ፡ ይኩን ፡ ምእመነ ፡ ኦርቶዶክሳዌ ፡ ወካህነ ፡ በጥዩቅ ።

፩ሺ፩፻፲፱ ራብዕ ፡ ግብረ ፡ ርትዕ ፡ ዘይደሉ ፡ ለፈታሕያን ፡ ወለሰማዕት ፡ ወተዳማሚሁ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ምእመነ ፡ ወጠቢበ ፡ በርትዕ ፡ እምንቅፈት ፡ ወድኅነ ፡ እምነውር ፡ ሀዳእ ፡ ለምሕረት ፡ ወለሥምረት ፡ ተዓጋሤ ፡ በጊዜ ፡ መዓት ፡ ወፈራሄ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወራትዐ ፡ በሃይማኖቱ ፡ በውስተ ፡ ዓለሙ ። እስመ ፡ ዘቦቱ ፡ ሃይማኖት ፡ ወዐቂበ ፡ ርትዕ ፡ ወንጹሕ ፡ ይትከሀሎ ፡ ከመ ፡ ይፍታሕ ፡ ማእከለ ፡ ዐብዳን ፡ ወማእከለ ፡ እንስት ፡ ወላዕለ ፡ ንዋየ ፡ ድኩማን ፡ ወለእለ ፡ ሀለዉ ፡ ታሕተ ፡ ዘይሜግበሙ ፡ ወዘርንቱ ፡ እምእደ ፡ ገጽ ፡ ወለዘአተረየ ፡ ህድአተ ፡ ወትዕግሥተ ፡ ወኢየስተሐቅሮሙ ፡ ወኢይትሌሉ ፡ ፍትሐታቲሆሙ ፡ በእንተ ፡ ዘየገብኡ ፡ ሎቱ ፡ እምነገር ፡ ዘየምሰዮ ። ወዳግማዊ ፡ ናሁ ፡ ተነግረ ፡ ውስተ ፡ አንቀጸ ፡ ሰማዕት ።

፩ሺ፩፻፳ ኃምስ ፡ ይኩን ፡ ግዑዘ ፡ እስመ ፡ ዘኢኮነ ፡ ሥሉጠ ፡ ላዕለ ፡ መግዕቱ ፡ ነፍሱ ፡ ኢይትከ



ስለሆነ ፡ ነው ። ሐዋርያ ፡ ጳውሎስ ፡ እንደተናገረ ፡ (ኤፌ ፡ ፭ ፡ ፳፪) ። ከታችኛው ፡ ይልቅ ፡ ለላይኛው ፡ ፍርድ ፡ ይገባዋል ። ወንድ ፡ አእምሮው ፡ የጸና ፡ ነውና ፡ ይፈርድም ፡ ዘንድ ፡ ለእርሱ ፡ ይገባዋል ። ሴት ፡ እንዳታስተምር ፡ ከካህናትም ፡ ቍጥር ፡ እንዳትሆን ፡ በመጻሕፍት ፡ እንደተነገረ ። ዳኛም ፡ ያለካህን ፡ አይሁን ።

፩ሺ፩፻፲፯ ዳግመኛም ፡ ልብ ፡ ከእውቀቶቹ ፡ ጋር ፡ ነው ። (ያለው ፡ መሆን ፡ ነው) ፡ ከእነርሱም ፡ አንዱ ፡ እንስሳዊ ፡ ጠባይዕ ፡ ነው ። ሁለተኛውም ፡ ጠቃሚ ፡ ነው ። ሲሻውም ፡ የሚጠቀመው ፡ የለም ፡ በማግበር ፡ ወደርሱ ፡ በሚያንጋጥጥ ፡ ግንዛብ ፡ አይበቃም ። ይኸውም ፡ ትጋትን ፡ ለማግኘት ፡ የሚከታተል ፡ ሁኖ ፡ ሳለ ፡ ነው ። የፍርድን ፡ ልዩነት ፡ የሚያውቅና ፡ አእምሮ ፡ ያማረለት ፡ ከድንቁርና ፡ የራቀ ፡ በአእምሮውም ፡ መራቀቅ ፡ የጭንቅና ፡ የተሰወረውን ፡ የፍርድ ፡ ፍጻሜ ፡ ወደ ፡ መግለጽ ፡ የሚደርስ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ነው ፡ እንጂ ። በአዋቆችና ፡ በከፉዎች ፡ መካከል ፡ የሚፈርድ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ነውና ፡ ከእነርሱ ፡ ይልቅ ፡ ልቡን ፡ ያጣ ፡ ዕውቀት ፡ የጐደለው ፡ ሊሆን ፡ አይገባም ።

፩ሺ፩፻፲፰ ሦስተኛ ፡ ኦርቶዶክሳዊ ፡ አማኝና ፡ በእርግጥም ፡ ካህን ፡ ይሁን ።

፩ሺ፩፻፲፱ አራተኛ ፡ ለዳኞችና ፡ ለምስክሮች ፡ ቅን ፡ ሥራ ፡ መሥራት ፡ የሚገባ ፡ ነው ። መጀመሪያው ፡ ግን ፡ የታመነ ፡ ብልህ ፡ ከመነቀፍ ፡ የራቀ ፡ ከነውር ፡ የዳነ ፡ ለምሕረትና ፡ ለመውደድ ፡ ዝግ ፡ ያለ ፡ በቍጣ ፡ ጊዜ ፡ የሚታገሥ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ በዓለሙ ፡ ውስጥ ፡ በሃይማኖት ፡ የቀና ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ይገባል ። ሃይማኖት ፡ ቅንነትና ፡ ንጽሕናንም ፡ መጠበቅ ፡ ያለው ፡ ሰው ፡ በአላዋቆችና ፡ በሴቶች ፡ መካከል ፡ በደካ ፡ አደጎች ፡ ገንዘብም ፡ በሚያስተዳድሩቸውም ፡ ሥር ፡ ሳሉት ፡ ይፈርድ ፡ ዘንድ ፡ ይቻለዋልና ። ፊት ፡ አይቶ ፡ ከማድላት ፡ የራቀ ፡ ይሁን ። ፀጥታንና ፡ ትዕግሥትን ፡ ገንዘብ ፡ ያደረገውን ፡ ሰው ፡ አይናቁት ። ከሚያስቈጣው ፡ ነገር ፡ ወገን ፡ ስለሚመልሱለት ፡ ፍርዱን ፡ አያቃልሉ ። ሁለተኛውም ፡ እነሆ ፡ በአንቀጸ ፡ ሰማዕት ፡ ተነግሯል ።

፩ሺ፩፻፳ አምስተኛ ፡ ነፃነት ፡ ያለው ፡ ይሁን ። ራሱን ፡ ለማስተዳደር ፡ ሥልጣን ፡ ያለው ፡ ያልሆነ ፡

አንቀጽ ፡ ፺፫ ።

ይጺሑ ፡ ፍኖተ ፡ አእምሮ ፡ ዘፍትሕ ፡ ሎንኔ ሆሙ ፡ ለመጻእያን ፡ በበኩነቶሙ ። እስመ ፡ ዘለበወ ፡ አእምሮቶሙ ፡ ለእሉ ፡ ፬ቱ ፡ አሥራው ፡ ይከውን ፡ እምሰብእ ፡ እለ ፡ የአምሩ ፡ ፍትሐ ፡ ወእለ ፡ ያስተሐምሙ ፡ ቦቱ ፡ በፍጻሜ ፡ አበይና ፡ ወአለብዎ ፡ ወብውሕ ፡ ሎቱ ፡ ይረሲ ከመ ፡ ይተርጕም ፡ ወይፍታሕ ፡ ፍትሐ ።

፩ሺ.፬፻፳፰ ዓሥር ፡ ለያእምር ፡ ዘይሠይሞ ፡ ፈታሒ ፡ ዘሀቀበ ፡ እሎንተ ፡ ትእዛዛተ ፡ አመ ፡ በዘአቅደመ ፡ አእምሮተ ፡ ግዕዙ ፡ አው ፡ በኀርዮ ፡ አው በሐተታ ፡ ወኀሢሥ ፡ እምእለ ፡ የአምር ፡ ኪያሆሙ ።

፩ሺ.፬፻፳፱ ፲ወ፩ዱ ፡ ዘጸሐፉ ፡ ሎቱ ፡ መጽሐፈ ፡ መባሕት ፡ ለአወፍዮቱ ፡ ሎንኔ ፡ ፍትሕ ፡ ወተፀምዶቱ ፡ ውስቴታ ፡ ወእምዝ ፡ ያግህዱ ፡ ዘንተ ፡ ወያሰምዑ ፡ ሎቱ ።

፩ሺ.፬፻፴ ፲ወ፪ቱ ፡ ቃለ ፡ ምህሮሁ ፡ ሶበ ፡ አወፈይዎ ፡ መጽሐፈ ፡ መባሕት ፡ አመ ፡ በኀባቡ ፡ አው ፡ በሕግጊሁ ፡ ውስተ ፡ ርእይ ።

፩ሺ.፬፻፴፩ ፲ወ፫ቱ ፡ ኢይክልእዎሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ ለእለ ፡ ውስተ ፡ ሢመቱ ፡ አው ፡ ለመብዝኅቶሙ ፡ ለመጺእ ፡ ኀቤሁ ፡ ወኢይእበይ ፡ ኵሉ ፡ ዘውስተ ፡ ሢመቱ ፡ አው ፡ መብዝኅቶሙ ፡ በእንተ ፡ ከመ ፡ ይሠየም ፡ ላዕሌሆሙ ።

፩ሺ.፬፻፴፪ ምስራፍ ፡ ዳግማዊ ፡ በእንተ ፡ ሥርዓቱ ፡ ለእመስኬ ፡ ኮነት ፡ ሢመቱ ፡ ላዕለ ፡ ኵሉ ፡ ይከውን ፡ ሥሉጠ ፡ ላዕለ ፡ ሰቡዑ ፡ ሎንኔያት ። እሉቱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ፈሊጠ ፡ ጋእዝ ፡ ወመተረ ፡ ባእስ ፡ አመ ፡ በተሳልሞ ፡ ወዕርቅ ፡ እንዘ ፡ ይሜህሩ ፡ አው ፡ በግብር ፡ ፈረሆሙ ።

፩ሺ.፬፻፴፫ ወካልኢትኒ ፡ ካዕበ ፡ አብጽሖተ ፡ ንዋያት ፡ ኀበ ፡ እለ ፡ ይደልዎሙ ፡ ሶበ ፡ ጸንዐት ፡ በእምነተ ፡ አፉሁ ፡ አው ፡ በአጠይቆ ፡ ሰማዕት ።

፩ሺ.፬፻፴፬ ወሣልሲት ፡ ከዊነ ፡ አመግቦ ፡ ላዕለ ፡ ዘይክልእዎ ፡ አስተዋፅኦተ ፡ ንዋይ ፡ እመኒ ፡ በእንተ ፡ ናእስ ፡ አው ፡ በእንተ ፡ ለበዱ ፡ አው ፡ በእንተ ፡ ተሣልቆቱ ፡ ከመ ፡ ይትዐቀብ ፡ ንዋዮሙ ፡ በዘ ይደሉ ፡ ወበእንተ ፡ ጠይቆተ ፡ ፍትሕ ።

፩ሺ.፬፻፴፭ ወራብዕት ፡ በእንተ ፡ አእምሮ ፡ ገዚያት ፡ ዘቄጺረ ፡ ጕልታት ፡ ለሀቂበ ፡ ሥረዊሃ ፡ ወፈሊጠ ፡ አስጼቂሃ ፡ ወኀሢእ ፡ ዘይትረከብ ፡ እም

ስለ ፡ ዳኛ ።

መጡ ፡ የቅጣቶችን ፡ ፍርድ ፡ የማወቅን ፡ ጐዳና ጥርጊያ ፡ ያደርጉ ፡ ዘንድ ፡ ነው ። እሊህን ፡ አራቱን ፡ አሥራው ፡ ማወቅን ፡ ያስተዋለ ፡ ሰው ፡ ፍርድ ፡ ከሚያውቁ ፡ ፍርድንና ፡ ማስተዋልንም ፡ በመፈጸም ፡ ከሚተጉ ፡ ሰዎች ፡ ወገን ፡ ይሆናልና ። እንዲተረጕም ፡ ፍርድም ፡ እንዲፈርድ ፡ ያደርግ ፡ ዘንድ ፡ ይገባዋል ።

፩ሺ.፬፻፳፰ አሥረኛ ። የሚሾመው ፡ ዳኛ ፡ አስቀድሞ ፡ ጠባዩን ፡ በማወቅ ፡ ወይም ፡ በምርጫ ፡ ወይም ፡ እነርሱን ፡ ከሚያውቃቸው ፡ ሰዎች ፡ በመጠየቅና ፡ በመመርመር ፡ እሊህን ፡ ትእዛዛት ፡ የጠበቀ ፡ መሆኑን ፡ ይወቅ ።

፩ሺ.፬፻፳፱ ፲፩ኛ ። የፍርድ ፡ ቅጣት ፡ ለመስጠትና ፡ በውስጧም ፡ በሹመቱ ፡ ጸንቶ ፡ ለመኖር ፡ ለማገልገል ፡ የመብት ፡ ደብዳቤ ፡ ለጻፉለት ፡ ሰው ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ይህን ፡ ይግለጹለት ። ዓዋጅም ፡ ያናግሩለት ።

፩ሺ.፬፻፴ ፲፪ኛ ። የመብት ፡ ደብዳቤ ፡ በሰጡት ፡ ጊዜ ፡ ንባቡን ፡ ወይም ፡ ሕጉን ፡ በመመልከትም ፡ ቢሆን ፡ የማስተማሩ ፡ ነገር ፡ ነው ።

፩ሺ.፬፻፴፩ ፲፫ኛ ። በሹመቱ ፡ ውስጥ ፡ ያሉትን ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ወይም ፡ ብዙዎችን ፡ ወደእርሱ ፡ ለመምጣት ፡ አይከልክሏቸው ። በሹመቱ ፡ ውስጥ ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ወይም ፡ አብዛኛዎቹ ፡ በላያቸው ፡ ስለሚሾምባቸው ፡ እንቢ ፡ አይበሉ ።

፩ሺ.፬፻፴፪ ሁለተኛ ፡ ምዕራፍ ። ስለ ፡ ሥርዓቱ ፡ ይናገራል ። ሹመቱ ፡ በሁሉ ፡ ላይ ፡ ከሆነች ፡ በሰባቱ ፡ ቅጣቶች ፡ ላይ ፡ የሠለጠነ ፡ ይሆናል ። ከእነርሱም ፡ አንዲቱ ፡ በፍቅርና ፡ በዕርቅም ፡ ቢሆን ፡ ተስማምተው ፡ ወይም ፡ በግድ ፡ ፈርተውም ፡ ቢሆን ፡ ፀብ ፡ ክርክርን ፡ ማራቅ ፡ ነው

፩ሺ.፬፻፴፫ ሁለተኛዪቱ ፡ ደግሞ ፡ በአፉ ፡ በማመን ፡ ወይም ፡ በምስክር ፡ በማስረዳት ፡ በጸናች ፡ ጊዜ ፡ ገንዘብን ፡ ለሚገባቸው ፡ ማድረስ ፡ (ማካፈል) ፡ ነው ።

፩ሺ.፬፻፴፬ ሦስተኛዪቱ ። ስለሕፃንነቱ ፡ ወይም ፡ ስለአላዋቂነቱ ፡ ወይም ፡ ስለዋዘኛነቱ ፡ ገንዘቡን ፡ ከማወጣጣት ፡ በሚከለክሉት ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ የማስተዳደር ፡ ሁኔታ ፡ ነው ። ገንዘባቸው ፡ በሚገባ ፡ ይጠበቅ ፡ ዘንድ ፡ ፍርዱንም ፡ ስለ ፡ መረዳት ።

፩ሺ.፬፻፴፭ አራተኛዪቱ ። ጉልቶች ፡ የሚቈጠሩበትን ፡ ጊዜያት ፡ ስለማወቅ ፡ ሥሯን ፡ ለመጠበቅና ፡ ሚዜን ፡ ስለመለየት ፡ ከእርሷ ፡ የሚገኘው

አንቀጽ ፡ ፵፫ ።

ኔሃ ፡ ወእስተዋጽኦቶ ፡ በእንተ ፡ ፍናዋቲሃ ። ወእመኒ ፡ ኮነ ፡ ድልወ ፡ ለአመግቦታ ፡ ይትኖ ለው ፡ እው ፡ ይሜ.ም ፡ ወእምዝ ፡ ያእምር ፡ እማ ኅፀንት ፡ ዘሀለወ ፡ ታሕተ ፡ እደዊሆሙ ፡ ለመ ግብት ፡ ወእምዝ ፡ ግብረ ፡ ይካትም ፡ ወእለ ፡ ሀለዉ ፡ ታሕተ ፡ ምግብና ።

፩ሺ.፩፻፴፮ ኃምሲት ፡ ግቢረ ፡ ትእዛዛት ፡ በከመ ፡ ወስነ ፡ እዛዚ ፡ ወባቲ ፡ አብሒት ፡ ሕግ ፡ እንበለ ፡ ተከ ልእ ፡ ወአመስ ፡ ቦ ፡ ዘአዘዘ ፡ ሎቱ ፡ ኪያሃ ፡ ይኩን ፡ ኖላዌ ፡ ወእመ ፡ አኮ ፡ ይሜ.ም ።

፩ሺ.፩፻፴፯ ሳድሲት ፡ አትልዎ ፡ ለዘይሜኒ ፡ ለፍትሕ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ በምግባር ፡ ዐቢየ ፡ ወኢይከውኖ ፡ ለዘአትለዎ ፡ ለእመ ፡ አትለወ ፡ ካልአ ፡ ዘኢን ግረ ፡ ውእቱ ፡ ሎቱ ። ወእምድኅረ ፡ ሞቱ ፡ ሥዩም ፡ ዘይበቍዕ ፡ ለሢመተ ፡ ፍትሕ ፡ ወለ እመ ፡ ኮነ ፡ ግብረ ፡ ዐቢየ ፡ ወአልቦቱ ፡ ሥል ጣን ፡ ከመ ፡ ይሜ.ም ፡ ይሠዩም ፡ እምነበ ፡ ካልኡ ፡ ዘቦቱ ፡ መባሕት ፡ ለዝንቱ ።

፩ሺ.፩፻፴፰ ሳብዒት ፡ ጥያቄ ፡ ስማዕት ፡ ለይኩኑ ፡ ንጹሓነ እለ ፡ ይከውኑ ፡ ስምዐ ፡ ወእለ ፡ የአምንዎሙ ፡ ወእለ ፡ ኮኑ ፡ ጌራነ ፡ እምላእካኒሁ ፡ ወኅሩይ ፡ ዘእምታሕቴሁ ፡ ከመ ፡ ያንብሮ ፡ ምስለ ፡ ጽን ዐት ፡ ወሃይማኖት ፡ ወከመ ፡ ይወልጥ ፡ ሀየንቴ ሆሙ ፡ እመ ፡ አስተርአየ ፡ ሀኬት ፡ ወስኢን ፡ ላዕሌሆሙ ።

፩ሺ.፩፻፴፱ ወለእመስ ፡ ኮነት ፡ ሢመቱ ፡ እምርት ፡ ዲበ ፡ ፩ዱ ፡ ግብር ፡ ዘእንበለ ፡ ካልኢ ፡ ይከውን ፡ ሕጹጸ ፡ ሢመት ፡ ዘእሁ ፡ ከመ ፡ ዘተውሂደመ ፡ ለአውስበ ፡ ብእሲት ፡ ወአኮ ፡ ላዕለ ፡ ንዋይ ፡ እው ፡ ላዕለ ፡ አሕዛብ ፡ ሀገር ፡ ዘእንበለ ፡ እድ.ያ ሚሃ ፡ ወላዕለ ፡ ፩ዱ ፡ ኅብር ፡ እምሰብእ ፡ ዘእን በለ ፡ ካልአኒሆሙ ፡ በእንተ ፡ ዘአእመረ ፡ ልሳነ ብሔሮሙ ፡ ወፍጥረቶሙ ፡ ዘእንበለ ፡ ካልአ ኒሁ ፡ ወኢይደሉ ፡ ከመ ፡ ይትበደሎ ፡ ዘንቱ ፡ ዘእንበለ ፡ ዳእሙ ፡ በምግብና ።

፩ሺ.፩፻፵ ምዕራፍ ፡ ፫ቱ ፡ በእንተ ፡ ዘይኤዝዝዎ ፡ ቦቱ ፡ ይቤ ፡ እግዚእነ ፡ በወንጌል ፡ ቅዱስ ፡ "ኢትፍ ትሑ ፡ በአድልዎ ፡ አላ ፡ ፍትሑ ፡ ጽድቀ ፡ ፍትሐ ።"

፩ሺ.፩፻፵፩ ድሰቅ ፡ ዘ፩ቱ ፡ ወይደሉ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡

ስለ ፡ ዳኛ ።

ንም ፡ ስለመውሰድ ፡ ስለሥራዎቿም ፡ ስለማወ ጣጣት ፡ ይናገራል ። እርሷን ፡ ለማስተዳደር ፡ የሚገባ ፡ ቢሆን ፡ ይጠብቃት ። ወይም ፡ ይሹም፡ ከዚሀ ፡ በኋላ ፡ ከአደራ ፡ ወገን ፡ በሹማምቱ ፡ እጅ ፡ ያለውን ፡ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ የድኃ ፡ አደጉ ንና ፡ በትድድር ፡ ሥር ፡ ያሉትን ፡ ሰዎች ፡ ሥራ ይወቅ ።

፩ሺ.፩፻፴፮ አምስተኛዪቱ ፡ አዛዥ ፡ እንደወሰነ ፡ ትእ ዛዙን ፡ ማድረግ ፡ ነው ። በእርሷም ፡ ያለመከል ከል ፡ ሕግ ፡ አዝዛለች ። እርሷን ፡ ያዘዘለት ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡ ግን ፡ ጠባቂ ፡ ይሁን ። ይህም ፡ ባይሆን ፡ ይሹም ።

፩ሺ.፩፻፴፯ ስድስተኛዪቱ ፡ በሥራ ፡ ታላቅ ፡ ቢሆን ፡ ለፍርድ ፡ የሚስማማውን ፡ ምክትል ፡ ማድረግ ፡ ነው ። ምክትል ፡ ላደረጉት ፡ እርሱን ፡ ያልነገረ ለትን ፡ (ያልፈቀደለትን) ፡ ሌላውን ፡ ምክትል ፡ ቢያደርግ ፡ አይገባውም ። ለፍርድ ፡ ሹመት ፡ የሚጠቅም ፡ ዳኛ ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ ሥራው ፡ ታላቅም ፡ ቢሆን ፡ ሊሾም ፡ ሥልጣን ፡ የለውም። ለዚህ ፡ መብት ፡ ካለው ፡ ከሌላው ፡ ይሾም ፡ እንጂ ።

፩ሺ.፩፻፴፰ ሰባተኛዪቱ ፡ የምስክሮች ፡ ማስረጃ ፡ ናት ። ምስክር ፡ የሚሆኑ ፡ ሰዎች ፡ ንጹሐንና ፡ የሚያም ኗቸው ፡ ይሁኑ ። ከአገልጋዮቹ ፡ ደጋግ ፡ የሆ ኑት ፡ ከበታቹ ፡ ያለው ፡ ምርጥ ፡ በሃይማኖት ከመጽናት ፡ ጋር ፡ ያኖረው ፡ ዘንድ ፡ ስንፍና ፡ ድካም ፡ በተገለጠባቸው ፡ ጊዜ ፡ ስለእነርሱ ፡ ይለውጥ ፡ ዘንድ ።

፩ሺ.፩፻፴፱ ሹመቱ ፡ በሌላው ፡ ሳይሆን ፡ በአንድ ፡ ሥራ ፡ የታወቀች ፡ ብትሆን ፡ ሹመቱ ፡ ጐደሎ ፡ ይሆ ናል ። በገንዘብ ፡ ያይደለ ፡ ሚስት ፡ ለማግባት ፡ ወይም ፡ በዙሪያዋ ፡ ሳይሆን ፡ በአንዲት ፡ መን ደር ፡ ከባልንጀሮቹ ፡ ተለይቶ ፡ ቋንቋቸውንና ፡ ትውልዳቸውን ፡ ስላወቀ ፡ በመላው ፡ ሳይሆን ፡ ከሰዎች ፡ በ፩ ፡ ወገን ፡ እንደተሾመ ፡ ሰው ፡ በሹ መት ፡ ቢሆን ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ይህን ፡ ሊተላለፍ ፡ አይገባውም ።

፩ሺ.፩፻፵ ሦስተኛ ፡ ምዕራፍ ፡ ስለሚያዝዙበት ፡ ይና ገራል ። ጌታችን ፡ በቅዱስ ፡ ወንጌል ፡ እውነ ተኛ ፡ ፍርድ ፡ ፍረዱ ፡ እንጂ ፡ በአድልዎ ፡ አት ፍረዱ ፡ አለ ። (ዮሐ ፡ ፯ ፡ ፳፬) ።

፩ሺ.፩፻፵፩ ድስቅ ፡ ፩ ። ቅንና ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡

ራትዐ ፡ ወተላዌ ፡ ፈቃዱ ፡ ለእግዚአብሔር ። ዘ፷ቱ ፡ ወነዋ ፡ ተጽሕፈ ፡ ውስተ ፡ መዝሙር ፡ "ወርትዐ ፡ ፍትሑ ፡ እ ፡ ደቂቀ ፡ እጓለ ፡ እመ ሕያው" ። ዘ፲ቱ ፡ ወካዕበ ፡ ይቤ ፡ እግዚአብ ሔር ፡ ኢታድሉ ፡ ለገጸ ፡ ባዕል ፡ በውስተ ፡ ፍትሕ ፡ ወኢትምሐሮ ፡ ለነዳይ ፡ እስመ ፡ ለፍ ትሕ ፡ አልቦ ፡ ውስቴቱ ፡ ምሕረት ፡ ወእእምሩ ዙንቱ ፡ ዙሉን ፡ ኃጣውእ ፡ ዘዘዚአሃ ፡ ከመ ፡ ኢይኩን ፡ እምኔክሙ ፡ ዐመፃ ፡ ለ፩ዱ ፡ ከመ ፡ ኢይትነሣእ ፡ ላዕሌክሙ ፡ መዓተ ፡ እግዚአብ ሔር ፡ በእንተ ፡ ፍትሐ ፡ ዐመፃ ፡ ዘእንትሙ ፡ ፈታሕክሙ ፡ ወውእቱ ፡ ይሴእለክሙ ።

፩ሺ.፬፻፺፪ ወተዐቀቡ ፡ እምተመስሎ ፡ በረበናት ፡ ዘካህ ናት ፡ እለ ፡ ኮኑ ፡ ስምዐ ፡ ላዕለ ፡ ሶስና ፡ በባቢ ሎን ፡ ወፈትሑ ፡ ላዕሌሃ ፡ ፍትሐ ፡ ሞት ፡ በዐ መፃ ፡ ከመ ፡ ኢትኩኑ ፡ ድልዋነ ፡ ለዙንቱ ፡ እም ፈታሕት ። እስመ ፡ ለሶስና ፡ አድኀና ፡ እግዚ አብሔር ፡ እምእደዊሆሙ ፡ ለዐላውያን ፡ ሕግ ፡ በእደ ፡ ዳንኤል ፡ ነቢይ ፡ ወለእልክቱሰ ፡ ረበ ናተ ፡ ካህናት ፡ ቀተሎሙ ፡ በእንተ ፡ ዘአበሱ ፡ ላዕሌሃ ፡ ወወድዮሙ ፡ ውስተ ፡ ዙንቱ ፡ እሳት ።

፩ሺ.፬፻፺፫ ወእግዚአብሔርሰ ፡ የአምር ፡ ፍትሐክሙ ፡ ዘትፈትሑ ፡ ቦቱ ፡ ወኢይትከሀለክሙ ፡ ትጉ ነዩ ፡ እምኔሁ ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ርቱዐ ፡ ፍትሕ ክሙ ፡ ትረክቡ ፡ ለጌሠ ፡ ሠናየ ፡ በርትዕ ፡ እም ኔሁ ፡ በዝ ፡ ዓለም ፡ ወበዘይመጽእኒ ። ወለእ መሰ ፡ ኮነ ፡ ፍትሕክሙ ፡ በዐመፃ ፡ ትረክቡ ፡ እኪየተ ፡ ብዙኀተ ።

፩ሺ.፬፻፺፬ ወእእምሩ ፡ ከመ ፡ ፍርሃተ ፡ ገጽ ፡ ይመጽእ ፡ በነሢአ ፡ እምኃ ፡ ወሕልያን ፡ ወትከውኑ ፡ ከማ ሆሙ ። ይደሉ ፡ ከመ ፡ ኢትትወከፍ ፡ እምኃ ፡ እምእሐዱኒ ፡ ሰበ ፡ ትሁብ ፡ ሢመተ ፡ ዘእንበለ ፡ እምኀበ ፡ ዘእልቦቱ ፡ መባሕት ፡ ዘከመ ፡ ወልድ ወወላዲ ።

፩ሺ.፬፻፺፭ ወያድልዎ ፡ ከመ ፡ የአዝዞ ፡ ለዘይትልዎ ፡ በዘ ተአዘዘ ፡ ቦቱ ፡ ውእቱ ፡ ወከመ ፡ የአዝዞሙ ፡ ለላእካኒሁ ፡ ወለመገብቱ ፡ በምንቴሁ ፡ በፈሪሀ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወበእስተሐምሞ ፡ በእንተ ፡ ኀጢአ ፡ ንዋያት ። ወየአዝዞሙ ፡ ለመርዳእያ ኒሁ ፡ ለምሒክ ፡ በተጸልአ ፡ ወኢይደሉ ፡ ከመ ፡ ይትጋበር ፡ ውስተ ፡ መካነ ፡ ምኵናን ፡ ተጣ



የሚከተል ፡ ሊሆን ፡ ይገባል ። ፯ ። በመዝሙ ርም ፡ እነሆ ፡ ተጽፏል ። የሰው ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፡ እውነት ፡ ፍረዱ ። (መዝ ፡ ፶፰ ፡ ፩) ። ፲ ፡ ዳግ መኛም ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ አለ ። በፍ ርድ ፡ ጊዜ ፡ ለባለጸጋ ፡ ፊት ፡ አታድላ ። ለድኃ ውም ፡ አትዘንለት ፡ አለ ፡ በፍርድ ፡ ውስጥ ፡ ምሕረት ፡ የለምና ። (ዘሌ ፡ ፲፱ ፡ ፲፭) ። ከእናንተ በአንዱ ፡ ላይ ፡ በደል ፡ እንዳይሆን ፡ የኀጢአቶ ችን ፡ ሁሉ ፡ ፍርድ ፡ በየራሷ ፡ እወቁ ። እናንተ ፡ በፈረዳችሁት ፡ የዓመፅ ፡ ፍርድ ፡ የእግዚአብሔ ር ፡ መዓት ፡ በላያችሁ ፡ እንዳይመጣ ፡ እርሱም ፡ ይጠይቃችኋል ።

፩ሺ.፬፻፺፪ በባቢሎን ፡ በሶስና ፡ ላይ ፡ የሐሰት ፡ ምስክ ሮች ፡ የሆኑና ፡ በዓመፅ ፡ የሞት ፡ ፍርድ ፡ የፈረ ዱባትን ፡ የካህናት ፡ መምህራንን ፡ ከመምሰል ፡ ተጠበቁ ። ከዳኞች ፡ ለቅጣት ፡ ዝግጁዎች ፡ እን ዳትሆኑ ። እግዚአብሔር ፡ ሶስናን ፡ በነቢይ ፡ ዳንኤል ፡ ቃል ፡ ከሕግ ፡ አፍራሾች ፡ እጅ ፡ አድ ኗታልና ። እኒህን ፡ የካህናት ፡ መምህራንን ፡ ግን ፡ በእርሷ ፡ ላይ ፡ ስለበደሉ ፡ ገደላቸው ። ወደእሳት ፡ ቅጣትም ፡ ጨመራቸው ። (ተረ ፡ ዳን ፡ ፶፰ ፡ ፷፩) ።

፩ሺ.፬፻፺፫ እግዚአብሔር ፡ ግን ፡ የምትፈርዱትን ፡ ፍርድ ፡ ያውቅባችኋል ። ከእርሱም ፡ ልትሸሸጉ ፡ አትችሉም ። ፍርዳችሁ ፡ የቀና ፡ ቢሆን ፡ በእው ነት ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ በዚህም ፡ ዓለም ፡ በሚመ ጣውም ፡ ዓለም ፡ መልካም ፡ ዋጋ ፡ ታገኛላችሁ ። ፍርዳችሁ ፡ በዓመፅ ፡ ቢሆን ፡ ግን ፡ ብዙ ፡ ፍዳ ፡ ታገኛላችሁ ።

፩ሺ.፬፻፺፬ ፊት ፡ አይቶ ፡ ማድላት ፡ እጅ ፡ መንሻንና ፡ መማለጃን ፡ በመቀበል ፡ እንደሚመጣ ፡ እወቁ ። እንደ ፡ እነርሱም ፡ ትሆናላችሁ ። ሹመት ፡ በሰ ጠኸው ፡ ጊዜ ፡ ካንድ ፡ ሰው ፡ እንኳ ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ እንዳትቀበል ፡ ይገባል ። መብት ፡ ከሌ ለው ፡ ዘንድ ፡ ቢሆን ፡ ነው ፡ እንጂ ። ይኸውም ፡ እንደ ፡ ልጆችና ፡ እንደ ፡ አባት ፡ ያለ ፡ ነው ።

፩ሺ.፬፻፺፭ ምክትሉን ፡ እርሱ ፡ በታዘዘበት ፡ ሊያዝዘው ፡ አገልጋዮችንና ፡ ሹማምቱንም ፡ እግዚአብሔ ርን ፡ በመፍራትና ፡ ገንዘብን ፡ ስለመሻት ፡ በመ ትጋት ፡ ስለእርሱ ፡ ፋንታ ፡ ሊያዝዛቸው ፡ ይገ ባል ። ረዳቶቹንም ፡ በጠብ ፡ ጊዜ ፡ ለመራራት ይዘዛቸው ። በሸንጎው ፡ ቦታ ፡ መገበያየት ፡ ወይም ፡ መሸረክ ፡ ወይም ፡ ይህን ፡ የሚመስለው

አንቀጽ ፡ ፵፫ ።

ያሎ ፡ ወኢ ፡ ተሳትፎ ፡ ወኢ ፡ ዘይመስሎ ፡ ለገዛ ንቲ ፡ ኢ ፡ ለነፍሱ ፡ ወኢ ፡ ለመጋቢሁ ፡ ዘለ ጤቅ ፡ ሎቱ ፡ ወከመ ፡ ኢይትወከፍ ፡ ፩ዱ ፡ እም ተጻላእያን ፡ ዘእንበለ ፡ በዓለ ፡ ዕዳሁ ፡ ወኢ ፡ እምድኅረ ፡ ተፈልጠቶሙ ።

፩ሺ.፬፻፵፮ ምዕራፍ ፡ ራብዕ ፡ በእንተ ፡ ትእዛዛት ፡ ፍትሑ ። ይደልዎ ፡ ቅድመ ፡ ከመ ፡ ያስተርኢ ፡ መጽሐፈ ፡ ሢመቱ ፡ ወይትነበብ ፡ በውስተ ፡ መካነ ፡ ምኵናኑ ፡ ከመ ፡ ያስማዕ ፡ ዜናሁ ፡ ወእምዝ ፡ ያዕርጉ ፡ ሎቱ ፡ ነገረ ፡ ምክንያቶሙ ፡ ለሙቁሓን ፡ ወለዕለ ፡ ሀለዉ ፡ በግዘት ፡ ይፍታሕ ፡ ለዘይደልዎ ፡ ፍትሐት ፡ እምኔሆሙ ፡ ወያኅድግ ፡ ለዘኢይደልዎ ፡ ፍትሐት ። ወእመኒ ፡ በእንተ ፡ ተአምኖቱ ፡ ወበስምዕ ፡ ዘኮነ ፡ ሎቱ ፡ አው በእንተ ፡ አበይዎ ፡ ላዕሌሁ ።

፩ሺ.፬፻፵፯ ወለዘኒ ፡ ይቤ ፡ ግፉዕ ፡ አነ ፡ ወኢሀለወ ፡ በዓለ ፡ ዕዳሁ ፡ ከመ ፡ የሐድስ ፡ ተኳንኖቶ ፡ ይጽሐፍ ፡ መልእክተ ፡ ኀበ ፡ በዓለ ፡ ዕዳሁ ፡ ከመ ፡ ይብጻሕ ፡ ለተኳንኖ ፡ ለእመ ፡ ሀለወ ፡ በመካን ፡ ቅሩብ ፡ ወለእመ ፡ ተድኅረ ፡ ይፍትሑ ፡ ወይፈንዎ ፡ እምድኅረ ፡ ወሀበ ፡ ትሕቢተ ። ወለዘሂ ፡ ተጠየቀ ፡ ከመ ፡ ነዳይ ፡ ውእቱ ፡ ይንሣእ ፡ እምኔሁ ፡ ተሓባዬ ፡ ከመ ፡ ይፍትሑ ፡ እስከ ፡ አመ ፡ ይረክብ ፡ ዘይፈዲ ፡ ሎቱ ፡ ዘተለቅሐ ። ወእምዝ ፡ የአዝዞሙ ፡ ለላእካኒሁ ፡ ከመ ፡ ኢያብኡ ፡ ኀቤሁ ፡ ዕድወ ፡ ዘእንበለ ፡ እድዉ ፡ ወኢያቅድሙ ፡ በዓለ ፡ ዕዳ ፡ እምበዓለ ፡ ዕዳሁ ፡ ወኢ ፡ ለዘተድኅረ ፡ እምነ ፡ ዘቀደመ ።

፩ሺ.፬፻፵፰ ወይደሉ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ሀዱእ ፡ ወኢ ተዓባዬ ፡ ወኢይፍታሕ ፡ እንዘ ፡ ቦቱ ፡ ዘየማስኖ ፡ ለሕሊናሁ ፡ ዘከመ ፡ ቍጥዓ ፡ ወፍርሃት ፡ መሀውከን ። ወዘከመ ፡ ኀዘን ፡ ወፍሥሓ ፡ መርስዓን ፡ ወዘከመ ፡ ረኀብ ፡ ወጽምእ ፡ ነካይያን ፡ ወዘከመ ፡ ደዌ ፡ ወሕማም ፡ አሕማምያን ። ወዘከመ ፡ ንዋም ፡ ወድቃስ ፡ መዋዕያን ፡ ወዘከመ ፡ ሀኬት ፡ ወድካም ፡ አሕማምያን ፡ ወበስካሪ ፡ ወቅሳሴ ፡ ወተእንትሎ ፡ እምብዝኁ ፡ ፈቲሐ ፡ ፍትሕ ። ወኢይደልዎ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ይሠውር ፡ ዘእንበለ ፡ ጊዜያት ፡ ለዕረፍት ፡ ወለገቢረ ፡ መፍቅዳት ።

፩ሺ.፬፻፵፱ ወእምከመ ፡ በጽሐ ፡ ኀቤሁ ፡ ተጻላእያን ፡

ስለ ፡ ዳኛ ።

ለራሱ ፡ ወይም ፡ ለታወቀው ፡ ሹሙ ፡ ሊደረግ ፡ አይገባም ። ከጠበኞች ፡ ሰዎች ፡ አንዱን ፡ ያለባላጋራው ፡ ወይም ፡ ከተለያዩ ፡ በኋላ ፡ ሊቀበል ፡ አይገባም ።

፩ሺ.፬፻፵፮ ፩ኛ ፡ ምዕራፍ ፡ ስለፍርዱ ፡ ትእዛዛት ፡ ይናገራል ። አስቀድሞ ፡ ወሬው ፡ ይሰማ ፡ ዘንድ ፡ የሹመቱ ፡ ደብዳቤ ፡ በአደባባይ ፡ ሊታይና ፡ ሊነበብ ፡ ይገባል ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የታሠሩትን ፡ ሰዎችና ፡ በግዞት ፡ ያሉትን ፡ ሰዎች ፡ ምክንያት ፡ ነገር ፡ ይንገሩት ። በእርሱ ፡ ሥልጣን ፡ ሊፈታ የሚገባውን ፡ ይፍታ ። መፈታት ፡ የማይገባውን ያቆየው ። ስለመታመኑና ፡ ስለ ፡ ተመሰከረለት ፡ ወይም ፡ ስለተፈረደበት ፡ ቢሆን ።

፩ሺ.፬፻፵፯ ከርከሩን ፡ ያድስ ፡ ዘንድ ፡ ባላጋራው ፡ በሌለበት ፡ እኔ ፡ ተበድያለሁ ፡ ቢል ፡ ወደ ፡ ባላጋራው ፡ ደብዳቤ ፡ ይጻፍ ። በቅርብ ፡ ቦታ ፡ ካለ ፡ ለመፈራረድ ፡ ይደርስ ፡ ዘንድ ። ቢቀር ፡ ዋስ ፡ ከሰጠ ፡ በኋላ ፡ ፈትቶ ፡ ይሰደደው ። ድኃ ፡ እንደሆነ ፡ ለታወቀ ፡ ሰው ፡ የተበደረውን ፡ የሚከፍልበት ፡ እስኪያገኝ ፡ ድረስ ፡ ከእርሱ ፡ ዋስ ፡ ይቀበል ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አጋፋሪዎቹን ፡ ባላጋራውን ፡ ከባላጋራው ፡ ለይተው ፡ ወደእርሱ ፡ እንዳያስገቡ ፡ ባለዕዳን ፡ ከባለዕዳው ፡ የኋለኛውንም ፡ ከቀደመው ፡ እንዳያስቀድሙ ፡ ይዘዛቸው ።

፩ሺ.፬፻፵፰ ፀጥ ፡ ያለ ፡ የማይታበይ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ይገባዋል ። አሳቡን ፡ የሚለውጥ ፡ ነገር ፡ እያለበት ፡ አይፍረድ ። ይኸውም ፡ እንደሚያውኩ ፡ እንደ ፡ ቁጣና ፡ እንደ ፡ ፍርሃት ፡ እንደሚያዘናጉ ፡ እንደ ፡ ኀዘንና ፡ እንደ ፡ ደስታ ፡ እንደሚነኩ ፡ እንደ ፡ ረኀብና ፡ እንደ ፡ ፅምእ ፡ እንደሚያሳምሙ ፡ እንደ ፡ ደዌና ፡ እንደ ፡ ሕማም ፡ ድል ፡ እንደሚነሡ ፡ እንደ ፡ እንቅልፍና ፡ እንደ ፡ ሽልብታ ፡ እንደሚያሳዝኑ ፡ እንደስንፍናና ፡ እንደ ፡ ድካም ፡ ያሉ ፡ ናቸው ። በስካርና ፡ በመቅለል ፡ ፍርድን ፡ ከመፍረድ ፡ ብዛት ፡ የተነሣም ፡ በመሰልቸት ፡ አይፍረድ ። ለዕረፍትና ፡ ፈቃድን ፡ ለመፈጸም ፡ በተወሰነው ፡ ጊዜ ፡ ካልሆነም ፡ በቀር ፡ ሊሰወር ፡ አይገባውም ።

፩ሺ.፬፻፵፱ የተጣሉ ፡ ሰዎች ፡ ወደእርሱ ፡ ከመጡ ፡ ጀማሪ

አንቀጽ ፡ ፵፱ ።

ይውሕን ፡ በቀዳማዊ ፡ ዘቀደመ ፡ ወኢይቅድሙ ፡ ለዘይድኅሬ ፡ እምውስተ ፡ ብዙኃ ፡ እምፍትሐት ፡ እሐቲ ። ወእመሰ ፡ እመስተባእሳን ፡ እለ ፡ ጸመዉ ፡ ወእለሂ ፡ በሐዊረ ፡ ፍኖት ፡ አው ፡ በደዌ ፡ ዘተዳደቆሙ ፡ ወይስተማሬ ፡ ማእከለ ፡ መስተባእሳን ፡ በበዊእ ፡ ወበንቢር ፡ ወበተወክሮሂ ፡ ወእስምዖ ፡ ኀቢዮሙ ፡ ወተናግሮ ፡ ሎሙ ፡ ወአርትዖ ፡ ውስተ ፡ ፍትሕ ፡ ሎሙ ፡ ወላዕለ ፡ ሆሙ ፡ ወኢይልጥስስ ፡ ምስለ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ወኢየሀብ ፡ ምክንያተ ፡ ወኢይትበአስ ፡ ወኢያመክኒ ፡ ቦቱ ፡ እመኒ ፡ ኮነ ፡ ጽኑዐ ፡ አው ፡ ድኩመ ፡ አው ፡ ንኡሰ ፡ ወክቡረ ፡ ከመ ፡ ኢይ ምስሎ ፡ ለክቡር ፡ ዘይፈርሆ ፡ ወኢንዴዮ ፡ ወጽ ኑዐ ፡ ከመ ፡ ኢይትቀበጹ ፡ ርትዐ ፡ ዘእዑ ፡ ወኢ ያስተደንግፅ ፡ ግብረ ፡ ፍትሕ ፡ እምከመ ፡ ተጋ እዙ ፡ መስተባእሳን ፡ በእንበለ ፡ በማኅበር ፡ ጽኑዕ

ስለ ፡ ዳኛ ።

በሆነው ፡ በፊተኛው ፡ ሰው ፡ ይጀምር ። በአን ዲት ፡ ፍርድ ፡ ኋለኛውን ፡ ከብዙዎች ፡ አያስቀ ድመው ። ከተጣሉት ፡ ሰዎች ፡ መንገድ ፡ በመ ሄድም ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ ድንገት ፡ ባገኛቸው ፡ ደዌ ፡ የደከሙ ፡ ቢኖሩ ፡ በተጣሉ ፡ ሰዎች ፡ መካ ከል ፡ በመግባትና ፡ በመቀመጥ ፡ በመቀበልና ፡ ወደ ፡ እነሱም ፡ በማዳመጥ ፡ እነርሱንም ፡ በማነ ጋገር ፡ ለእነሱም ፡ ፍርድን ፡ በማቅናት ፡ ትጉ ህ ፡ ይሁን ። ከእነርሱም ፡ ከአንዱ ፡ ጋራ ፡ አያሾክሹክ ፡ (ቀይጽ ፡ አያድርግ) ። ምክንያ ትም  አያስጠው  አያጣለውም ። ብርቱ ወይም ፡ ደካማ ፡ ወይም ፡ ድኃ ፡ ባለጸጋም ቢሆን ፡ አያመካኝበት ። ባለጸጋውን ፡ የሚፈ ሩት ፡ እንዳይመስለው ። ድኃና ፡ ችግረኛም በፍርዱ ፡ ተስፋ ፡ እንዳይቆርጡ ። የተጣሉት ከተከራከሩ ፡ በኋላ ፡ ጽኑ ፡ ችግር ፡ ካልሆነ በቀር ፡ ፍርድ ፡ መስጠትን ፡ ወደኋላ  አያብል ።

፩ሺ.፬፻፶፱ ወኢይፍታሕ ፡ ለርእሱ ፡ ወኢ ፡ ለአሐዱ ፡ እም ወላዲዮሁ ፡ ወኢ ፡ ለእምኒሁ ፡ ወውሉዱ ፡ ወውሉደ ፡ ውሉዱ ፡ ወኢ ፡ ለእኀዊሁ ፡ ወብእ ሲቱ ፡ ምስለ ፡ ካልእኒሆሙ ። ወይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይፍታሕ ፡ ለካልእ ፡ ምስለ ፡ ካልእ ፡ ወከመ ፡ ይፍታሕ ፡ ሎሙ ፡ ምስለ ፡ ካልእኒሆሙ ፡ ለእመ ፈቀዱ ፡ መስተባእሳን ፡ ወይትከወኖ ፡ እንከ ፡ ከመ ፡ ይእበዮ ። ወባሕቱ ፡ እሉ ፡ ይትኃሰኑ ፡ ምስለ  ካልእኒሆሙ ፡ ኀበ ፡ መኳንንት  ወኢ ይከውኖ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ስምዐ ፡ በእንተ እሉሙ ። ወኢይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይፍታሕ ፡ ለጸ ላኢሁ ፡ ወላዕሌሁ ፡ ካዕበ ፡ ወኢይደልዎ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ስምዐ ፡ በላዕሌሁ ፡ እስመ ፡ ግብ ረት ፡ ዘፍትሕ ፡ ከመተት ፡ እሙንቱ ፡ ወማብረ ፡ ከዊነ ፡ ስምዕ ፡ ኀብእት ፡ ይእቲ ።

፩ሺ.፬፻፶፱ ለራሱ ፡ ከወላጆቹም ፡ ስአንደኛው ፡ ወይም ፡ ለእዩቱ ፡ ስልጆቹ ፡ ስልጅ ፡ ልጆቹም ፡ ወይም ፡ ለወንድሞቹ ፡ ለሚስቱም ፡ ከሌሎች ፡ ጋራ ፡ አይፍረድ ። ስሌላው ፡ ከሌላው ፡ ጋራ ፡ የተጣሉ ፡ ሰዎች ፡ ከወደዱ ፡ ከሌሎች ፡ ጋራ ፡ ይፈርድላ ቸው ፡ ዘንድ ፡ ይገባዋል ። እንቢ ፡ ሊልም ፡ እን ግዲህ ፡ ይገባዋል ። ነገር ፡ ግን ፡ እነርሱ ፡ ከሌ ሎች ፡ ጋራ ፡ ከሹሙ ፡ ዘንድ ፡ ይፋረዱ ። ስለነር ሱም ፡ ምስክር ፡ ሊሆን ፡ አይገባውም ። ዳግመ ኛም ፡ በጠላቱ ፡ ላይ ፡ ሊፈርድ ፡ አይገባውም ። በእርሱም ፡ ምስክር ፡ ሊሆን ፡ አይገባውም ። የፍርድ ፡ ሥራዎች ፡ ግልጾች ፡ ናቸውና ። የምስ ክርነት ፡ ሁኔታ ፡ ሥራ ፡ ግን ፡ የተሰወረች ፡ ናትና ።

፩ሺ.፬፻፶፮ ወእምከመ ፡ ፈትሐ ፡ ፍትሐ ፡ ለፅዱ ፡ ወእ ምዝ ፡ ተሐደሰ ፡ እምሳሌሁ ፡ ዘከማሁ ፡ ይደ ልዎ ፡ ከመ ፡ ይፍታሕ ፡ ቦቱ ፡ በዘየበጽሕ ፡ ጸሕቆ ፡ ኀቢሁ ፡ በውእቱ ፡ ጊዜ ፡ ወእመኒ ፡ ኢተባረ ፡ ምስለ ፡ ፍትሑ ፡ ዘቀደመ ፡ ፈተሐ ፡ ከማሁ ፡ እምሳሊሁ ። ወኢያብጥል ፡ ፍትሖ ፡ ነፍሱ ፡ ወኢ ፡ ፍትሐ ፡ ካልኡ ፡ በእንበለ ፡ ለእመ ፡ ወለወ ፡ ነገረ ፡ ሕገዊ ፡ ዘኢተባረ ፡ ምስለ ፡ ቃለ ፡ ሕግ ፡ ገሃደ ፡ አው ፡ በትርጓሜ ፡ አው ፡ በትእዛዝ ፡ ቀኖናት ፡ ዘተጋብኡ ፡ በእ

፩ሺ.፬፻፶፮ ለአንዱ ፡ ፍርድ ፡ ቢፈርድ ፡ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ እንደዚሁ ፡ የመሰለ ፡ ቢታደስ ፡ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ እሳቡን ፡ ወደ ፡ እርሱ ፡ በሚያደርስ ፡ ገንዘብ ፡ ሊፈርድበት ፡ ይገባዋል ። በመጽሐፍ ፡ ከቀደ መው ፡ ፍርዱ ፡ ጋራ ፡ ምንም ፡ ባይተባበር ፡ ምሳሌው ፡ እንደዚሁ ፡ ነው ። የራሱን ፡ ፍርድ ፡ ወይም ፡ የሌላውን ፡ ፍርድ ፡ አይለውጥ ። ከሕግ ቃል ፡ ጋራ ፡ የማይተባበር ፡ ሕጋዊ ፡ ነገርን ፡ በግልጽ ፡ ወይም ፡ በትርጓሜ ፡ ወይም ፡ አባቶች ገንዘብ ፡ ባደረጉት ፡ እውቀት ፡ ስለእነርሱ ፡

አንቀጽ ፡ ፺፫ ።

ንቲአሆን ፡ አበው ፡ በአእምሮ ፡ ዘአጥረይዎ ፡ እሙ ፡ ዘይመስሉ ፡ ለልቡናሁ ፡ አእምሮ ፡ እስመ ፡ ተመይጠተ ፡ ርትዕ ፡ ይኄይስ ፡ እምተኅልፎ ፡ ሳዕለ ፡ ቃል ፡ ስሩዕ ፡፡ ወይፍታሕ ፡ በዘተ ግህደ ፡ እምቃል ፡ እሙንቱ ፡ ውስተ ፡ መንበረ ፡ ፍትሕ ፡ ለእመ ፡ ተጠየቀ ፡ አእምሮቱ ፡ በኅቡእ ፡ ወበኅበ ፡ ትእማኒ ፡ እው ፡ በዘተከሥተ ፡ በስማዕት ፡ ለእመ ፡ ቆመ ፡ እው ፡ መሐላ ፡ ለእመ ፡ ይለወ ፡ ወኢይፍታሕ ፡ ሳዕለ ፡ ዘኢየአምሮ ፡ ዘእንበለ ፡ ግጸዌ ፡፡

፩ሺ፩፻፶፪ ምስራፍ ፡ ኃምስ ፡፡ በእንተ ፡ መሐላ ፡ ይቤ ፡ ጳውሎስ ፡ ሐዋርያ ፡ ሰብ ፡ ፮፡፲ ፡ "ወመሐላስ ፡ ዘይምሕል ፡ ሰብእ ፡ በዘውእቱ ፡ የዐቢ ፡ እምኔሁ ፡ ይምሕል ፡ ወኵሉ ፡ ኃእዝ ፡ ዘትከውን ፡ ማእከሌሆሙ ፡ ትትፌጸም ፡ በመሐላ ፡፡ ወበእንተ ፡ ውእቱ ፡ ፈድፋደ ፡ አፍቀረ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከመ ፡ ያርኢ ፡ ለወራስያን ፡ ተስፋ ፡ ከመ ፡ ተስፋሁ ፡ ኢየዐሉ ፡ ወአጽንዖ ፡ በቃለ ፡ መሐላ" ፡፡ ወሶበ ፡ ኢዘሎ ፡ ምንትኒ ፡ ዘየዐቢ ፡ እምኔሁ ፡ ከመ ፡ ይምሐል ፡ ቦቱ ፡ መሐለ ፡ በር እሱ ፡ ወይቤ ፡ እን ፡ ባርኮ ፡ እባርከከ ፡ ወአብዝኆ ፡ አስተባዝኀከ ፡፡ ወቃለ ፡ እግዚእነ ፡ ዘውስተ ፡ ወንጌል ፡ ዘይቤ ፡ ኢትምሐሉ ፡ ግሙራ ፡ ወእከ ፡ ዘይቤ ፡ በእንተ ፡ ተፋትሖተ ፡ አላ ፡ ይቤ ፡ በእንተ ፡ ተናግሮ ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ፈጸመ ፡ ዘንተ ፡ ቃለ ፡ በቃሉ ፡ ዘይብል ፡ ለትኩን ፡ ቃልክሙ ፡ እመኒ ፡ እወ ፡ እወ ፡ ወእመኒ ፡ አልቦ ፡ አልቦ ፡፡ ወይቤ ፡ ካዕበ ፡ ዘተወሰከስ ፡ ላዕለ ፡ ዝንቱ ፡ እምእኩይ ፡ ውእቱ ፡፡ ወተወስኮስ ፡ ይእቲ ፡ እንተ ፡ ኢይትፈቀድ ፡ ኀቢያ ፡ ወከዊነ ፡ መሐላስ ፡ በጊዜ ፡ ኃእዝ ፡ ናሁ ፡ ይትፈቀድ ፡ በበይነ ፡ ግብር ፡ ወባሕቱ ፡ ይደሉ ፡ ለሰብእ ፡ ከመ ፡ ኢይምሐል ፡ በዘይትከሀሎ ፡ ይቤሎ ፡ መሐላሁ ፡ በንዋዩ ፡ ወዘእንበለ ፡ ንዋዩ ፡ በእንተ ፡ ሰበየ ፡ እግዚአብሔር ፡ ባሕቲቱ ፡ ወበእንተ ፡ ዘይሴፎ ፡ በሀሰወ ፡ ኀቢሁ ፡፡

፩ሺ፩፻፶፫ ወይቤ ፡ ቅዱስ ፡ ዮሐንስ ፡ አፈወርቅ ፡ በውስተ ፡ ትርጓሜ ፡ ዝንቱ ፡ ቃል ፡ ወእመ ፡ ትቤ ፡ ምንት ፡ ይእቲ ፡ መሐላ ፡ እንተ ፡ የኀሥሥ ፡ ወይ መጽእ ፡ ወይሁብ ፡ ሎቱ ፡ እምኔነ ፡ ለቢጹ ፡ በጊዜ ፡ ፈቀደ ፡ ኪያሃ ፡ እቤ ፡ በፈሪሀ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይእቲ ፡፡ ወዘኒ ፡ ይገብር ፡ በሕገ ፡ ትእ

ስለ ፡ ዳኛ ፡፡

በተሰበሰቡ ፡ በመጻሕፍት ፡ ትእዛዝ ፡ ወይም ፡ ለል ቡናው ፡ በመሰለው ፡ ሕጋዊ ፡ ነገርን ፡ ካልለ ወጠ ፡ በቀር ፡ ወደማይጠቅም ፡ ነገር ፡ ከመተላ ለፍ ፡ ይልቅ ፡ ወደ ፡ ቅን ፡ ነገር ፡ መመለስ ፡ ይሻላልና ፡ እወቅ ፡፡ በፍርድ ፡ አደባባይ ፡ ከታ መነው ፡ ቃል ፡ የተነሣ ፡ በተገለጸለት ፡ ገንዘብ ፡ በእርሱና ፡ በታማኙ ፡ ዘንድ ፡ እውቀቱ ፡ ቢረጋ ገጥ ፡ ወይም ፡ በምስክሮቹ ፡ በተገለጸው ፡ ነገር ፡ ቢጸና ፡ ወይም ፡ መሐላ ፡ የሚገባው ፡ ቢሆን ፡ ይፍረድ ፡፡ በማያውቀውም ፡ ላይ ፡ ሳይለይ ፡ አይ ፍረድ ፡፡

፩ሺ፩፻፶፪ ፭ኛው ፡ ምዕራፍ ፡ ስለመሐላ ፡ ይናገራል ፡፡ ሐዋርያ ፡ ጳውሎስ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡፡ ዕብ ፡ ፮ ፡፡ መሐላስ ፡ የሚምል ፡ ሰው ፡ ከእርሱ ፡ በሚበ ልጥ ፡ ይምላል ፡፡ በመካከላቸው ፡ የምትደረግ ፡ ክርክር ፡ ሁሉ ፡ በመሐላ ፡ ትፈጸማለች ፡፡ ስለዚ ህም ፡ ተስፋ ፡ ለሚወርሱ ፡ ተስፋውን ፡ እንዳያ ስቀር ፡ ይገልጽ ፡ ዘንድ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፈጽሞ ወደደ ፡፡ በመሐላ ፡ ቃልም ፡ አጸናው ፡፡ ይምልበ ትም ፡ ዘንድ ፡ ከእርሱ ፡ የሚበልጥ ፡ ምንም ፡ ስለሌለ ፡ መባረክን ፡ እባርክሃለሁ ፡ መብዛትንም እበዛሃለሁ ፡ ብሎ ፡ በራሱ ፡ ማለ ፡፡ (ዕብ ፡ ፮ ፡ ፲፫ - ፲፰) ፡፡ ጌታችንም ፡ በወንጌል ፡ ከቶ ፡ አትማሉ ፡ ያለው ፡ ቃል ፡ ስለመፋረድ ፡ አይደለም ፡፡ ስለ መናገር ፡ ተናገረ ፡ እንጂ ፡፡ ይህንን ፡ ትእዛዝ ፡ እርሱ ፡ ራሱ ፡ ቃላችሁ ፡ እውነቱን ፡ እውነት ፡ ሐሰቱን ፡ ሐሰት ፡ ትሁን ፡ በሚል ፡ ቃሉ ፡ ፈጽ ሞታልና ፡፡ ዳግመኛም ፡ በዚህ ፡ ላይ ፡ የተጨመ ረውስ ፡ ከክፉ ፡ የተገኘ ፡ ነው ፡ አለ ፡፡ (ማቴ ፡ ፭ ፡ ፴፯ - ፴፯) ፡፡ በእርሷ ፡ ላይ ፡ መጨመርስ ፡ የማ ትፈለግ ፡ ናት ፡፡ በክርክር ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ የመሐላ ሁኔታ ፡ በግልጽ ፡ ያስፈልጋል ፡፡ ነገር ፡ ግን ሰሰው ፡ መሐላውን ፡ በገንዘብ ፡ ወይም ፡ ያለገን ዘብ ፡ ማስቀረት ፡ በሚቻለው ፡ ሁናቴ ፡ ስለእግ ዚአብሔር ፡ ገናናነት ፡ ብቻ ፡ በእርሱም ፡ ያለ ውን ፡ ተስፋ ፡ ስለሚያደርግ ፡ እንዳይምል ፡ ይገባዋል ፡፡

፩ሺ፩፻፶፫ ቅዱስ ፡ ዮሐንስ ፡ አፈ ፡ ወርቅም ፡ ይህን ፡ ቃል በተረጐመበት ፡ አንቀጽ ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡፡ መሐ ላ ፡ ምንድር ፡ ናት ? ፡ ብትል ፡ ከእኛ ፡ አንዱ ፡ በጓደኛው ፡ ላይ ፡ እርሷን ፡ በወደደ ፡ ጊዜ ፡ የሚ ሻት ፡ የሚያመጣት ፡ የሚሰጣት ፡ መሐላ ፡ እግ ዚአብሔርን ፡ በመፍራት ፡ ናት ፡ እላለሁ ፡፡ የመ

ዛዛት ፡ መሢሐውያት ፡ ኢይፈቅድ ፡ መሐላ ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ይከውን ፡ በኀበ ፡ ሰብእ ፡ ፍሩሀ ፡ ወእግዚአብሔር ፡ ይከውኖ ፡ ረዳኤ ።

፩ሺ፬፻፶፰ በስ ፡ ፪ቱ ፡ ኢትምሐል ፡ በስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእንተ ፡ ግብር ፡ ዕሩቅ ፡ ወፈድፋደሰ ፡ በሐሰት ፡ ወናሁ ፡ አዘዘነ ፡ ከመ ፡ ኢንምሐል ፡ በካልእ ፡ እምትእዛዛተ ፡ መጻሕፍት ፡ እላ ፡ ለእመ ፡ ኮነ ፡ በግብር ፡ ንምሐል ፡ በእንተ ፡ ሕጸተ ፡ እእምሮቶሙ ፡ ለሰብእ ፡ ወእኮ ፡ ዘእንበለ ፡ ፍርሀተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከመ ፡ ኢንትኩነን ፡ በመሐላ ፡ ዘምሉእ ፡ ፍርሀተ ። ዘ፹ወ፫ቱ ፡ ወእመቦ ፡ እምኍልቈ ፡ ካህናት ፡ ዘይምሕል ፡ በስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ በሐሰት ፡ ይሰደድ ፡ ፫ተ ፡ ዓመተ ፤

፩ሺ፬፻፶፱ መክ ፡ ፶ወ፰ቱ ፡ ፻፳ወ፺ቱ ፡ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ማእከለ ፡ ፪ቱ ፡ እደው ፡ ተሰናእዎት ፡ በተግባር ፡ እው ፡ ተሳትፎት ፡ እው ፡ ኪዳን ፡ ወጸሐፉ ፡ ማእከሌሆሙ ፡ መጽሐፈ ፡ ጥዩቀ ፡ ለአጽንዖ ፡ መሐላ ፡ ዘማእከሌሆሙ ፡ ከመ ፡ ውእቶሙ ፡ ኢይገብኡ ፡ እምዘተሰነአዉ ፡ ቦቱ ። ወለእመ ፡ ገብአ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ እምነ ፡ ዘተጽሕፈ ፡ ይገሥጽ ፡ መኰንን ፡ በእንተ ፡ መሐላሁ ፡ በሐሰት ፡ ወይደልዎ ፡ ይግበር ፡ ዘሀለወ ፡ ጽሑፈ ፡ በመጽሐፍ ። መጅ ፡ ፳ወ፩ዱ ፡ ወዘሂ ፡ ፈትሐ ፡ ላዕሌሁ ፡ መኰንን ፡ ከመ ፡ ይምሐል ፡ ወአንበረ ፡ እዴሁ ፡ ላዕለ ፡ ወንጌል ፡ ቅዱስ ፡ ወመሐለ ፡ ቦቱ ፡ ወእምዝ ፡ ተከሥተ ፡ ሐሰቱ ፡ ይትገሠጽ ።

፩ሺ፬፻፷ ክፍል ፡ አእምር ፡ ከመ ፡ እምላካዊት ፡ ሕግ ፡ ናሁ ፡ ትፈቅድ ፡ ሥነ ፡ ምግባራት ፡ በእግብዖርትዕ ፡ በጥንተ ፡ ቀዳሚ ፡ ሕግ ፡ እምገቢ ፡ ቁሙ ፡ ግብራት ፡ ኀብእት ፡ ወገቢር ፡ በውስተ ፡ ሕግ ፡ ደኀሬ ፡ ወንዋ ፡ ነበረ ፡ ተከልአ ፡ በውስተ ፡ ሕግ ፡ ብሊት ፡ እመሐላ ፡ በሐሰት ፡ ወከመ ፡ ይትገሠጽ ፡ ዘወድቀ ፡ ቦቱ ። ወመሐላሰ ፡ በውስተ ፡ ሕግ ፡ ሐዲስ ፡ በፍትሐ ፡ ልቡና ፡ ውእቱ ፡ ከመ ፡ ኢይንብቡ ፡ ቦቱ ፡ ግሙራ ፡ በእንተ ፡ ዘይቤ ፡ እግዚእነ ፡ በወንጌል ፡ “ተብህለ ፡ ለቀደምትክሙ ፡ ኢተሐስዉ ፡ ውስተ ፡ መሐላ ፡ ወአንሰ ፡ እብለክሙ ፡ ኢትምሐሉ ፡ ግሙራ ።” ።



ሚሕን ፡ የትእዛዛት ፡ ሕግንም ፡ የሚሠራ ፡ መሐላን ፡ አይሻም ። እርሱ ፡ በሰው ፡ ዘንድ ፡ የተፈራ ይሆናልና ። እግዚአብሔርም ፡ ረዳት ፡ ይሆነዋልና

፩ሺ፬፻፶፰ በስ ፡ ፪ ። በተርታ ፡ ነገር ፡ ይልቁንም ፡ በሐሰት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ አትማል ። ከመጻሕፍትም ፡ ትእዛዝ ፡ ወጥተን ፡ በሌላ ፡ እንዳንምል ፡ እነሆ ፡ አዝዞናል ። በሰዎች ፡ እውቀተ ፡ ማነስ ፡ በግድ ፡ እንድንምል ፡ ቢሆን ፡ ነው ፡ እንጂ ። ፍርሃትን ፡ በተመላ ፡ መሐላ ፡ እንዳይፈረድብንም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያለመፍራት ፡ አይሁን ። ፹፫ ። ከካህናት ፡ ወገን ፡ በሐሰት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ የማለ ፡ ቢኖር ፡ ፫ ፡ ዓመት ፡ ይለይ ።

፩ሺ፬፻፶፱ መክ ፡ ፶፰ ፡ ፻፳፺ ። በሁለት ፡ ሰዎች ፡ መካከል ፡ የሥራ ፡ ስምምነት ፡ ወይም ፡ ሽርክነት ፡ ወይም ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ቢኖር ፡ በመካከላቸውም ፡ ያለውን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ለማጽናት እነርሱ ፡ ከተስማሙበት ፡ ውል ፡ እንዳይመለሱ፡ የሚያረጋግጥ ፡ ደብዳቤ ፡ በመካከላቸው ፡ ቢጽፉ ፡ ከእነርሱም ፡ አንዱ ፡ ከተጻፈው ፡ ውል ፡ ቢመለስ ፡ በሐሰት ፡ ስለመማሉ ፡ ዳኛ ፡ ይቅጣው ። በመጽሐፍ ፡ ተጽፎ ፡ ያለውንም ፡ ያድርግ ፡ ዘንድ ፡ ይገባዋል ። መጅ ፡ ፳፩ ። ዳኛ ፡ እንዲምል ፡ የፈረደበትም ፡ ሰው ፡ እጁንም ፡ በቅዱስ ፡ ወንጌል ፡ ላይ ፡ ጭኖ ፡ ቢምልበት ፡ ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ሐሰቱ ፡ ቢገለጽ ፡ ይቀጣ ።

፩ሺ፬፻፷ ክፍል ። እነሆ ፡ የአምላክ ፡ ሕግ ፡ በመጀመሪያው ፡ ሕግ ፡ መሠረትነት ፡ ርትዕን ፡ በማግለጽ ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ በተሠወረች ፡ ሥራ ፡ በመጽናት ፡ በኋለኛውም ፡ ሕግ ፡ በመሥራት ፡ የምግባራትን ፡ ደግነት ፡ እንደምትወድ ፡ እወቅ ። እነሆ ፡ በብሉይ ፡ ሕግም ፡ በሐሰት ፡ ከመማል ፡ መከልከል ፡ እንዲገባ ፡ የወደቀበትም ፡ እንዲቀጣ ፡ ተጽፏል ። (ዘዳ ፡ ፭ ፡ ፲፩) ። በሐዲስ ፡ ሕግ ፡ ግን ፡ በልቡና ፡ ፍርድ ፡ መሐላ ፡ ከቶ ፡ የማይናገሩት ፡ ነው ። ጌታችን ፡ በወንጌል ፡ ከእናንተ ፡ በፊት ፡ ለነበሩት ፡ ሰዎች ፡ በሐሰት ፡ አትማሉ ፡ የተባለውን ፡ ሰምታችኋል ፤ እኔ ፡ ግን ፡ ከቶ ፡ አትማሉ ፡ እላችኋለሁ ፡ ስላለ ፡ ነው ። (ማቴ ፡ ፭ ፡ ፴፫ - ፴፯)

እንቀጽ ፡ ፵፫ ።

ወእለ ፡ ይበጽሑ ፡ ኀቤሁ ፡ ወእለሂ ፡ ኢይበጽሑ ድስቅ ፡ ፲ቱ ፡ ለየሀልዉ ፡ ምስሌክሙ ፡ ኤጲስ ቆጶሳት ፡ በመንበረ ፡ ፍትሕ ፡ ቀሳውስት ፡ ወዲ ያቆናት ፡ ወፍትሑ ፡ ዘእንበለ ፡ አድልዎ ፡ በር ትዕ ፡ ከመ ፡ ሰብአ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወእእምሩ ፡ ከመ ፡ ክርስቶስ ፡ ወልደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሀልው ፡ ውእቱ ፡ ምስሌክሙ ፡ በሀውደ ፡ ፍትሕ ፡ ከመ ፡ ይርአይ ፡ ዘትፈትሑ ፡ ቦቱ ፡ ወይሰማዕ ፡ ዘትትናገሩ ፡ ቦቱ ፡ ወናሁ ፡ ይቤ ፡ በውስተ ፡ ሕግ ፡ ኢትጎበር ፡ ምስለ ፡ ብዙኃን ለገቢረ ፡ እከይ ፡ ወኢትትወከፍ ፡ ነገረ ፡ ዕሩዐ ፡ ወኢትንበር ፡ ውስተ ፡ ማኅበርሙ ፡ ለእለ ፡ ያፀ ርው ፡ ጽድቀ ።

፩ሺ.፩፻፷፭ ክፍል ፡ ወይደሉ ፡ ከመ ፡ ያስተዳልዉ ፡ ለፈ ታሕት ፡ ምንባረ ፡ ንጹሐ ፡ ወጽሩየ ፡ ኀበ ፡ ኢይ ለክፎሙ ፡ ቍር ፡ ወኢሐሩር ፡ ወኢጺእት ፡ በውስቴታ ፡ ወኢይንበሩ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ ክርስ ቲያን ፡ በምሥዋዕ ፡ ለፈቲሐ ፡ ፍትሕ ፡ እስመ ፡ በዋእ ፡ ኀበ ፡ ምሥዋዕ ፡ ኢብውሕ ፡ ዘእንበለ ፡ ለካህናት ፡ ከመ ፡ ይባኡ ፡ ወኢይደሉ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ውስቴቱ ፡ ተባእሶ ፡ ወክሳሕ ።
ወመፍትው ፡ ከመ ፡ የሀልዉ ፡ ኀቤሁ ፡ ማእም ራን ፡ ወእለ ፡ ይከውኑ ፡ ሰምዐ ፡ ከመ ፡ ሶበ ፡ ተዳደቆ ፡ ጠዋይ ፡ ነገር ፡ ከመ ፡ ይትማከር ፡ ምስሌሆሙ ፡ በእንቲአሁ ። ወለእመኒ ፡ ኢተ ጠየቀ ፡ ፈቲሐ ፡ ፍትሕ ፡ ያስተድኅር ፡ ኪያሁ ፡ እስከ ፡ ይጤየቅ ።

፩ሺ.፩፻፷፮ ምዕራፍ ፡ ፯ቱ ። በእንተ ፡ ጊዜያተ ፡ ፍትሕ ፡ ወክዋኔሁ ። መክ ፡ ፱ ፡ ኢይሥርዑ ፡ መኳንንት ፡ በምንትኒ ፡ እምሥርዓታቲሆሙ ፡ በዕለተ ፡ እሑድ ፡ ወኢያፍርሁ ፡ በውስቴቱ ፡ ሰብአ ፡ ኢ ፡ በዓለ ፡ ዕዳ ፡ ወኢ ፡ መኰንን ፡ ወኢ ፡ ሐራ ፡ ወኢ ፡ መጸብሐዊ ።

፩ሺ.፩፻፷፯ ድስቅ ፡ ፲ቱ ፡ ወይኩን ፡ ተጋብእትክሙ ፡ በእንተ ፡ ፍትሕክሙ ፡ እምዕለተ ፡ ሰኑይ ፡ ወለ እመ ፡ ሀለወ ፡ ሀየ ፡ ተጋእዞ ፡ ፍልጡ ፡ ኪያሃ ፡ ወኩኑ ፡ ዕሩቃነ ፡ በዝንቱ ፡ ኑኀ ፡ ይእቲ ፡ ሰሙን ፡ እስከ ፡ ዕለተ ፡ ሰንበት ፡ ከመ ፡ ትትፈ ጸም ፡ ነገረ ፡ ተባእሶ ። ወበዕለተ ፡ እሑድ ፡ ቅድ ስት ፡ ትከውኑ ፡ እንከ ፡ ዘፍሁ ፡ አስተሳለም ክሙ ፡ ማእከለ ፡ ተጻብእያን ፡ ወእምከመ ፡ በጽሑ ፡ ኀቤክሙ ፡ ተጻላእያን ፡ ይቁሙ ፡ ክል ኤሆሙ ፡ በቅድሜክሙ ፡ ማእከለ ፡ መንበረ ፡

ስለ ፡ ዳኛ ።

ወደእርሱ ፡ ስለሚደርሱና ፡ ስለማይደርሱ ፡ ይና ገራል ። ድስቅ ፡ ፲ ፡ ኤጲስቆጶሳት ፡ ሆይ ፡ ከፍ ርድ ፡ ሸንጎ ፡ ቀሳውስትና ፡ ዲያቆናት ፡ ከእና ንተ ፡ ጋር ፡ ይኑሩ ። የእግዚአብሔርም ፡ ሰዎች ፡ እንደመሆናችሁ ፡ ያለ ፡ አድልዎ ፡ በእውነት ፡ ፍረዱ ። የእግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ክርስቶስ ፡ የምትፈርዱትን ፡ ሊያይ ፡ የምትናገሩትንም ሊሰማ ፡ በፍርድ ፡ አደባባይ ፡ ከናንተ ፡ ጋር ፡ እንዳለ ፡ እወቁ ። እነሆ ፡ በመጽሐፍ ፡ ክፋትን ፡ ለመሥራት ፡ ከብዙዎች ፡ ጋራ ፡ አትተባበር ፡ የማይረባ ፡ ነገርንም ፡ አትቀበል ፡ እውነትን ፡ በማይናገሩ ፡ ሰዎች ፡ ስብሰባ ፡ ውስጥም ፡ አት ቀመጥ ፡ ተብሏል ። (ሚራ ፡ ፳ ፡ ፲፱) ።

፩ሺ.፩፻፷፭ ክፍል ፡ ብርድና ፡ ሐሩር ፡ ክፉ ፡ ሽታም ፡ ከማያገኛቸው ፡ ንጹሕና ፡ ጥሩ ፡ መቀመጫ ፡ ለዳኞች ፡ ሊያዘጋጁ ፡ ይገባል ። በሚሠዋበት በቤተክርስቲያን ፡ ውስጥ ፡ ፍርድ ፡ ለመፍረድ ፡ አይቀመጡ ። ወደ ፡ ምሥዋዕ ፡ መግባት ፡ ከካህ ናት ፡ በቀር ፡ ሌሎች ፡ ይገቡ ፡ ዘንድ ፡ አይገባ ምና ። ጠብና ፡ ጩኸት ፡ በውስጡ ፡ ሊሆን ፡ አይገባም ። አዋቂዎችና ፡ ምስክር ፡ የሚሆኑ ፡ ሰዎች ፡ ጠማማ ፡ ነገር ፡ ባጋጠመው ፡ ጊዜ ፡ ስለእርሱ ፡ ከእነርሱ ፡ ጋር ፡ እንዲማከር ፡ ከእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ሊኖሩ ፡ ይገባል ። ፍርዱም ፡ ያልተረዳው ፡ ቢሆን ፡ እስኪረዳው ፡ ድረስ ፡ ያቆይ ።

፩ሺ.፩፻፷፮ ሰባተኛ ፡ ምዕራፍ ፡ ስለፍርድ ፡ ጊዜያትና ፡ ስለሁኔታው ፡ ይናገራል ። መክ ፡ ፱ ። መኳንንት በዕለተ ፡ እሑድ ፡ ከሥርዓታቸው ፡ ወገን ፡ በም ንም ፡ አይሥሩ ። በዚያም ፡ (በእሑድ ፡ ቀን) ፡ አበዳሪና ፡ ዳኛ ፡ ቊፍራና ፡ ቀራጭም ፡ ሰውን ፡ አያስፈሩሩ ።

፩ሺ.፩፻፷፯ ድስቅ ፡ ፲ ። ስለፍርዳችሁ ፡ መሰብሰባችሁ ፡ ከሰኞ ፡ጀምሮ ፡ ይሁን ። ከዚያም ፡ ክርክር ፡ ቢኖ ር ፡ እርሱን ፡ ለዩ ። በዚህ ፡ በዚህች ፡ ሳምንት ፡ ርዝመትም ፡ እስከ ፡ ቅዳሜ ፡ ድረስ ፡ ከነገር ፡ ተለዩ ። የጠብ ፡ ነገር ፡ ይፈጸም ፡ ዘንድ ። በከበ ረች ፡ በዕለተ ፡ እሑድም ፡ እነሆ ፡ በተጣሉት ፡ መካከል ፡ አስታራቂዎች ፡ ትሆናላችሁ ። የተጣ ሉ ፡ ሰዎችም ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ ቢደርሱ ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፡ ባህል ፡ በፍርድ ፡ ሸንጎ ፡ መካከል ፡ ሁለ ቱም ፡ በፊታችሁ ፡ ይቁሙ ። የጥፋቸውንም ፡

አንቀጽ ፡ ፵፫ ።

ፍትሕ ፡ ከመ ፡ ባህለ ፡ ሕግ ፡ ወእምከመ ፡ ሰማ ዕክሙ ፡ ቃለ ፡ ተጻልአቶሙ ፡ ፍትሑ ፡ ማእከሌ ሆሙ ፡ በጽድቅ ፡ ወበርትዕ ፡ ወኢትፍትሑ ፡ በቃለ ፡ ፩ዱ ፡ ሰድው ፡ ዘእንበለ ፡ ይብጻሕ ፡ በዓለ ፡ ዕዳሁ ፡ እላ ፡ ሶበ ፡ ይትራከቡ ፡ ፪ሆሙ ፡ ተጻላእያን ፡ ፍትሑ ፡ ማእከሌሆሙ ፡ በርትዕ ። ይቤ ፡ እግዚአብሔር ፡ ኅሥዋ ፡ ለጽድቅ ፡ ወፍ ትሑ ፡ ባቲ ፡ ወሶበ ፡ ትነብሩ ፡ ለኰንኖ ፡ እንዘ ፡ ተጻላእያን ፡ ይትኳነኑ ፡ በቅድሜክሙ ፡ ገጸ ፡ በገጽ ፡ ኢትስምይዎሙ ፡ ኢ፡ነወ ፡ እስከ ፡ ይጓ ብኡ ፡ ዕርቀ ፡ ወሥረዩ ፡ ዕዳሆሙ ፡ በጽድቅ ።

፩ሺ፬፻፷፯ ወናሁ ፡ ንቤ ፡ ከመ ፡ ኢይደሉ ፡ ትፍትሑ ፡ ላዕለ ፡ ፩ዱ ፡ ዘእንበለ ፡ ይብጽሑ ፡ ፪ሆሙ ፡ ኅቡረ ፡ እስመ ፡ አንትሙ ፡ ለእመ ፡ ሰማዕክሙ ፡ ቃለ ፡ ፩ዱ ፡ ወቅስቶ ፡ ዚአሁ ፡ ወፈታሕክሙ ፡ ፍቱነ ፡ እንዘ ፡ ኢሀለወ ፡ ካልኡ ፡ ምስሌክሙ ፡ ከመ ፡ ያውሥእ ፡ በእንተ ፡ ንፍሱ ፡ ትከውኑ ፡ አንትሙ ፡ ድልዋነ ፡ ለኰንኔ ፡ ዘፈታሕክሙ ፡ ቦቱ ፡ ወትከውኑ ፡ በቅድመ ፡ እግዚአብሔር ፡ አኃዜ ፡ ነዮሉ ፡ ሱተፋኒሃ ፡ ለሐሰት ፡ ወመክፈ ልቶ ፡ ዚአሃ ።

፩ሺ፬፻፷፰ መከ ፡ ፳ወ፱ቱ ፡ ኢይደልዎ ፡ ለብእሲ ፡ ከመ፡ ይረሲ ፡ ግብረ ፡ ህየንቴሁ ፡ በእንተ ፡ ተዋቅሶ ፡ ቅስት ፡ በኀበ ፡ ፈታሒ ፡ እስመ ፡ ኢይትዔረይ ፡ በክብር ፡ ምስለ ፡ እግእዚ ፡ ግብር ።

፩ሺ፬፻፷፱ ክፍል ፡ ፩ዱ ፡ ወአእምር ፡ ከመ ፡ እምጽአ ፡ ሰማዕት ፡ ለጥያቄ ፡ ላዕለ ዘይሰኪ ፡ ወመሐላሰ ላዕለ ዘይክሕድ ። ወለእመ ተሣመረ በመ ሐላሁ ፡ ላዕለ ፡ ዘይሰኪ ፡ ዝኒ ፡ ይከውን ፡ ወይትገ ብእ ፡ ዕዳ ፡ ላዕለ ፡ ዘክሕደ ፡ ኪያሁ ፡ እስመ ፡ ሰካዪ ፡ ለሊሁ ፡ ኅሣሢሁ ፡ ውእቱ ፡ ወዘይሰከይ ዎሂ ፡ ለሊሁ ዘይትኑሠሡ እምኔሁ ። ወሰክየ ትሰ ኢይከውን ፡ ዘእንበለ በዘውእቱ ብዉሕ ፡ ላዕለ ፡ አስተዋፅኦቱ ፡ ለዘይሰኪ ፡ በእ ንቲአሁ ፡ በከመ ፡ ብዉሕ ፡ ላዕለ ፡ አስተዋፅ ኦቱ ፡ ውእቱ ፡ ዘይሰክይዎ ፡ ቦቱ ፡ በእንቲአሁ ።

፩ሺ፬፻፸ ወእምከመ በጽሑ ፡ ፪ኤሆሙ ፡ ተጻላእያን ለተፋትሖ ፡ ይብሎሙ ፈታሒ በሉ ተና ገሩ ፡ ወለሊሆሙ ያርምም እስከ ይትናገሩ ። ወለእመ ፡ ሰከዩ ፡ ለለ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ይቅ ድም ዘሰከየ አቅዲሙ ፡ ወእምከመ ፈጸመ ነገረ ቅስቱ ፡ ይስምዑ ቅስቶ ካልኡ ። ወለ እመ ኀሥ ፩ዱ በነገር ለካልኡ ፡ አው

ስለ ፡ ዳኛ ።

ነገር ፡ ከሰማችሁ ፡ በኋላ ፡ በመካከላቸው ፡ በእ ውነትና ፡ በቅን ፡ ፍረዱ ። ባላጋራው ፡ ሳይመጣ በ፩ ፡ ባላጋራ ፡ ቃል ፡ አትፍረዱ ። ሁለቱ ፡ ተከራካሪዎች ፡ በተገናኙ ፡ ጊዜ ፡ በመካከላቸው በቅን ፡ ፍረዱ ፡ እንጂ ። እግዚአብሔር ፡ ጽድቅን (እውነት) ፡ ሺት ፡ በእርሷም ፡ ፍረዱ ፡ ብሏል ። (ኢሳ ፡ ፩ ፡ ፲፯) ። የተጣሉ ፡ ሰዎች ፡ በፊታችሁ ፡ ሲከራከሩ ፡ ለፍርድ ፡ በተቀመጣችሁ ፡ ጊዜ ፡ እስኪታረቁ ፡ ድረስ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ወንድሞች፡ አትበሏቸው ። ዕዳቸውንም ፡ በእውነት ፡ ይቅር በሏቸው ።

፩ሺ፬፻፷፯ እነሆ ፡ ሁለቱም ፡ በአንድነት ፡ ሳይቀርቡ ፡ በአንዱ ፡ ላይ ፡ ልትፈርዱ ፡ እንዳይገባ ፡ ተናገርን ። ሌላው ፡ በስራሱ ፡ መልስ ፡ ይሰጥ ፡ ዘንድ ፡ ከእ ናንተ ፡ ጋር ፡ ሳይኖር ፡ የአንዱን ፡ ቃልና ፡ ክር ክሩን ፡ ሰምታችሁ ፡ ፈጥናችሁ ፡ ብትፈርዱ ፡ በፈረዳችሁበት ፡ ፍርድ ፡ ለመቀጣት ፡ እናንተ ፡ ዝግጁዎች ፡ ትሆናላችሁና ። ሁሉን ፡ በያዘ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የሐሰት ፡ ተባባሪዎችና፡ የእርሷ ፡ ዕድል ፡ ፈንታ ፡ ትሆናላችሁ ።

፩ሺ፬፻፷፰ መክ ፡ ፳፱ ። ለሰው ፡ በዳኛ ፡ ዘንድ ፡ ስለጠቡ ክርክር ፡ ባሪያውን ፡ ነገረ ፡ ፈጅ ፡ ሊያደርግ ፡ አይገባውም ። ባሪያ ፡ በክብር ፡ ከጌታው ፡ ጋር ፡ አይተካከልምና ።

፩ሺ፬፻፷፱ ክፍል ፡ ፩ ። የማስረጃ ፡ ምስክር ፡ ማምጣት ፡ ለከሳሽ ፡ እንደሆነ ፡ እወቅ ። መሐላ ፡ ግን ፡ ለሚ ክድ ፡ ነው ፡ በከሳሽ ፡ ላይ ፡ በመሐላው ፡ ቢስ ማሙ ፡ ይህም ፡ ይሆናል ። ዕዳም ፡ እርሱን ፡ ወደ፡ ካደ ፡ ይመለሳል ። ከሳሽ ፡ እርሱ ፡ ራሱ ፡ ፈላ ጊው ፡ ነውና ፡ ተከሳሽ ፡ ግን ፡ ከእርሱ ፡ የሚፈ ለግበት ፡ ነውና ። ስለእርሱ ፡ የከሰሱትም ፡ ሰው፡ በማውጣጣቱ ፡ ላይ ፡ እንደሚገባው ፡ ክስ ፡ ስለ ፡ እርሱ ፡ የተከሰሰበትን ፡ ለማውጣጣት ፡ ሥልጣን ፡ ባለው ፡ ላይ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ አይ ሆንም ።

፩ሺ፬፻፸ ሁለቱ ፡ ተከራካሪዎች ፡ ለመፋረድ ፡ ከቀረቡ ፡ ዳኛው ፡ በሉ ፡ ተናገሩ ፡ ይበላቸው ። እርሱም ፡ እስኪናገሩ ፡ ድረስ ፡ ዝም ፡ ይበል ። ከእነርሱም ፡ እያንዳንዱ ፡ ቢካሰስ ፡ አስቀድሞ ፡ የከሰሰው ፡ ይቅደም ። (ከሳሽ) ፡ የጠቡን ፡ ነገር ፡ ከፈጸመ ፡ በኋላ ፡ የሌላውን ፡ (የተካሳሹን) ፡ ክርክር ፡ ይስሙ ። አንዱ ፡ ሌላውን ፡ በነገር ፡ ቢነካው ፡

አንቀጽ ፡ ፶፫ ።

እሙዕአ ፡ ቃለ ፡ ሕሡመ ፡ ይክልአ ፡ ወለእመ ፡ ደገመ ፡ ይገሥጽ ፡ ወእመኒ ፡ ወሰከ ፡ ያውግዞ ።

፩ሺ.፩፻፸፩ ወዘሂ ፡ ሰከየ ፡ ግብረ ፡ ዘኢይትለበው ፡ ይበሎ ፡ አጠይቅ ፡ ነገረከ ፡ ዘሰከይከ ፡ በእንቲአሁ ። ወኢይፍታሕ ፡ በዘሰከየ ፡ እስከ ፡ ያዜክር ፡ ንዋየ ፡ ዘእሙር ፡ ክዋኔሁ ፡ ለንባብ ፡ ዘኢይትዌለጥ ፡ ከመ ፡ ዘይብል ፡ እነ ፡ ወሀብክዎ ፡ ፱ ፡ ዲናራተ ፡ ዘምስር ፡ ወበእንተ ፡ ዘኮነ ፡ ዲናራት ፡ ዘምስር ፡ ክዋኔሁ ፡ ውእቱ ፡ ዝንቱ ፡ ወበእንተ ፡ ዘኮነት ፡ ኍላቌሃ ፡ ፱ ፡ ውእቱ ፡ ወለእመኒ ፡ ሰከየ ፡ ሰክዮተ ፡ ዘጥዩቅ ፡ ወዘይትለበው ፡ ይበሎ ፡ ለካልኡ ፡ ምንተ ፡ ትብል ፡ ወለእመኒ ፡ አምነ ፡ ወእምዝ ፡ ይበሎ ፡ ለሰካዪ ፡ ናሁ ፡ ተአምነ ፡ ለከ ፡ ወለእመ ፡ ነሥአ ፡ ንዋዮ ፡ ይፍታሕ ፡ ሎቱ ፡ በእንቲአሁ ፡ ላዕለ ፡ በዓለ ፡ ለዱ ። ወእመኒ ፡ ክሕዶ ፡ ለዘሰከየ ፡ ኪያሁ ፡ ይበሎ ፡ ለዘክሕደ ፡ ብከኑ ፡ ሰምዕ ፡ ወለእመ ፡ ይቤ ፡ አልቦ ፡ ይበሎ ፡ ለካዪ ፡ ትምሕሎኑ ፡ ወእመኒ ፡ ፈርሀ ፡ መሐላ ፡ ወአግብአ ፡ ለዘሰከየ ፡ ወእመኒ ፡ መሐለ ፡ ዘሰከየ ፡ ደለዎ ፡ ነሢአ ፡ ንዋዩ ። ወእመሰ ፡ ይቤ ፡ ካልኡ ፡ እምድኅረ ፡ ፈርሀ ፡ መሐላ ፡ እነ ፡ እምሕል ፡ ኢይሰምዖ ፡ እምኔሁ ፡ ዘእንበለ ፡ በሥምረት ፡ ካልኡ ፡ አው ፡ ገብአ ፡ ውስተ ፡ ካልእ ፡ ዓውደ ፡ ምኵናን ፡ ወኢአበየ ፡ ተመይጦ ፡ እመሐላ ፡ ኢይትከላእ ።

፩ሺ.፩፻፸፪ ወዘኒ ፡ ይቤ ፡ ብየ ፡ ጥዩቅ ፡ ሰማዕት ፡ ክሡታነ ፡ ወኀሠሠ ፡ መሐላ ፡ ዕድው ፡ እምበዓለ ፡ ለዱሁ ፡ እምቅድመ ፡ ያብጽሖ ፡ ኪያሁ ፡ ኢያምሕሎ ፡ ሎቱ ፡ ወለእመ ፡ ይቤ ፡ ሰካዪ ፡ ብየ ፡ ጥዩቅ ፡ ሰማዕት ፡ ወለእመ ፡ ይቤ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ እምድኅረ ፡ አበየ ፡ ይሰምዕዎ ። ወለእመ ፡ ኮኑ ፡ ሰማዕታቲሁ ፡ ኢአክልያነ ፡ ይትኃሠሥዎ ፡ ከመ ፡ ይወስክ ፡ ለአጠይቆ ። ወለእመ ፡ ኮኑ ፡ ራትዓነ ፡ ወፍርሃት ፡ ውስቴቶሙ ፡ ይደልዎ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ይፍልጥ ፡ ማእከሌሆሙ ፡ ወይሕትቶሙ ፡ ለለ፩ዱ ፡ ለለሉ ፡ በእንተ ፡ ከዊነ ፡ ስምዕ ፡ ወጥዩቃቲሃ ፡ ወመከና ፡ በከመ ፡ ገብረ ፡ ዳንኤል ፡ በጊዜ ፡ ረበናት ፡ እለ ፡ ኮኑ ፡ ሰምዐ ፡ ላዕለ ፡ ሶስና ። ወለእመ ፡ ኀብሩ ፡ ይትሌሥጽዎሙ ፡ በባሕቲቶሙ ፡ በአፍርሆ ፡ ወበተግሣጽ ፡ እምግብራት ፡ ኀሳፍያት ፡ ወኢኀሳፍያት ፡ ወሰለተ ፡ ዕድሜ ፡ ወአዘክሮ ፡ በዘኮነ ፡ ተዳሎ ፡ እምተግሣጽ ፡ እምላካዊ ፡ ላዕለ ፡ እለ ፡ ኮኑ ፡ ሰምዐ ፡ በሐሰት ፡ ወእምነ ፡ እማርያት ፡ መንፈሳውያት ፡ እስመ ፡ ገቢአ ፡ ኀበ ፡ ርትዕ ፡ ይኄ

ስለ ፡ ዳኛ ።

ወይም ፡ ከፉ ፡ ቃል ፡ ቢናገር ፡ ይከላከለው ። ቢደግምም ፡ ይቅጣው ። ቢጨምርም ፡ ይለየው ።

፩ሺ.፩፻፸፩ በማይታወቅ ፡ ሥራ ፡ የከሰሰውንም ፡ ስለእርሱ ፡ የከሰሰበትን ፡ ነገር ፡ አስረዳ ፡ ይበለው ። የታወቀ ፡ የገንዘቡን ፡ አኳኋን ፡ በማይለወጥ ፡ አነጋገር ፡ እስኪያስረዳ ፡ ድረስ ፡ በከሳሽ ፡ አይፍረድበት ። እኔ ፡ አምሳ ፡ የምስር ፡ ዲናር ፡ ሰጠሁት ፡ እንደሚል ፡ ነው ። የምስር ፡ ዲናር ፡ ሁኔታዋ ፡ ይህ ፡ ስለሆነ ፡ ቍጥሯም ፡ ፶ ፡ ስለሆነ ፡ ነው ። የታወቀ ፡ የተረዳ ፡ ክስ ፡ ቢከስ ፡ ግን ፡ ተከሳሽን ፡ ምን ፡ ትላለህ ? ይበለው ። ቢያምን ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ከሳሽን ፡ እነሆ ፡ አምኖልሃል ፡ ይበለው ። ገንዘቡን ፡ ቢፈልግ ፡ ስለርሱ ፡ በባለ ፡ ዕዳው ፡ ላይ ፡ ይፍረድለት ። የከሰሰውን ፡ ቢክደው ፡ የካደውን ፡ ምስክር ፡ አለህን ? ይበለው ። የለኝም ፡ ቢል ፡ ከሳሽ ፡ ትምላለህን ? ይበለው ። መሐላውን ፡ ፈርቶ ፡ ለከሳሽ ፡ ቢመልስ ፡ (አንተ ፡ ማል ፡ ቢለው) ፡ ከሳሽም ፡ ቢምል ፡ ገንዘቡን ፡ መቀበል ፡ ተገባው ። ተከሳሽ ፡ መሐላውን ፡ ከፈራ ፡ በኋላ ፡ እኔ ፡ እምላለሁ ፡ ቢል ፡ በከሳሽ ፡ ፈቃድ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ አይስሙት ። ወይም ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ የፍርድ ፡ ሸንጎ ፡ ቢመለስ ፡ (ይግባኝ ፡ ቢል) ፡ ከመሐላም ፡ መመለስን ፡ እንቢ ፡ ባይል ፡ አይከልከል ።

፩ሺ.፩፻፸፪ የታወቀ ፡ የምስክር ፡ ማስረጃ ፡ አለኝ ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ ባላጋራው ፡ ከባለዕዳው ፡ መሐላን ፡ ቢፈልግ ፡ እርሱን ፡ ሳያቀርብ ፡ አያምሉለት ። ከሳሽ ፡ የምስክር ፡ ማስረጃ ፡ አለኝ ፡ ቢል ፡ ከእነርሱም ፡ አንዱ ፡ እንቢ ፡ ካለ ፡ በኋላ ፡ አለብኝ ፡ ቢል ፡ ይስሙት ። ምስክሮቹ ፡ የማይበቁ ፡ ቢሆኑ ፡ ለማረጋገጥ ፡ እንዲጨምር ፡ ይጠይቁት ። ቅኖች ፡ ቢሆኑ ፡ ፍርሃትም ፡ ቢኖራቸው ፡ በመካከላቸው ፡ ለይቶ ፡ እያንዳንዳቸውን ፡ ስለሚመሰክሩበት ፡ ሁኔታ ፡ ስለማስረጃውና ፡ ስለቦታዋ ፡ ሊመረምራቸው ፡ ይገባዋል ። ዳንኤል ፡ በሶስና ፡ ላይ ፡ ምስክር ፡ በሆኑ ፡ በሁለቱ ፡ ረበናት ፡ እንዳደረገ ። ቢተባበሩ ፡ ካለፉትና ፡ ካላለፉት ፡ ሥራዎች ፡ ከሰለተ ፡ ሞትም ፡ የተነሣ ፡ በማስፈራራትና ፡ በማስገረም ፡ ከዚህ ፡ አስቀድሞ ፡ በሐሰት ፡ ምስክር ፡ በሆኑ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ ከአምላካዊ ፡ ቅጣትና ፡ ከመንፈሳውያት ፡ ምልክቶች ፡ የተነሣ ፡ በማሳሰብ ፡ ይቅጣቸው ። ከንቱ ፡ ነገርን ፡ በመሥራት ፡ ከመደፋፈር ፡ ወደ ፡ ቅንነት ፡

ይስ ፡ እምተኃብሎ ፡ ላዕለ ፡ ገቢረ ፡ ክንቱ ፡ እስመ ፡ እምገቢረ ፡ ክንቱ ፡ ንስሓ ፡ እምእሁ ። ወአዝልፎሰ ፡ ላዕለ ፡ ገቢረ ፡ ክንቱ ፡ ወሰኮ ፡ ኃጢአት ፡ በዲበ ፡ ኃጢአት ።

፩ሺ፬፻፸፫ ወእመ ፡ ጸንዑ ፡ እምድኅረ ፡ ዝንቱ ፡ ላዕለ ፡ ስምዐ ፡ ከዊን ፡ ወፍርሀት ፡ ሀሎ ፡ ውስቴቶሙ ፡ ይደልዎ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ይበሎ ፡ ለዘሰከዮ ፡ ንዋ ፡ ኮኑ ፡ ስምዐ ፡ ላዕሌከ ፡ እገሌ ፡ ወእገሌ ፡ ወተወከፍከ ፡ ስምዖሙ ፡ ወነዋ ፡ አባሕኩከ ፡ እምተናቅፎ ፡ ሰማዕት ፡ ከመ ፡ ይፍታሕ ፡ ማእከሌሆሙ ፡ በአጠይቆ ፡ ሰማዕት ። ወሰእመ ፡ ተንፍቀ ፡ ሰማዕታት ፡ በጥያቄ ፡ እመኒ ፡ ኮሎሙ ፡ አው ፡ ተርፈ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ትብጥል ፡ ሰማዕት ፡ ቀዳሚት ፡ እንተ ፡ አምጽአት ፡ ዕዳ ፡ በዘሰከዮ ፡ ቦቱ ፡ ወናሁ ፡ ተፈልጠ ፡ ፩ዱ ፡ እምእለ ፡ ይከውኑ ፡ ስምዐ ።

፩ሺ፬፻፸፬ ክፍል ፡ ፪ቱ ፡ ወእመኒ ፡ አርመመ ፡ ዘሰከዮ ፡ ወኢአምነ ፡ ወኢክሕደ ፡ ይበሎ ፡ ፈታሒ ፡ ዳግመ ፡ በኑኃሁ ፡ ተሠጥዎ ፡ አውሥእ ፡ ወእመ ፡ አበሰ ፡ ይደልወከ ፡ ቃለ ፡ መሐላ ፡ አው ፡ ተሐባዪ ፡ ሀብ ፡ በዘሰከዩከ ። ወሰእመ ፡ ይቤ ፡ ዘሰከዮ ፡ ብየ ፡ ሰማዕት ፡ ከመ ፡ አልቦቱ ፡ ምንትኒ ፡ እምነቢየ ፡ በዘይሰከየኒ ፡ የሀብዎ ፡ መዋዕለ ፡ ዕድሜ ፡ ለአብጽሖቶ ፡ ጥያቄሁ ፡ ወሰከዩኒ ፡ ይነድግ ፡ እስከ ፡ ያመጽእ ፡ ሰማዕተ ። ወለእመ ፡ ተድኅረ ፡ እምነ ፡ ዕድሜ ፡ ዘይደሉ ፡ ለአብጽሖተ ፡ ጥያቄሁ ፡ ይደልዎ ፡ እመሂ ፡ መሐላ ፡ አው ፡ አሚን ። ወለእመኒ ፡ ኮነ ፡ ብዙኀ ፡ ነገር ፡ ማእከሌሆሙ ፡ ለሰማዕት ፡ ይፈትሕ ፡ በዘምዕ ፡ እምኔሆሙ ። ወለእመ ፡ ኢነበበ ፡ ቃለ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ይፈትሑ ፡ በሀልዎቶሙ ፡ በከመ ፡ ይፈትሑ ፡ በኢሀልዎቶሙ ። ወቃልኒ ፡ ቃሉ ፡ ለዘሀሎ ፡ ንዋይ ፡ ውስተ ፡ እዴሁ ፡ ምስለ ፡ መሐላሁ ፡ ለእመ ፡ ኢያምጽአ ፡ ሰማዕተ ፡ ላዕለ ፡ ካልኡ ፡ በእንተ ፡ ወሊዶቱ ።

፩ሺ፬፻፸፭ ወዘእሰተዋደየ ፡ ወዘተበይወ ፡ ላዕለ ፡ ብእሲት ፡ እንተ ፡ ኢለመደት ፡ ተፋትሖ ፡ ወኢሐዊረ ፡ ፍኖት ፡ ኀበ ፡ ተማይጦ ፡ ወተፋኖዶ ፡ ኢየገብርዋ ፡ ለበጺሕ ፡ አላ ፡ ተአዝዝ ፡ ከመ ፡ ትሚም ፡ ላቲ ፡ ዘየንቲሃ ፡ ዘይቀውም ፡ በምትክማ ። ወእምከመ ፡ ይበጽሕ ፡ ላዕሌሃ ፡ መሐላ ፡ ይፈኑ ፡ ኀቤሃ ፡ ዘያምሕላ ፡ ፩ደ ፡ እምፈታሕያን ።

፩ሺ፬፻፸፮ ወይደልዎ ፡ ለፈታሒ ፡ ከመ ፡ ይጽሕፍ ፡



መመለስ ፡ ይሻላልና ። ከንቱ ፡ ነገርን ፡ ከመሥራት ፡ መመለስ ፡ ንስሐ ፡ ነውና ። ከንቱ ፡ ነገርን ፡ በመሥራት ፡ ማዘውተር ፡ ግን ፡ በኃጢአት ፡ ላይ ፡ ኃጢአት ፡ መጨመር ፡ ነው ።

፩ሺ፬፻፸፫ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ምስክር ፡ በመሆን ፡ ቢጸኑ ፡ ፍርሃትም ፡ ቢኖራቸው ፡ የከሰሱትን ፡ ሰው ፡ እገሌና ፡ እገሌ ፡ እነሆ ፡ ምስክር ፡ ሆነውብሃል ። ምስክርነታቸውንም ፡ ተቀብለሃል ። ምስክርነታቸውንም ፡ ስመንቀፍ ፡ ፈቅጄልሀ ፡ ነበር ፡ ብሎ ፡ በምስክሮች ፡ አስረጅነት ፡ በመካከላቸው ፡ ይፈርድ ፡ ዘንድ ፡ ይገባዋል ። ምስክሮችም ፡ በማስረዳት ፡ ጊዜ ፡ ቢለያዩ ፡ ሁሉም ፡ ወይም ፡ ከእነርሱ ፡ አንዱ ፡ ቢቀር ፡ በተከሳሹ ፡ ላይ ፡ ዕዳ ፡ ያመጣችበት ፡ የቀደመችቱ ፡ ምስክርነት ፡ ትፈርሳለች ። ምስክር ፡ ከሆኑት ፡ ሰዎች ፡ አንዱ ፡ እነሆ ፡ ተለይቷልና ።

፩ሺ፬፻፸፬ ክፍል ፡ ፪ ። የተከሰሰው ፡ ዝም ፡ ቢል ፡ ባያምን ፡ ወይም ፡ ባይክድ ፡ ዳግመኛም ፡ ዳኛው ፡ መልስ ፡ በመሻት ፡ መልስ ፡ ስጥ ፡ ያም ፡ ባይሆን ፡ የመሐላ ፡ ቃል ፡ ይገባሃል ፡ ወይም ፡ በከሰሱህ ፡ ነገር ፡ ዋስ ፡ ስጥ ፡ ይበለው ። የከሰሱት ፡ ሰው ፡ በከሰሰኝ ፡ ነገር ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ ምንም ፡ እንደሌለው ፡ ምስክር ፡ አለኝ ፡ ቢል ፡ መረጃውን ፡ ለማትረብ ፡ የቀጠሮ ፡ ቀን ፡ ይስጡት ። ከሳሹም ፡ ምስክሮቹን ፡ እስኪያመጣ ፡ ይተወው ። መረጃውን ፡ ለማቅረብ ፡ ከሚገባው ፡ ቀጠሮ ፡ ወደኋላ ፡ ቢል ፡ መሐላ ፡ ወይም ፡ ማመን ፡ ቢሆን ፡ ይገባዋል ። በምስክሮች ፡ መካከል ፡ የነገር ፡ ብዛት ፡ ቢሆን ፡ ከእነርሱ ፡ ላቸነፈው ፡ (ለበዛው) ፡ ይፍረዱ ። ከእነርሱ ፡ ያንዱ ፡ ቃል ፡ ባይበልጥ ፡ ባለመኖራቸው ፡ እንደሚፈርዱ ፡ በመኖራቸው ፡ ይፍረዱ ። ስለ ፡ መካዱም ፡ በተከሳሹ ፡ ላይ ፡ ምስክር ፡ ካላመጣ ፡ ነገሩ ፡ ከመሐላው ፡ ጋራ ፡ በእጁ ፡ ገንዘብ ፡ ያለበት ፡ ሰው ፡ ነገር ፡ ነው ።

፩ሺ፬፻፸፭ መፋረድን ፡ ወደገበያ ፡ መንገድ ፡ መሄድን ፡ መንገድን ፡ ያለመደችውን ፡ ሴት ፡ ደፍሮ ፡ የከሰሰ ፡ ሰው ፡ ከዳኛ ፡ ድረሽ ፡ ብለው ፡ አያስገድዷት ። በመቋሚያዋ ፡ የሚተካ ፡ ነገረ ፡ ፈጅ ፡ ትሾም ፡ ዘንድ ፡ ትዘዝ ፡ እንጂ ፡ ለእርሷ ፡ መሐላ ፡ ከተገባትም ፡ የሚያምላት ፡ ከዳኞች ፡ ወገን ፡ እንዱን ፡ ወደ ፡ እርሷ ፡ ይላክ ።

፩ሺ፬፻፸፮ ለዳኛ ፡ በጽ ፡ ወይም ፡ በማበባ ፡ ምስክር ፡

አንቀጽ ፡ ፺፫ ።

ለተፋትሖ ፡ መጽሐፈ ፡ ዕውቀ ፡ ወፍሉጠ ፡ ኀበ ፡ ካልእ ፡ ፈታሒ ፡ እንዘ ፡ ይከውን ፡ በውስቴቱ ፡ ስምዐ ፡ ላዕለ ፡ ነፍሱ ፡ በስምዐ ፡ ፪ቱ ፡ እው ፡ ዘይፈያፍድ ፡ ወስውእቱ ፡ ፈታሒ ፡ ካልእ ፡ ያይ ልዎ ፡ ከመ ፡ ይነጽር ፡ ውስተ ፡ ጠይቆተ ፡ ፍትሑ ፡ ወእምዝ ፡ ይፍታሕ ፡ በቱ ፡ ሰበ ፡ ተወ ከፈ ፡ ስምዖሙ ፡ ለሰማዕታት ፡ ዘውስቴቱ ። ወፍጻሜ ፡ ምዕራፍ ፡ ሳብዕ ፡ በእንተ ፡ ፍትሐት ፡ ናሁ ፡ ይነግር ፡ በበእንቀጸ ፡ ፍትሑ ፡ ዘከመ ፡ ኵልታት ፡ ወከዊነ ፡ ግዕዛን ፡ ወአንብሮ ፡ ማኅ ፀንት ፡ ወትውህስታት ፡ ወሤጥ ፡ ወተዓስቦ ፡ ወተዋርሶ ፡ ወጽሒፈ ፡ ትእዛዝ ፡ ወዘይመስሉ ፡ ለዝንቱ ።

ስለ ፡ ዳኛ ።

ራሱ ፡ በውስጡ ፡ ምስክር ፡ ሁኖ ፡ ለመፈራረድ፡ የታወቀና ፡ የተለየ ፡ መዝገብ ፡ ወደሌላ ፡ ዳኛ ፡ ሊጽፍ ፡ ይገባዋል ። ለዚያም ፡ ለሌላው ፡ ዳኛ ፡ የፍርዱን ፡ እርግጠኛነት ፡ ሊመለከት ፡ ይገባ ዋል ፡ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ በውስጡ ፡ ያሉትን ፡ የምስ ክሮችን ፡ ምስክርነት ፡ በተቀበለ ፡ ጊዜ ፡ (ከተቀ በለ ፡ በኋላ) ፡ ይፍረድበት ። የሰባተኛው ፡ ምዕራፍ ፡ መጨረሻ ፡ ስለፍርዶች ፡ እነሆ ፡ በየፍ ርዱ ፡ እንቀጽ ፡ ይናገራል ። ይኸውም ፡ እንደ ፡ ጉልቶች ፡ እንደ ፡ ነጻነት ፡ ሁኔታ ፡ እንደ ፡ እደራ ማስቀመጥ ፡ እንደ ፡ ትውስቶችና ፡ እንደዋጋ ፡ እንደኪራይና ፡ እንደውርስ ፡ ትእዛዝን ፡ እንደ መጻፍና ፡ ይህንም ፡ እንደሚመስለው ፡ ያለ ፡ ነው ።

፩ሺ.፬፻፸፯ ምዕራፍ ፡ ሳምን ፡ በእንተ ፡ ገቢረ ፡ ዕርቅ ። ገቢረ ፡ ዕርቅሰ ፡ እዙዝ ፡ ውእቱ ፡ በእንተ ፡ ዘይቤ ፡ እግዚእነ ፡ በወንጌል ፡ "ሑር ፡ ቅድመ ፡ ወተዐረቅ ፡ ምስለ ፡ እኁከ ፡ ወእምዝ ፡ ገቢእከ ፡ አብእ ፡ መባእከ ። ወብፁዓንሰ ፡ ከዕበ ፡ ብፁ ዓን ፡ ገብርያነ ፡ ሰላም ፡ እስመ ፡ እሙንቱ ፡ ውሉ ደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይሰመዩ ። ወሐዋርያትኒ ፡ ይቤሉ ፡ ኢመፍትው ፡ ለአግብርተ ፡ ክርስ ቶስ ፡ ተጻልኦ ።

፩ሺ.፬፻፸፯ ስምንተኛ ፡ ምዕራፍ ፡ ዕርቅ ፡ ስለማድረግ ፡ ይናገራል ። ዕርቅ ፡ ማድረግስ ፡ የታዘዘ ፡ ነው ። ጌታችን ፡ በወንጌል ፡ አስቀድመህ ፡ ሂድና ፡ ከወንድምህ ፡ ጋር ፡ ታረቅ ። ከዚያም ፡ ተመል ስህ ፡ መባህን ፡ ስጥ ፡ ብሏል ፡ ነው ። (ማቴ ፡ ፭ ፡ ፳፫ - ፳፬) ። ዳግመኛም ፡ ዕርቅን ፡ የሚያደርጉ ፡ ሰዎች ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ፡ እነርሱ ፡ የእግዚአብ ሔር ፡ ልጆች ፡ ይባላሉና ፡ በማለቱ ፡ ነው ። (ማቴ ፡ ፭ ፡ ፱) ። ሐዋርያትም ፡ ለክርስቶስ ፡ እገ ልጋዮች ፡ መጣላት ፡ አይገባቸውም ፡ ብለዋል ።

፩ሺ.፬፻፸፰ ዘኤፌሶን ፡ ፫ቱ ፡ ወይኩን ፡ ዘይፀውሮ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔክሙ ፡ ለካልኡ ፡ ወኩኑ ፡ ዕቁባነ ፡ በዐ ቂበ ፡ ፍቅር ፡ መንፈሳዊት ፡ በማእሰረ ፡ ዕርቅ ። ዘ፬ቱ ፡ ወኢታዕርቡ ፡ ፀሐየ ፡ ዲበ ፡ መዓትክሙ፡ ወኢታህብዎ ፡ ፍኖተ ፡ ለሰይጣን ፡ ለእስሕቶት ክሙ ።

፩ሺ.፬፻፸፰ ኤፌሶን ፡ ፫ ። ከእናንተ ፡ አንዱ ፡ ሌላውን ፡ የሚሸከመው ፡ ይሁን ። በዕርቅ ፡ ማሠሪያነት ፡ መንፈሳዊት ፡ ፍቅርን ፡ በመጠበቅ ፡ የተጠበቃ ችሁ ፡ ሁኑ ። (ኤፌ ፡ ፬ ፡ ፩ - ፫) ። ፬ ። በቁጣችሁ ላይ ፡ ፀሐይን ፡ አታስገቡ ። ለይጣንም ፡ እንዲያ ስታችሁ ፡ ጐዳና ፡ አትስጡት ። (ኤፌ ፡ ፬ ፡ ፳፮ - ፳፯) ።

፩ሺ.፬፻፸፱ ድስቅ ፡ ፳ቱ ፡ ወተዐቀቡ ፡ ከመ ፡ ትግበሩ ፡ ሰላመ ፡ ማእከለ ፡ ተጻላእያን ፡ እምቅድመ ፡ ይፃእ ፡ ፍትሕ ፡ እምኤጲስቆጶስ ፡ ወተፋትሖሰ ፡ ኢኮነ ፡ ሠናየ ፡ በምንትኒ ፡ ግሙራ ፡ እመፍቅ ዳተ ፡ ዝንቱ ፡ ዓለም ፡ እስመ ፡ እመንድቦተ ፡ ፩ዱ ፡ ለካልኡ ፡ በምንትኒ ፡ እመፍቅዳተ ፡ ዝንቱ ፡ ዓለም ፡ እምግብረ ፡ ሰይጣን ፡ ውእቱ ፡ ወእመክራሁ ። ወያፍጥን ፡ ሰብእ ፡ ወይሥዐር ፡ ዘንተ ፡ በጕጕዓ ፡ ወለእመኒ ፡ ውእቱ ፡ የኀጕል፡ ኅዳጠ ፡ እምንዋይ ፡ ይኄይሰከ ፡ ከመ ፡ ትኅ ጕል ፡ ኅዳጠ ፡ እምንዋይከ ፡ ወትጌጕእ ፡ ለተ

፩ሺ.፬፻፸፱ ድስቅ ፡ ፳ ። ከኤጲስቆጶስ ፡ ፍርድ ፡ ሳይወጣ፡ በተጣሉ ፡ ሰዎች ፡ መካከል ፡ ዕርቅ ፡ ከማድረግ፡ ተጠበቁ ። ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ፈቃድ ፡ የተነሣ ፡ በማ ንኛውም ፡ ነገር ፡ መካሰስ ፡ ከቶ ፡ መልካም ፡ አይደለም ። ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ፈቃድ ፡ የተነሣ ፡ በማንኛውም ፡ ነገር ፡ አንዱ ፡ ሌላውን ፡ ማስጨ ነቅ ፡ ከሰይጣን ፡ ሥራ ፡ ከፈተናው ፡ የተገኘ ፡ ነውና ። ሰው ፡ ፈጥኖ ፡ በችኮላ ፡ ይህን ፡ ይሻር ። እርሱ ፡ ከገንዘቡ ፡ ጥቂት ፡ ቢያጠፋ ፡ አንተም ፡ ከገንዘብህ ፡ ጥቂት ፡ ብታጠፋ ፡ ከሰውም ፡ ሁሉ፡ ጋር ፡ ወንድሜ ፡ ወንድሜ ፡ ለመባባል ፡ ብትቻ

አንቀጽ ፡ ፹፫ ።

አንምተ ፡ ኵሉ ፡ ሰብእ ፡ እኮ ፡ ለአኃዊከ ፡ ባሕቲቶሙ ፡ እላ ፡ ምስለ ፡ ኵሎሙ ፡ አሕዛብ ፡ እስመ ፡ አንተ ፡ ለእመ ፡ ነኮልከ ፡ ዘዝንቱ ፡ ዓለም ፡ እኮ ፡ ዘተነኮል ፡ እም ፡ ዘእግዚአብሔር እምከመ ፡ ኮንከ ፡ ላእከ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘተሐዩ ፡ በትእዛዘ ፡ ክርስቶስ ። ለእለ ፡ ተበእሱ ፡ አስተጋብእዎሙ ፡ በተፋቅሮ ፡ ወለመስተጻርራን ፡ አስተሳልምዎሙ ፡ ከመ ፡ ይኩኑ ፡ ሰንአዋን ፡ እስመ ፡ እግዚእን ፡ ይቤ ፡ ብፁዓን ፡ ገባርያን ፡ ሰላም ፡ እስመ ፡ እሙንቱ ፡ ውሉደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይሰመዩ ።

፩ሺ፩፻፹ ዘ፲ወ፪ቱ ፡ ወእለሰ ፡ ይገብሩ ፡ ጽልአ ፡ ወጸብአ ፡ ወተጋእዞ ፡ ወተፋትሖ ፡ ዐማፅያን ፡ እሙንቱ ፡ ወነኪራን ፡ እምእግዚአብሔር ፡ እስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላከ ፡ ምሕረት ፡ ውእቱ ።

፩ሺ፩፻፹፩ ዘቆሮንቶስ ፡ ፮ቱ ፡ "ናሁ ፡ እኩንንከሙ ፡ ሥጋከሙ ፡ ቅድመ ፡ እመ ፡ ኮንከሙ ፡ ተጻላእያን ፡ ወትትገአዙ ፡ በበይናቲከሙ ፡ ወለምንት ፡ ዘኢትትዔገሉ ፡ ወለምንት ፡ ዘኢትትገፍዑ ፡ እላ ፡ አንትሙሰ ፡ ተዓጋልያን ፡ ወገፋዕያን ፡ አኃዊከሙ ፡ ካዕበ ፡ ኢተአምሩኑ ፡ ከመ ፡ ዐማፅያን ፡ ኢይወርስዋ ፡ ለመንግሥተ ፡ እግዚአብሔር" ።

፩ሺ፩፻፹፪ ወእእምር ፡ ከመ ፡ ዕርቅ ፡ ዘበእንተ ፡ ንዋይ ፡ በፍኖተ ፡ እርዮት ፡ ወውሂቦት ፡ ሰቢዝም ፡ መሐላ ፡ ወመተረ ፡ ተጻልኦ ፡ ወተፋትሖ ፡ በእንተ ፡ ፈቃደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወነፈር ፡ እም ሰብእ ። ወውእቱ ፡ ይትከፈል ፡ ኀበ ፫ቱ ፡ እከፋል ፡ ተዓርቆ ፡ ዘምስለ ፡ ተአምኖ ፡ ወዕርቅ ፡ ዘምስለ ፡ ክሒድ ፡ ወዕርቅ ፡ ዘምስለ ፡ አርምሞ ፡ ወውእቱ ፡ ሶበ ፡ ኢየአምን ፡ በዘይስእልዎ ፡ ላዕሌሁ ፡ ወኢይክሕድሂ ።

፩ሺ፩፻፹፫ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ዕርቅ ፡ በእንተ ፡ ንዋይ ፡ በውሂበ ፡ ንዋይ ፡ ይትፌጸም ፡ በእንቲአሁ ፡ ውሂበ ፡ ንዋይ ፡ በእንተ ፡ ንዋይ ። ወይኩን ፡ ዘከመ ፡ ይገብሩ ፡ በምሥያጥ ፡ ወተማይጦ ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ዕርቅ ፡ በእንተ ፡ ንዋይ ፡ ዘቦቱ ፡ በቀኑዓት ፡ ይኩን ፡ በከመ ፡ ተዐሰበ ፡ ወኵሉ ፡ ድልው ፡ ውእቱ ፡ ለእመ ፡ ኢኮነ ፡ ውስቴቱ ፡ ርደ ፡ በአምሳል ፡ ለእመ ፡ ይከውን ፡ ዕርቅ ፡ በእንተ ፡ ፳ ፡ ርኩብት ፡ በጊዜሃ ፡ ወ፲ ፡ በዕድሜ ፡ እው ፡ በመስፈርት ፡ እው ፡ በእንተ ፡ ሥርናይ ፡ ብሉይ ፡

ስለ ፡ ዳኞ ።

ኩል ፡ ይሻልሃል ። ለወንድሞችህ ፡ ብቻ ፡ አይደለም ። ከአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ጋራ ፡ ነው ፡ እንጂ ። በክርስቶስ ፡ ትእዛዝ ፡ የምትኖር ፡ የእግዚአብሔር ፡ አገልጋይ ፡ ከሆንክ ፡ የዚህን ፡ ዓለም ፡ ገንዘብ ፡ ብታጣ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ የሚገኘውን ፡ የምታጣ ፡ አይደለህምና ። የተጣሉትን ፡ ሰዎች ፡ በፍቅር ፡ አንድ ፡ አድርጋቸው ። የተጣሉትንም ፡ አስታርቃቸው ። የተስማሙ ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ። ጌታችን ፡ ሰላምን ፡ የሚያደርጉ ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ። እነርሱ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ ይባላሉና ፡ ብሏልና ። (ማቴ ፡ ፭ ፡ ፱) ።

፩ሺ፩፻፹ ፲፪ ። ጠብን ፡ መጣላትን ፡ ክርክርንና ፡ መፋረድን ፡ የሚያደርጉ ፡ ሰዎች ፡ ዓመፀኞች ፡ ናቸው ። ከእግዚአብሔርም ፡ የተለዩ ፡ ናቸው ። እግዚአብሔር ፡ የይቅርታ ፡ አምላክ ፡ ነውና ።

፩ሺ፩፻፹፩ ቆሮንቶስ ፡ ፮ ። እነሆ ፡ እርስበርሳችሁ ፡ የምትጣሉና ፡ የምትከራከሩ ፡ በነበራችሁበት ፡ ጊዜ ፡ ሥጋችሁን ፡ አስገዝታችሁ ፡ ነበረ ። የማትቀሙ ፡ ለምንድን ፡ ነው ? የማትበደሉስ ፡ ለምንድን ፡ ነው ? እናንተስ ፡ ገና ፡ ሁለተኛ ፡ ወንድሞቻችሁን ፡ የምትቀሙ ፡ የምትበድሉም ፡ ናችሁ ። ዓመፀኞች ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ እንዳይወርሱ ፡ አታውቁምን ? (፩ ፡ ቆሮ ፡ ፮ ፡ ፯ - ፲፩) ።

፩ሺ፩፻፹፪ ስለታወቀ ፡ ገንዘብ ፡ የሚሆን ፡ ዕርቅ ፡ በማስተካከል ፡ መንገድ ፡ መሐላን ፡ ለመበገርት ፡ (ለማስቀረት) ፡ ስለእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ ከሰው ፡ ስለማፈር ፡ መፋረድንና ፡ መጣላትን ፡ ለመቁረጥ ፡ እንደሆነ ፡ እወቅ ። እርሱም ፡ ከ፫ ፡ ይከፈላል ። ከማንም ፡ ጋራ ፡ የሚሆን ፡ ዕርቅ ፡ ከመካድም ፡ ጋር ፡ የሚሆን ፡ ዕርቅ ፡ ከዝምታም ጋር ፡ የሚሆን ፡ ዕርቅ ፡ አለ ። ይኸውም ፡ በከሰሱት ፡ ነገር ፡ ባያምን ፡ ወይም ፡ ባይክድ ፡ ነው ።

፩ሺ፩፻፹፫ ስለገንዘብ ፡ የሚሆን ፡ ዕርቅ ፡ ገንዘብ ፡ በመስጠት ፡ ቢሆን ፡ ስለእርሱ ፡ የገንዘብ ፡ ስጦታ ፡ ስለገንዘብ ፡ ይፈጸማል ። በመሸጥና ፡ በመግዛት ፡ ጊዜ ፡ እንደሚያደርጉት ፡ ይሁን ። ዕርቁ ፡ ትርፍ ፡ ስላለው ፡ ገንዘብ ፡ ቢሆን ፡ እንደተዋዋሉት ፡ ይሁን ። አራጣ ፡ ከሌለበት ፡ ሁሉ ፡ የተገባ ፡ ነው ። ለምሳሌ ፡ ዕርቁ ፡ በጊዜዋ ፡ በተገኘች ፡ በኻያ ፡ በቀጠሮ ፡ ፲ ፡ ወይም ፡ በመስፈሪያ ፡ ወይም ፡ ስለከረመ ፡ ስንዴና ፡ አዲስ ፡ ስንዴ ፡ በቀጠሮ ፡ ስለመስጠት ፡ ቢሆን ፡ በእ

አንቀጽ ፡ ፵፬ ።

ክሙ ፡ በሙብልዕኒ ፡ ወበመስቴ ፡ ወበዘርኡ ፡ ሥርዓተ ፡ ሕግ ፡ በከመ ፡ ዳንኤል ፡ ወ፫ቱ ፡ ደቂቅ ፡ ከመ ፡ ያድኅንክሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ እምእናብስት ፡ ወእምእሳት ። ወይሰባሕ ፡ ስሙ በእንተ ፡ ሥነ ፡ ተእዝዞትክሙ ፡ ወያግብእክሙ ኀበ ፡ ሀገርክሙ ፡ ከመ ፡ እለ ፡ ዘከርናሆሙ ።

ስለ ፡ ብሉይና ፡ ሐዲስ ።

ዓትም ፡ ሁሉ ፡ ጠብቁት ። እንደ ፡ ዳንኤልና ፡ እንደ ፡ ፫ ፡ ደቂቅ ፡ (እንደ ፡ ሦስቱ ፡ ልጆች) ፡ ከአናብስትና ፡ ከእሳት ፡ ያድናችሁ ፡ ዘንድ ። (ዳን ፡ ፫ ፡ ፳፬ - ፳፯። ፮ ፡ ፲፱-፳፬) ። ስለመታዘዛችሁም ፡ መበጀት ፡ ስሙ ፡ ይመሰገን ፡ ዘንድ ፡ እንደ ፡ ጠቀስናቸው ፡ ሰዎች ፡ ወደ ሀገራችሁ ፡ ይመልሳችሁ ፡ ዘንድ ።

---

## አንቀጽ ፡ ፵ወ፭ቱ ፡

በእንተ ፡ ዘይደሉ ፡ ተናግሮቱ ፡ በዝንቱ ፡ መጽሐፍ ፡ እምብሉይ ፡ ወሐዲስ ፡ ካልእ ፡ እምዘተነግረ ፡ ውስተ ፡ አንቀጽ ፡ በበገጹ ።

፩ሺ፰፻፹፫ ወሰበ ፡ ኮነ ፡ ብእሲ ፡ ፍጡረ ፡ በነፍስ ፡ ወሥጋ ፡ ይለው ፡ ከመ ፡ ይሥርዑ ፡ ሎቱ ፡ ፪ቱ ፡ ሕገጋተ ። ቀዳማዊ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ለአፈጽሞተ ፡ ምግባራቲሁ ፡ እለ ፡ በከሠት ፡ እንተ ፡ ህለወት ፡ በእባላቲሁ ፡ ዘእፍአ ። ወካልእኒ ፡ ሕግ ፡ ለአፈጽሞተ ፡ ምግባራቲሁ ፡ ዘውስጥ ፡ እንተ ፡ ህለዋ ፡ በሕሊናሁ ፡ ወኀይላቲሁ ፡ ወርከበ ፡ ታቲሁ ፡ ዘውስጥ ።

፩ሺ፰፻፹፬ ወቀዳማዊ ፡ ሕግ ፡ ይቀውም ፡ በሥርዓተ ፡ ሕግ ፡ ቀዳማዊ ፡ ዘውእቱ ፡ ሕገ ፡ ርትዕ ፡ ይትዐወቅ ፡ አሪት ፡ ወተሠርዐ ፡ በውስቴቱ ፡ ዘኮንኦ ያት ፡ ሥጋውያት ፡ ዘያስተርእዩ ፡ በእንተ ፡ ምግባራት ፡ ሥጋውያት ፡ ዘበሙ ፡ ይደሉ ፡ ፍትሕ ፡ በኀበ ፡ ፈታሕት ፡ ዘከመ ፡ ቀቲለ ፡ ቀታሊ ፡ ወተፈድዮ ፡ ዕዳ ፡ እምነ ፡ ሰራቂ ፡ ወዘቢጠ ፡ ዐማፂ ፡ ወዘተነግረ ፡ በእንቲአሁ ፡ ካልእ ፡ እምዝንቱ ። ወኵሉ ፡ ዘተነግረ ፡ በውስቴቱ ፡ ከመ ፡ ያብጽሕ ኀበ ፡ ዝንቱ ፡ ወከመ ፡ ይበጽሕ ፡ ቦቱ ፡ በምግባር ፡ መንፈሳዊ ፡ ከመ ፡ ሙሴ ፡ ወኤልያስ ፡ ትሩፋነ ፡ ምግባር ።

፩ሺ፰፻፹፭ ወዳግማዊሰ ፡ መንፈሳዊ ፡ ውእቱ ፡ ቀዊም ፡ በሕግ ፡ ደኃራዊ ፡ ወውእቱ ፡ ሕገ ፡ ፍጹሜ ፡ ወተሠርዐ ፡ በውስቴቱ ፡ ሕግ ፡ ልቡናዊ ፡ በእንተ ፡ ምግባራት ፡ ዘውስጥ ፡ ዘይትኀሠሥ ፡ ቦቱ ፡ ነፍስ ፡ ሰብእ ፡ በውስቴቱ ፡ ነፍሱ ፡ ማእከሌሁ ፡ ወማእከለ ፡ ፈጣሪሁ ፡ በሥምረተ ፡ ርእሱ ፡ ዘከመ ፡ ተከልአ ፡ እመዓት ፡ ወእምነጽሮ ፡ በፍትወት ፡ ወእፍቅሮተ ፡ ወርቅ ፡ ወሠርዮ ፡ ለዘእበሰ ፡ ወተሀ

## አንቀጽ ፡ ፵፭ ።

በአንቀጽ ፡ ውስጥ ፡ በየወገኑ ፡ ከተነገረው ፡ ሌላ ከብሉይና ፡ ከሐዲስ ፡ መጥቶ ፡ በዚህ ፡ መጽሐፍ ሊናገሩት ፡ ስለሚገባው ፡ ይናገራል ።

፩ሺ፰፻፹፫ ሰው ፡ ከነፍስና ፡ ከሥጋ ፡ የተፈጠረ ፡ እንደ ፡ መሆኑ ፡ ሁለት ፡ ሕጎች ፡ ሊሠሩለት ተገባ ። መጀመሪያው ፡ በሕዋሳተ ፡ እፍአ ፡ ያለች ፡ በግልጽ ፡ የሚሠሩ ፡ ሥራዎችን ፡ ለማስፈጸም ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ነው ። ሁለተኛውም ፡ ሕግ ፡ በሐሳቡና ፡ በኀይሉ ፡ በውስጥም ፡ በሚያገኙት ፡ ነገሮች ፡ ያሉትን ፡ የውስጥ ፡ ሥራዎችን ፡ ለማስፈጸም ፡ ነው ።

፩ሺ፰፻፹፬ መጀመሪያው ፡ ሕግ ፡ በመጀመሪያው ፡ ሕግ ፡ ሥርዓት ፡ ይጸናል ። ይኸውም ፡ የቀና ፡ ሕግ ፡ ነው ። ኦሪት ፡ እንደሆነች ፡ ይታወቃል ። ስለ ፡ ሥጋውያት ፡ ሥራዎች ፡ የሚገልጹ ፡ ሥጋውያት ፡ ቅጣቶችም ፡ በውስጡ ፡ ተሠሩ ። በዳኞች ፡ ዘንድ ፡ ፍርድ ፡ የሚገባቸው ። ይኸውም ፡ ነፍስ ገዳዩን ፡ እንደመግደል ፡ ከሌባም ፡ ገንዘብን ፡ እንደመክፈል ፡ ዓመፀኛንም ፡ እንደመግረፍ ፡ ያለ ፡ ነው ። ከዚህም ፡ ሌላ ፡ ስለእርሱ ፡ የተነገረው ፡ ነው ። በውስጡ ፡ የተነገረው ፡ ሁሉ ፡ ወደዚህ ፡ ያደርስ ፡ ዘንድ ፡ ነው ። በሥራ ፡ ፍጹማን ፡ እንደሆኑ ፡ እንደ ፡ ሙሴና ፡ እንደ ፡ ኤልያስ ፡ በመንፈሳዊ ፡ ሥራም ፡ ስሙዳን ፡ ይሆኑ ፡ ዘንድ ፡ ነው ።

፩ሺ፰፻፹፭ ሁለተኛው ፡ ግን ፡ መንፈሳዊ ፡ ነው ። በኋለኛው ፡ ሕግ ፡ መጽናት ፡ ነው ። እርሱም ፡ የመጨረሻ ፡ ሕግ ፡ ነው ። ሰው ፡ በራሱ ፡ ፈቃድ ፡ በእርሱና ፡ በፈጣሪው ፡ መካከል ፡ ራሱን ፡ በራሱ ፡ ስለሚገሥጽባቸው ፡ ውስጣውያን ፡ ሥራዎች ፡ ልቡናዊ ፡ ሕግ ፡ በውስጡ ፡ ተጽፏል ። ይኸውም ፡ ከቁጣና ፡ በፍትወት ፡ ከማየት ፡ እንደመከልከል ፡ ጠላትን ፡ እንደመው

ቅቡ ፡ እምጽጋብ ፡ ወስካር ፡ ወእትሕቶ ፡ ርእስ ፡ ለኵሉ ፡ ሰብእ ፡ ወዘተ ፡ ይእቲ ፡ እምዘትነኢዮት ፡ እንተ ፡ ባቲ ፡ ይፈትሕ ፡ ሰብእ ፡ ላዕለ ፡ ነፍሱ ፡ በሥምረተ ፡ ልቡ ፡ ዘይፈቅድ ፡ ይኩን ፡ ብእሴ ፡ ፍጹመ ፡ ወኢኮንት ፡ ይእቲ ፡ እምዘትነኢዮት ፡ እንተ ፡ ይፈትሖ ፡ ባቲ ፡ መኳንንት ፡ ላዕለ ፡ ሰብእ ፡ በግብር ።

፩ሺ፭፻፺፯ ወኢተሠርዐ ፡ በደኃራዊ ፡ ሕግ ፡ አብጥሎቱ ፡ ለዘተነግረ ፡ በሕግ ፡ ቀዳማዊ ፡ እስመ ፡ ይቤ ፡ እግዚእነ ፡ "ኢመጻእኩ ፡ ከመ ፡ እሥዐሮ ፡ ለሕግ ፡ አላ ፡ ከመ ፡ እፈጽሞ ።" ወይእዜኒ ፡ እን ክለ ፡ ኢተሐገነ ፡ እሰርዖቶ ፡ ፍትሖሙ ፡ ለፈታ ሕት ። ወበእንተዝ ፡ ተጽሕፈ ፡ ውስተ ፡ ዓሥር ፡ ምዕራፍ ፡ ዘድስቅ ፡ ፍጡን ፡ ሥረዩ ፡ ኃጣ ውአ ፡ አኃዊክሙ ፡ እኮ ፡ ዘንብል ፡ ዘንተ ፡ ለፈታሕት ። ወሰምዐ ፡ ኮነ ፡ በውስተ ፡ ዝንቱ ፡ መጽሐፍ ፡ ወካልኣኒ ፡ ላዕለ ፡ ብዙኅ ፡ እምፍት ሐታት ፡ በዘነበረ ፡ እምኔሃ ፡ ውስተ ፡ አሪት ፡ ወለእመ ፡ ተደርሰ ፡ ይለወ ፡ ከመ ፡ ይንበር ፡ ውስተ ፡ ዝንቱ ፡ መጽሐፍ ፡ በኵሉ ፡ ዘነበረ ፡ ውስተ ፡ ዘቀዳሚ ፡ ሕግ ፡ እምግብር ፡ ለፈታ ሕት ፡ በእንተ ፡ ፈቲሕ ፡ ዘቦቱ ፡ ይፈትሑ ፡ ላዕለ ፡ ሰብእ ፡ በእንተ ፡ ምግባራት ፡ ግሁዳት ። ወበኵሉ ፡ ዘተነግረ ፡ በሕግ ፡ ደኃራዊ ፡ እምነ ፡ ገሥጸተ ፡ ብእሲ ፡ በሕሊናሁ ፡ በኵሉ ፡ ክብር ፡ ዘሎ ፡ በእንቀጸ ፡ ዚአሁ ።

፩ሺ፭፻፺፰ ወናሁ ፡ ተነግረ ፡ በዝንቱ ፡ እንቀጽ ፡ እምነ ፡ ውእቱ ፡ ቃላት ፡ ፍሉጣት ፡ ካልእ ፡ እምዘ ፡ ተነ ግረ ፡ በእናቅጽ ። ለቀዳማዊሰ ፡ እምቅድመ ፡ ተናግሮቱ ፡ ንበል ፡ ከመ ፡ ሕግ ፡ ቀዳማዊ ፡ ሶበ መጽአ ፡ ሕግ ፡ ደኃራዊ ፡ ኢጸንዐ ፡ ሕግ ፡ ቀዳ ማዊ ፡ በኵለንታሁ ፡ ወኢበጠለ ፡ ኵለንታሁ ፡ አላ ፡ ኀበ ፡ ፪ቱ ፡ ክፍል ፡ ተከፍለ ። ፩ዱሰ ፡ ክፍል ፡ ተርፈ ፡ ኀበ ፡ ሀላዌሁ ፡ እስመ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ፡ ኵነኔ ፡ ፍትሑ ፡ ሀልው ፡ ዘኢይትማሰል ፡ ምስለ ፡ ካልኣኒሁ ፡ እምግባራተ ፡ ትሩፋት ፡ ዘውእቱ ፡ እምልኮ ፡ ፈጣሪ ፡ ዘእንበለ ፡ ፍጡ ራን ፡ ወተከልአ ፡ እምቀቲል ፡ ወዝሙት ። ወ፩ ዱኒ ፡ ክፍል ፡ ተፀርዐ ፡ በምልኡ ፡ እስመ ፡ ግብረ ፡ ቀዊም ፡ ቦቱ ፡ ተፀርዐ ፡ በምልኡ ፡ ወዘ ይትፈቀድ ፡ እምኔሁ ፡ ኮነ ፡ ዘከመ ፡ ሕርመተ ፡ ሐራውያ ፡ እስመ ፡ መፍትድ ፡ እምኔሁ ፡ ውስተ

ደድ ፡ የበደለን ፡ ይቅር ፡ እንደማለት ፡ ከጥጋ ብና ፡ ከስካር ፡ እንደመጠበቅ ፡ ራስንም ፡ ለሰው ሁሉ ፡ ዝቅ ፡ ዝቅ ፡ እንደማድረግ ፡ ያለ ፡ ነው ። ይችውም ፡ ከቅጣቶች ፡ ወገን ፡ ፍጹም ፡ ሰው ፡ ሊሆን ፡ የወደደ ፡ ሰው ፡ በራሱ ፡ ፈቃድ ፡ በሰው ነቱ ፡ ላይ ፡ ሰው ፡ የሚፈርድባት ፡ ናት ። መኳ ንንት ፡ በግድ ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ ከሚፈርዷቸው ፡ ቅጣቶች ፡ ወገን ፡ አይደለችም ።

፩ሺ፭፻፺፯ በፊተኛው ፡ ሕግ ፡ የተነገረውን ፡ ማፍረስ ፡ በኋለኛው ፡ ሕግ ፡ አልተጻፈም ። ጌታችን ፡ ሕግን ፡ ልፈጽመው ፡ እንጂ ፡ ልሽረው ፡ አል መጣሁም ፡ ብሏልና ። (ማቴ ፡ ፭ ፡ ፲፯) ። እን ግዲያውስ ፡ ዛሬም ፡ የዳኞችን ፡ ፍርድ ፡ መሻር ፡ አልታዘዘም ። ስለዚህ ፡ በድስቅ ፡ በ፲ኛው ፡ ምዕራፍ ፡ ተጽፏል ። የወንድሞቻችሁን ፡ በደል ፡ ፈጥናችሁ ፡ ይቅር ፡ በሉ ። ይህንም ፡ ለዳኞች ፡ የምንናገር ፡ አይደለንም ። በዚህም ፡ ውስጥ ፡ መጽሐፍ ፡ ምስክር ፡ ሆነ ። ሌላውም ፡ ከርሱዋ ፡ ወጥቶ ፡ በኦሪት ፡ በተጻፈው ፡ ከፍ ርድ ፡ ወገን ፡ በብዙ ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ተገለጹ ፡ ሥራዎችም ፡ ዳኞች ፡ ከሥራ ፡ ወገን ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ ስለሚፈርዱበት ፡ ፍርድ ፡ በቀደመው ፡ ሕግ ፡ በተጻፈው ፡ ሁሉ ፡ ድርሰት ፡ ቢደረስ ፡ ከዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ ጋራ ፡ ሊቀመጥ ፡ ተገባ ። በሥ ራው ፡ ሁሉ ፡ በሐሳቡ ፡ ሰውን ፡ ከመገሠጽ ፡ የተ ነግ ፡ በኋለኛው ፡ ሕግ ፡ የተጻፈው ፡ ሁሉ ፡ በእር ሱው ፡ አንቀጽ ፡ አለ ።

፩ሺ፭፻፺፰ በየአንቀጹ ፡ ከተነገረው ፡ ሌላ ፡ ልዩ ፡ ከሆኑ ፡ ቃላት ፡ መጥቶ ፡ እነሆ ፡ በዚህ ፡ አንቀጽ ፡ ተነ ገረ ። የመጀመሪያውን ፡ ሕግ ፡ ከመናገሩ ፡ አስ ቀድሞ ፡ እንደ ፡ መጀመሪያው ፡ ሕግ ፡ ኋለኛው፡ ሕግ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ የፊተኛው ፡ ሕግ ፡ በ፪ ፡ ክፍል ፡ ተከፈለ ፡ እንጂ ፡ መላውም ፡ አልተሻ ረም ። መላውም ፡ አልጸናም ፡ እንበል ። አንደ ኛው ፡ ክፍል ፡ በሰበት ፡ ጸና ። ከትሩፋት ፡ ሥራ ዎች ፡ ወገን ፡ ከሌሎች ፡ ጋራ ፡ የማይመሳሰል ፡ የፍርዱ ፡ ቅጣት ፡ ሁልጊዜ ፡ ይኖራልና ። ይኸ ውም ፡ ከፍጡራን ፡ ለይቶ ፡ ፈጣሪን ፡ ማምለክ፡ ከመግደልና ፡ ከመስሰንም ፡ መከልከል ፡ ነው ። ፩ኛውም ፡ ክፍል ፡ በሙሉ ፡ ተሻረ ። በእርሱ ፡ ጸንቶ ፡ መኖር ፡ በሙሉ ፡ ተሸሯልና ። ከእርሱ ፡ የሚሻውም ፡ ከዕሪያ ፡ እንደመከልከል ፡ ያለ ፡ ነበር ። በቀደመው ፡ ሕግ ፡ ከእርሱ ፡ የሚሻው ፡

እንቀጽ ፡ ፺፩ ።

ሕግ ፡ ቀዳማዊ ፡ ኮነ ፡ ከመ ፡ ኢይደመሩ ፡ ሕዝበ ፡ እግዚአብሔር ፡ ምስለ ፡ አሕዛብ ፡ እለ ፡ ኢያመልክዎ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ዘበንቤሆሙ ፡ ሀሎ ፡ ብዙኅ ፡ አሕርው ፡ ከመ ፡ ኢይትመየጡ ፡ ኀበ ፡ አምልኮቶሙ ፡ ወልማዳቲሆሙ ፡ እኪት ።

፩ሺ፭፻፳፰ ወሶበ ፡ ሰፈነ ፡ እሚን ፡ ላዕለ ፡ ኵሉ ፡ አሕዛብ ፡ ወኢተርፉ ፡ ዘእንበለ ፡ ኅዳጣን ፡ ዐላውያን ፡ በፈቃድ ፡ እምላካዊ ፡ ደለወ ፡ ፈቂድ ፡ ኀበ ፡ ተጋብአቶሙ ፡ ለመሃይምናን ፡ ወደለወ ፡ እፀርአቲ ፡ ለዘይክልእ ፡ ወለዘይክልእዎሂ ። ወ፩ዱ ፡ ክፍል ፡ ኮነ ፡ ፍጹመ ፡ በተወስኮ ፡ ላዕሌሁ ፡ ዘከመ ፡ ገቢረ ፡ ሠናይ ፡ ለፍቁር ፡ ወለጸላእት ፡ ካዕበ ፡ ወሕጹጽስ ፡ ዘኮነ ፡ ሕጹጸ ፡ አምፍጻሜ ፡ ኮነ ፡ ፍጹመ ፡ ዘከመ ፡ ገቢረ ፡ ሠናይ ፡ በዕለተ ፡ ሰንበታት ፡ ዘተአዘዘ ፡ ቀዳሚ ፡ ኀዲገ ፡ ኵሉ ፡ ግብር ፡ ውስቴቶን ። ወ፩ዱ ፡ ክፍል ፡ ኮነ ፡ ሥጋዌ ፡ ወፈለሰ ፡ ኀበ ፡ ግብር ፡ መንፈሳዊ ፡ ወኮነ ፡ ህየንተ ፡ አንጽሖ ፡ ሥጋ ፡ በማያት ፡ ወደማት ፡ አንጽሖ ፡ ነፍስ ፡ በንስሐ ፡ ወሥርዓታቲሃ ። ወህየንተ ፡ ተስፋ ፡ መንግሥተ ፡ ምድር ፡ ወሠናያቲሃ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ወዘለዓለም ፡ ተድላሃ ።

፩ሺ፭፻፳፱ ወይእዜኒ ፡ ኢይትፈቀዳ ፡ በዝንቱ ፡ መጽሐፍ ፡ ኵሎን ፡ ትእዛዛት ፡ እለ ፡ ቀደማ ። ወዘይትፈቀድስ ፡ እምብሔረ ፡ እሪት ፡ ዳግማዊ ፡ ዘይቤ ፡ ቃሉ ፡ ለልዑል ፡ ሎቱ ፡ ስብሐት ፡ አነ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክከ ፡ ኢትግበር ፡ ለከ ፡ አምላከ ፡ ዘእንበሌየ ። ወኢትግበር ፡ ለከ ፡ ግልፈዋተ ፡ ወኢእምሳላተ ፡ ዘውስተ ፡ ሰማይ ፡ ዘላዕሉ ፡ ወኢዘውስተ ፡ ምድር ፡ ዘታሕቱ ፡ ወኢትስግድ ፡ ሎሙ ፡ ወኢታምልኮሙ ። እስመ ፡ አነ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክከ ። "ኢትምሐል በስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፈጣሪከ ፡ በሐሰት ፡ እስመ ፡ ኢያነጽሖ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለዘይምሕል ፡ ስሞ ፡ በሐሰት ። "ወአክብር ፡ አባከ ፡ ወእመከ ፡ ከመ ፡ ትርከብ ፡ ሠናየ ፡ ወይኑኅ ፡ መዋዕሊከ ። "ኢትቅትል ፡ ወኢትዘሙ ፡ ኢትስርቅ ፡ ወኢትኩን ፡ ስምዐ ፡ በሐሰት ፡ ላዕለ ፡ ቢጽከ ። ወኢትፍቱ ፡ ቤተ ፡ ካልእከ ፡ ኢ ፡ ብእሲቶ ፡ ወኢገብሮ ፡ ወኢ ፡ እመቶ ፡ ወኢ ፡ እንስሳሁ ፡ ወኢ ፡ ኵሎ ፡ ዘአጥረየ ፡ ቢጽከ ።

ስለ ፡ ብሉይና ፡ ሐዲስ ።

የእግዚአብሔር ፡ ወገኖች ፡ እግዚአብሔርን ፡ ከማያመልኩት ፡ በአነርሱ ፡ ዘንድ ፡ ብዙ ፡ ስራይ ፡ ካላቸው ፡ ከአሕዛብ ፡ ጋራ ፡ እንዳይቀርቡ ፡ ነበርና ። ወደአምልኮታቸውና ፡ ወደክፉ ፡ ልማዳቸው ፡ እንዳይመለሱ ።

፩ሺ፭፻፳፰ ሃይማኖት ፡ በአሕዛብ ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ በሰፈነ ፡ ጊዜ ፡ ከጥቂቶችም ፡ ዐላውያን ፡ በቀር ፡ በአልቀሩ ፡ ጊዜ ፡ በእምላካዊ ፡ ፈቃድ ፡ ምእመናንን ፡ ወደመሰብሰብ ፡ መሻት ፡ ተገባ ። የሚከለክለውንና ፡ የሚከለክሉትን ፡ ነገርም ፡ መሻር ፡ ተገባ ። አንደኛውም ፡ ክፍል ፡ ተጨምሮበት ፡ ፍጹም ፡ ሆነ ። ለወዳጅ ፡ ዳግመኛም ፡ ለጠላት ፡ በጎ ፡ እንደመሥራት ፡ ያለው ፡ ነው ። ከፍጹምነት ፡ ሕፀፅ ፡ የነበረውም ፡ ፍጹም ፡ ሆነ ። ይኸውም ፡ ቀድሞ ፡ ሥራን ፡ ሁሉ ፡ መተው ፡ በታዘዘባቸው ፡ ሰንበታት ፡ ቀን ፡ በጎ ፡ እንደመሥራት ፡ ያለ ፡ ነው ። አንዱ ፡ ክፍል ፡ ሥጋዊ ፡ ነበረ ። ወደመንፈሳዊም ፡ ሥራ ፡ ተላለፈ ። ሥጋን ፡ በውኃና ፡ በደም ፡ ስለማንጻት ፡ ፈንታ ፡ በንስሐና ፡ በሥርዓቶቿ ፡ ነፍስን ፡ ማንጻት ፡ ሆነ ። የምድር ፡ መንግሥትንና ፡ ተድላ ፡ ደስታዋን ፡ ተስፋ ፡ ስለማድረግ ፡ ፈንታም ፡ መንግሥተ ፡ ሰማይንና ፡ የዘለዓለም ፡ ተድላዋን ፡ ተስፋ ፡ ማድረግ ፡ ሆነ ።

፩ሺ፭፻፳፱ ዛሬም ፡ በዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ የቀደሙት ፡ ትእዛዛት ፡ ሁሉ ፡ አያፈልጉም ። የሚሻውስ ፡ በ፪ኛው ፡ ብሔረ ፡ ኦሪት ፡ ምስጋና ፡ ይግባውና ፡ ልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡ ፈጣሪህ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነኝ ። ከእኔ ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ አምላክ ፡ አታድርግ ። ያለው ፡ ቃል ፡ ነው ። ጣዖቶችንም ፡ ከላይ ፡ በሰማይ ፡ ያሉትን ፡ ከታችም ፡ በምድር ፡ ያሉትን ፡ ምስሌዎች ፡ ለአንተ ፡ አታድርግ ። አትስገድላቸውም ። አታምልካቸውም ። ፈጣሪህ ፡ እኔ ፡ እግዚአብሔር ነኝና ። በፈጣሪህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ስም ፡ በሐሰት ፡ አትማል ። እግዚአብሔር ፡ በሐሰት ፡ በስሙ ፡ የሚምለውን ፡ እያነፃውምና ። መልካም ፡ ነገርንም ፡ ታገኝ ፡ ዘንድ ፡ ዕድሜህም ፡ ይረዝም ፡ ዘንድ ፡ አባትና ፡ እናትህን ፡ አክብር ። አትግደል ፡ አትስስን ፡ አትስረቅ ፡ በባልንጀራህ ፡ ላይ ፡ በሐሰት ምስክር ፡ አትሁን ። የጓደኛህን ፡ ቤቱን ፡ ሚስቱንም ፡ ወንድ ፡ ባሪያውንና ፡ ሴት ፡ ባሪያውን ፡ እንስሳውንም ፡ ባልንጀራህ ፡ የገዛውን ፡ ሁሉ ፡

አንቀጽ ፡ ፵፩ ።

፩ሺ፭፻፹ ወዛቲ ፡ ትእዛዛተ ፡ ፍትሕ ፡ እንተ ፡ ተሠርዐት ፡ ሎሙ ፡ እመበ ፡ ዘአጥረየ ፡ ገብረ ፡ ዕብራዌ ፡ ይትቀነዮ ፡ ፮ተ ፡ ዓመተ ፡ ወበሳብዕት ፡ ዓመት ፡ ያግዕዞ ፡ ወይፃእ ፡ ዘእንበለ ፡ ሤጥ ፡ ወለእመ ፡ ቦእ ፡ ምስለ ፡ ብእሲቱ ፡ ይፃእ ፡ ምስሌሃ ። ወለእመኒ ፡ ወሀቦ ፡ እግዚኡ ፡ ብእሲተ ፡ ወወለደት ፡ ሎቱ ፡ ደቂቀ ፡ ወአዋልደ ፡ ብእሲት ፡ ወውሉዳ ፡ ይትቀነዩ ፡ ለእግዚኦሙ ፡ ውእቱሰ ፡ ይፃእ ፡ ባሕቲቱ ፡ ወለእመ ፡ ይቤ ፡ ገብር ፡ አፍቀርክዎ ፡ እግዚእየ ፡ ወብእሲትየ ፡ ወውሉድየ ፡ ወኢይፈቅድ ፡ ግዕዛነ ፡ ለይኩን ፡ ሎቱ ፡ ገብረ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ። ወለእመኒ ፡ ሤጠ ፡ ወለተ ፡ እመቱ ፡ እንተ ፡ ይእቲ ፡ ወለተ ፡ ገብሩ ፡ ኢትጻእ ፡ እምቤቱ ፡ በከመ ፡ ይጸንዑ ፡ አእማት ፡ ወኢይሚጣ ፡ ለሕዝብ ፡ ነኪር ።

፩ሺ፭፻፹፩ ወለእመ ፡ ተበአሱ ፡ ፪ቱ ፡ ሰብእ ፡ ወዘበጦ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ለካልኡ ፡ አው ፡ ገፍዖ ፡ ወኢሞተ ፡ ወሰከበ ፡ ውስተ ፡ ምስካቡ ፡ ወእምዝ ፡ ተንሥአ ፡ ወአንሶሰወ ፡ ጽጐ ፡ ተመርጕዞ ፡ በትረ ፡ ይድኅን ፡ ዘዘበጦ ፡ አላ ፡ የሀቦ ፡ ህየንተ ፡ ዕርዓቲሁ ፡ ወየሀቦ ፡ ዓስቦ ፡ ለዐቃቤ ፡ ሥራይ ። ወእመ ፡ ዘበጠ ፡ ብእሲ ፡ ዓይነ ፡ ገብሩ ፡ አው ፡ ዓይነ ፡ እመቱ ፡ ወአጥፍአ ፡ ዓይኖ ፡ ያግዕዞ ፡

፩ሺ፭፻፹፪ ወለእመ ፡ ወግአ ፡ ላሕም ፡ ብእሴ ፡ ወቀተሎ ፡ ይገርዎ ፡ ለላሕም ፡ ወኢይብልዑ ፡ ሥጋሁ ፡ ወይድኅን ፡ በዓለ ፡ ላሕም ፡ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ላሕም ፡ ዘይወግእ ፡ እምትማልም ፡ ወእምቅድመ ፡ ትማልም ፡ ወአስምዑ ፡ ላዕለ ፡ እግዚኡ ፡ ወኢዐቀቦ ፡ ላሕሙኒ ፡ ይትወገር ፡ በእብን ፡ ወይቅትልዎ ፡ ካዕበ ፡ ለእግዚኡ ። ወለእመ ፡ ፈትሑ ፡ ላዕሌሁ ፡ ዕዳ ፡ ይፍዲ ፡ ቤዛ ፡ ነፍሱ ፡ ዘኀሠሡ ፡ እምኔሁ ። ወለእመ ፡ ቀተለ ፡ ላሕም ፡ ገብረ ፡ አው ፡ አመተ ፡ የሀቡ ፡ ሤጦ ፡ ለእግዚኡ ፡ ወይውግርዎ ፡ ለላሕም ።

፩ሺ፭፻፹፫ ወእመቦ ፡ ብእሲ ፡ ዘከሠተ ፡ ግበ ፡ አው ፡ ከረየ ፡ ዓዘቅተ ፡ ወኢከደኖ ፡ አፉሁ ፡ ወጸድፈ ፡ ውስቴቱ ፡ ላሕም ፡ ወእመኒ ፡ አድግ ፡ እግዚአ ፡ ዓዘቅት ፡ ይፍዲ ፡ ለእግዚኡ ፡ ወገደላሁኒ ፡ ይንሣእ ፡ ውእቱ ። ወላሕም ፡ ለእመ ፡ ወግአ ፡

ስለ ፡ ብሉይና ፡ ሐዲስ ።

አትመኝ ። (ዘፀ ፡ ፳ ፡ ፫ - ፲፯) ።

፩ሺ፭፻፹ የተሠራችላቸው ፡ የፍርድ ፡ ትእዛዝ ፡ ይህች ፡ ናት ። ዕብራዊ ፡ ባሪያ ፡ የገዛ ፡ ቢኖር ፡ ስድስት ፡ ዓመት ፡ ይግዛው ፡ በ፯ኛውም ፡ ዓመት ፡ ነጻ ፡ ያውጣው ። ያለዋጋም ፡ ይውጣ ። ከሚስቱም ፡ ጋር ፡ ቢገባ ፡ ከእርስዋ ፡ ጋር ፡ ይውጣ ። ጌታው ፡ ሚስት ፡ ቢያጋባውም ፡ ወንድ ፡ ልጅና ፡ ሴቶች ፡ ልጆችም ፡ ብትወልድለት ፡ ሚስቲና ፡ ልጆቿ ፡ ለጌታቸው ፡ ይገዙ ። እርሱ ፡ ግን ፡ ብቻውን ፡ ይውጣ ። ባሪያውም ፡ ጌታዬንና ፡ ሚስቴን ፡ ልጆቼንም ፡ እወድዳለሁ ፡ ነጻነትንም ፡ አልሻም ፡ ቢል ፡ እስከ ፡ ዘለዓለም ፡ ባሪያ ፡ ይሁነው ። የሴት ፡ ባሪያውንም ፡ ልጅ ፡ ቢሸጥ ፡ ይህችም ፡ የወንድ ፡ ባሪያው ፡ ልጅ ፡ ናት ። ሴቶች ፡ ባሮች ፡ ትልወት ፡ ሁነው ፡ እንደሚሰጡ ፡ ከቤቱ ፡ አትውጣ ። ለባዕድ ፡ ወገንም ፡ አይሸጣት ።

፩ሺ፭፻፹፩ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ ቢጣሉና ፡ ከእነርሱ ፡ አንዱ ፡ ሌላውን ፡ ቢመታው ፡ ወይም ፡ ቢገፋው ፡ ባይሞትም ፡ በአልጋውም ፡ ላይ ፡ ቢተኛ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ተነሥቶ ፡ በትር ፡ እየተመረኰዘ ፡ ጥግ ፡ ለጥግ ፡ ቢሄድ ፡ የመታው ፡ ይድናል ። ሥራ ፡ የፈታበትን ፡ ይስጠው ፡ እንጂ ። የወጌሻውንም ፡ ዋጋ ፡ ይስጥ ። ሰው ፡ የወንድ ፡ ባሪያውን ፡ ዓይን ፡ ወይም ፡ የሴት ፡ ባሪያውን ፡ ዓይን ፡ መትቶ ፡ ቢያጠፋ ፡ ስለ ፡ ዓይኑ ፡ ፈንታ ፡ ነጻ ፡ ያውጣው ።

፩ሺ፭፻፹፪ በሬ ፡ ሰው ፡ ወግቶ ፡ ቢገድል ፡ በሬውን ፡ ይውገሩት ። ሥጋውንም ፡ አይብሉት ። ባለበሬውም ፡ ይዳን ። በሬው ፡ ከትናትና ፡ ከትናትናም ፡ በፊት ፡ የሚዋጋ ፡ ቢሆን ፡ በባለቤቱም ፡ ቢያዳኙበት ፡ ባይጠብቀውም ፡ በሬው ፡ በድንጋይ ፡ ይወገር ። ባለቤቱንም ፡ ደግሞ ፡ ይግደሉት ። የነፍስ ፡ ዋጋ ፡ ቢፈርዱበትም ፡ ከእርሱ ፡ የፈለጉትን ፡ የነፍሱን ፡ ዋጋ ፡ ይክፈል ። በሬ ፡ ወንድ ፡ ባሪያ ፡ ወይም ፡ ሴት ፡ ባሪያ ፡ ቢገድል ፡ ዋጋውን ፡ ለጌታው ፡ ይስጡ ፡ በሬውንም ፡ ይውገሩት ።

፩ሺ፭፻፹፫ ጉድጓድ ፡ የከፈተ ፡ ወይም ፡ የውሀ ፡ ጉድጓድ ፡ የቈፈረ ፡ ቢኖር ፡ አፉን ፡ ባይገጥመው ፡ ላም ፡ ወይም ፡ አህያ ፡ በውስጡ ፡ ቢወድቅ ፡ ባለጉድጓዱ ፡ ይክፈል ። የሞተውንም ፡ እርሱ ፡ ይውሰድ ። በሬ ፡ የሌላውን ፡ ሰው ፡ በሬ ፡ ቢወጋ ፡

አንቀጽ ፡ ፵፫ ።

ላሕመ ፡ ካልእ ፡ ብእሲ ፡ ወሞተ ፡ ፩ዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ይሢጥዎ ፡ ለሕያው ፡ ላሕም ፡ ወይትካፈሉ ፡ ሤጦ ፡ ወሤጠ ፡ ምዉት ፡ ካዕበ ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ወጋኤ ፡ ላሕሙ ፡ እምትማልም ፡ ወእምትካት ፡ ወኢዐቀቦ ፡ እግዚእ ፡ ዚአሁ ፡ ይፍዲ ፡ ላሕመ ፡ ተክለ ፡ ላሕም ፡ ወነደላ ፡ ዘሞተ ፡ ውእቱ ፡ ይንሣእ ።

፩ሺ.፭፻፸፬ ወለእመ ፡ ተውሕሰ ፡ ብእሲ ፡ እምቢጹ ፡ እንስሳ ፡ ወተሰብረ ፡ ወሞተ ፡ ወኢሀለወ ፡ እውሐሲ ፡ ምስሌሁ ፡ ለእግዚእ ፡ ንዋይ ፡ ይፍዲ ። ወእመሰ ፡ ሀለወ ፡ እግዚእ ፡ ንዋይ ፡ ምስሌሁ ፡ ኢይፍዲ ፡ ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ዘተዓሰባ ፡ በዓስብ ፡ ወሞተት ፡ ዘእንበለ ፡ ተዓስቦት ።

፩ሺ.፭፻፸፭ ወለእመቦ ፡ ዘአስሐታ ፡ ለድንግል ፡ እንተ ፡ ኢተሐፅየት ፡ ወሰከበ ፡ ምስሌሃ ፡ የሀብ ፡ ሕዬሃ፡ ወትኩኖ ፡ ብእሲተ ። ወለእመ ፡ አበየ ፡ አቡሃ ፡ ከመ ፡ ያስተዋስባ ፡ ሎቱ ፡ የሀባ ፡ ሕዬሃ ፡ በእምጣነ ፡ ሕዬሆን ፡ ለደናግል ።

፩ሺ.፭፻፸፮ ወለመኳንንት ፡ ኢትሕምዮሙ ፡ ወኢትሰርፍ ፡ ላዕለ ፡ መኰንነ ፡ ሕዝብከ ፡ ወኢታስተዶኀር ፡ ቀዳምያተ ፡ ዓውደ ፡ እክልከ ፡ ወምክያዳቲከ ፡ ወበኩረ ፡ ውሉድከ ፡ ወረስዮሙ ፡ ሊተ ። ወከማሁ ፡ ግበር ፡ ሊተ ፡ ላሕመከ ፡ ወበግዐከ ፡ ወእድግከ ፡ ወዘተወልደሂ ፡ እምኔሆሙ ፡ ስቡዐ ፡ መዋዕለ ፡ ይንበር ፡ ምስለ ፡ እሙ ፡ ወእመ ፡ ሳምንት ፡ ዕለት ፡ አምጽኦ ፡ ሊተ ።

፩ሺ.፭፻፸፯ ወለእመ ፡ ረከብከ ፡ ላሕመ ፡ ጸላኢከ ፡ ግዱፈ ፡ እው ፡ አድጎ ፡ አግብእ ፡ ሎቱ ። ወለእመ ፡ ርኢከ ፡ አድግ ፡ ጸላኢከ ፡ ውዱቀ ፡ በታሕተ ፡ ፆሩ ፡ ኢትትዓደዎ ፡ እስከ ፡ ታነሥእ ፡ ምስሌሁ ። ወኢትሳተፍ ፡ በቀቲለ ፡ ጻድቅ ፡ ወንጹሕ ፡ ኢታድኅን ፡ ወሕልያነ ፡ ኢትንሣእ ፡ እስመ ፡ ሕልያን ፡ ያዐውር ፡ አዕይንተ ፡ ወይመይጥ ፡ ነገረ ፡ ርቱዐ ።

፩ሺ.፭፻፸፰ ትጉ ፡ ወለእመቦ ፡ ዘአበሰ ፡ ወስሕተ ፡ በምንትኒ ፡ በቅድሳተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘእንበለ ፡ እእምሮ ፡ ያብእ ፡ ቍርባነ ፡ ህየንተ ፡ ዘአበሰ ፡ ቦቱ ፡ እምቅድሳት ፡ ወያግብእ ፡ በዲቤሁ ፡ ምስሌሁ ፡ ትኅምሥቶ ፡ ወይሰድ ፡ ኀበ ፡ ካህን ፡ ወያስተሥሪ ፡ በእንቲአሁ ፡ በቅድሳት ፡ ዘቍርባን ፡ ወይትኀደግ ፡ ሎቱ ።

ስለ ፡ ብሉይና ፡ ሐዲስ ።

ከእነርሱ ፡ አንዱ ፡ ቢሞት ፡ ያልሞተውን ፡ በሬ ፡ ሸጠው ፡ ዋጋውን ፡ ይካፈሉ ። ዳግመኛም ፡ የሞተውን ፡ በሬ ፡ ዋጋ ። በሬው ፡ ከትናትና ፡ ከጥንት ፡ ጀምሮ ፡ ተዋጊ ፡ ቢሆን ፡ ጌታውም ፡ ባይጠብቀው ፡ በበሬው ፡ ምትክ ፡ በሬ ፡ ይክፈል ። የሞተውን ፡ ሥጋ ፡ እርሱ ፡ ይውሰድ ። (ዘፀ ፡ ፳፩ ፡ ፳፰ - ፴፮) ።

፩ሺ.፭፻፸፬ ሰው ፡ ከጓደኛው ፡ እንስሳ ፡ ቢዋስ ፡ ቢሰበርና ቢሞት ፡ ያዋሰውም ፡ ሰው ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ባይኖር ፡ ለባለገንዘቡ ፡ ይክፈል ። የገንዘቡ ፡ ጌታ ፡ አብሮት ፡ ቢኖር ፡ ግን ፡ አይክፈል ። በኪራይ ፡ የተከራያት ፡ ብትሆንም ፡ ያለኪራይ ፡ ሞተች ።

፩ሺ.፭፻፸፭ ያልታጨችውን ፡ ልጃገረድ ፡ ያሳተና ፡ አብሯት ፡ የተኛ ፡ ቢኖር ፡ ማጫዋን ፡ ሰጥቶ ፡ ሚስት ፡ ትሁነው ። አባቷም ፡ ለእርሱ ፡ ያጋባት ፡ ዘንድ ፡ እንቢ ፡ ቢል ፡ በልጃገረዶች ፡ ማጫ ፡ ልክ ፡ ማጫዋን ፡ ይስጣት ። (ዘፀ ፡ ፳፪ ፡ ፲፬ - ፲፰) ።

፩ሺ.፭፻፸፮ መኳንንትን ፡ አትሟቸው ። የወገንህን ፡ ሹም ፡ አትሳደብ ። የእህልህንና ፡ የወይንህን ፡ ቀዳምያትም ፡ የልጅህንም ፡ በኩር ፡ ወደኋላ ፡ አትበል ። ለእኔም ፡ አድርጋቸው ። እንደዚሁም፡ ላምህንና ፡ በግህን ፡ አህያህንም ፡ ለእኔ ፡ አድርግ ። ከእነርሱም ፡ የተወለደው ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ ከእናቱ ፡ ጋር ፡ ይቆይ ። በስምንተኛውም ፡ ቀን፡ ለእኔ ፡ አምጣልኝ ። (ዘፀ ፡ ፳፪ ፡ ፳፰ - ፴፩) ።

፩ሺ.፭፻፸፯ የጠላትህን ፡ በሬ ፡ ወይም ፡ አህያውን ፡ ጠፍቶ ፡ (ኮብልሎ) ፡ ብታገኘው ፡ መልስለት ። የጠላትህንም ፡ አህያ ፡ ከጭነቱ ፡ በታች ፡ ወድቆ ፡ ብታይ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ አስክታነሣው ፡ ድረስ ፡ አትለፈው ። ጻድቁንም ፡ በመግደል ፡ አትተባበር ። ኃጢአተኛውንም ፡ አታድን ። መማለጃም ፡ አትቀበል ። መማለጃ ፡ ዓይንን ፡ እሳውሮ ፡ ቀናውን ፡ ነገር ፡ ይለውጣልና ። (ዘፀ ፡ ፳፫ ፡ ፬ - ፱) ።

፩ሺ.፭፻፸፰ ትጉ ። ሳያውቅ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቅድሳት፡ በማናቸውም ፡ የበደለና ፡ የሳተ ፡ ቢኖር ፡ ከተቀደሰው ፡ ወገን ፡ ስለበደለበት ፡ ፈንታ ፡ ቍርባን ያቅርብ ። በዓይነቱ ፡ ላይ ፡ ከእርሱ ፡ ጋራ ፡ አምስት ፡ አድርጎ ፡ ያግባ ። ወደካህኑም ፡ ይውሰድ ። ስለእርሱም ፡ ለቍርባን ፡ በተቀደሰው ፡ ነገር ፡ ያስተሥርይለት ፡ ይሠረይለታልም ፡ (ዘሌ ፡ ፭ ፡ ፲፮) ።

እንቀጽ ፡ ፶፰ ።

፩ሺ፰፻፸፱ ወእመቦ ፡ ዘአበሰ ፡ በአሐቲ ፡ ግብር ፡ እምዘ ፡ አሕረመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘኢ.ብውሕት ፡ ለገቢር ፡ ወኢያእመረ ፡ ያብእ ፡ ቍርባነ ። ወለእመ ተንሕለዎ ፡ ፩ዱ ፡ ለቢጹ ፡ በማኅፀንት ፡ አው ፡ በተሰናእዎ ፡ ተማባር ፡ አው ፡ ዘየምስዮ ፡ ለቢጹ ፡ አው ፡ ዘይዔምዮ ፡ አው ፡ ዘረከበ ፡ ግድፍተ ፡ አው ፡ ጕያዪተ ፡ ወክሕደ ፡ ኪያሃ ። ወዘይምሕል ፡ በአሐቲ ፡ እምነ ፡ እሉ ፡ ኵሎሙ ፡ እንተ ፡ ይገብራ ፡ ሰብእ ፡ ወይኤብስ ፡ ባቲ ፡ ወእምከመ፡ አበሰ ፡ ያግብእ ፡ ዘተዓገለ ። ወእመኒ ፡ ዘዐመፀ ፡ አው ፡ ማኅፀንተ ፡ ዘአንበሩ ፡ ኀቤሁ ፡ አው ፡ ግድፍተ ፡ አው ፡ ጕያዪተ ፡ ዘረከበ ፡ አው ፡ ዘመሐለ ፡ ላዕሌሁ ፡ በሐሰት ፡ ያግብእ ፡ ወይወስክ ፡ ላዕሌሁ ፡ ትኅምስቶ ፡ ወየሀቦ ፡ ለዘውእቱ ፡ ሎቱ በዕለተ ፡ ቅስቱ ፡ አው ፡ በዕለተ ፡ ተአመነ ፡ በአበሳሁ ፡ ወያብእ ፡ ቍርባነ ።

፩ሺ፰፻፹ ወእመ ፡ ቦ ፡ ብእሲ ፡ እምደቂቀ ፡ እስራኤል ፡ አው ፡ እምነኪራን ፡ እለ ፡ ይነብሩ ፡ ማእከሌሆሙ ፡ ዘይበልዕ ፡ ምንተኒ ፡ እምደም ፡ አወርድ መዓትየ ፡ ላዕለ ፡ ይእቲ ፡ ነፍስ ፡ እንተ ፡ በልዓት ፡ ደመ ፡ ወእደመስሳ ፡ እምሕዝባ ።

፩ሺ፰፻፹፩ ኢትክሥት ፡ ኀፍረተ ፡ እምከ ፡ ወኢ ፡ ኀፍረተ፡ ብእሲተ ፡ እቡከ ፡ አው ፡ ኀፍረተ ፡ እኅትከ ፡ ወወለተ ፡ ወልድከ ፡ ወወለተ ፡ ወለትከ ፡ ወኀፍረተ ፡ ወለታ ፡ ለብእሲተ ፡ አቡከ ፡ ወእኅተ ፡ አቡከ ። ወእኅታ ፡ ለእምከ ፡ ወብእሲተ ፡ እኅወ ፡ አቡከ ፡ ወብእሲተ ፡ እኁከ ፡ ወብእሲተ ፡ ወልድከ ፡ ወብእሲተ ፡ ወልዳ ። ወከማሁ ፡ ወለተ ፡ ወልዳ ፡ ወወለተ ፡ ወለታ ፡ ወብእሲተኒ፡ ምስለ ፡ እኅታ ፡ እንተ ፡ ሀለወት ፡ በሕይወታ ፡ ወብእሲተኒ ፡ በጊዜ ፡ ተክቶሃ ፡ ወኢትርከቦስ ፡ በብእሲተ ፡ ካልእከ ። ወተብዕትኒ ፡ ኢይስክብ ፡ ምስለ ፡ ተባዕት ፡ ከመ ፡ ሰኪበ ፡ አንስት ፡ ወኢ ይርከብዋ ፡ ብእሲ ፡ ወኢ ፡ ብእሲት ፡ በምንትኒ ፡ እምእንስሳ ።

፩ሺ፰፻፹፪ ወእመ ፡ ተዓጽዱ ፡ እክለ ፡ ማእረርክሙ ፡

ስለ ፡ ብሉይና ፡ ሐዲስ ።

፩ሺ፰፻፸፱ እግዚአብሔር ፡ ከከለከለው ፡ ወገን ፡ ሊሠርዋት ፡ በማይገባ ፡ በአንዲት ፡ ሥራ ፡ የበደለ ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡ ባያውቅም ፡ ቍርባን ፡ ያቅርብ ። ዘሌ ፡ ፭ ፡ ፲፯ - ፲፰) ። አንዱም ፡ ባልጀራውን ፡ አደራ ፡ በማስቀመጥ ፡ ወይም ፡ በሥራ ፡ ስምምነት ፡ ቢክዳው ፡ ወይም ፡ ጓደኛውን ፡ የሚያስቆጣው ፡ ወይም ፡ የሚበድለው ፡ ወይም ፡ የጠፋችውን ፡ ወይም ፡ የኮበለለችውን ፡ አግኝቶ ፡ እርሱዋን ፡ ቢክድ ፡ ሰው ፡ ከሚሠራቸው ፡ ከእነዚሀ ፡ ሁሉ ፡ በአንዲቱ ፡ የማለ ፡ በእርሱዋም ፡ የበደለ ፡ ከበደለም ፡ በኋላ ፡ የቀማውን ፡ ይመልስ ። የሰረቀውንም ፡ ወይም ፡ በእርሱ ፡ ዘንድ ፡ ያስቀመጡበትን ፡ አደራ ፡ ወይም ፡ የጠፋችውን፡ ወይም፡ የኮበለለችውን፡ ያገኘ፡ ወይም፡ በሐሰት ፡ የማለበትን ፡ ነገር ፡ ቢሆን ፡ ይመልስ ። በእርሱም ፡ ላይ ፡ አምስት ፡ እድርጎ ፡ ይጨምር ። ለእርሱም ፡ ለሆነው ፡ (ለባለገንዘቡ) ፡ በተከራከረበት ፡ ወይም ፡ በደሉን ፡ ባመነበት ፡ ቀን ፡ ይስጠው ። ቍርባንም ፡ ያቅርብ ። (ዘሌ ፡ ፮ ፡ ፩ -፯) ።

፩ሺ፰፻፹ ከእስራኤል ፡ ጆልች ፡ ወይም ፡ ከ...ካከላቸው፡ ከሚኖሩ ፡ ልዩ ፡ ወገኖች ፡ ከደም ፡ ወገን ፡ ምንም ፡ ምን ፡ የሚበላ ፡ ቢኖር ፡ ደም ፡ በበላች ፡ ሰውነት ፡ ላይ ፡ መዓቴን ፡ አወርዳለሁ ። ከወገኗም ፡ ለይቼ ፡ እጠፋታለሁ ። ( ዘሌ ፡ ፲፯ ፡ ፲ - ፲፭ ) ።

፩ሺ፰፻፹፩ የእናትህን ፡ ኀፍረት ፡ አትግለጽ ። የአባትህን ፡ ሚስት ፡ ኀፍረትም ፡ የእኅትህንም ፡ ኀፍረት ፡ የወንድ ፡ ልጅህን ፡ ሴት ፡ ልጅም ፡ የሴት፡ ልጅህን ፡ ሴት ፡ ልጅም ፡ የአባትህን ፡ የሚስት፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ኀፍረትም ፡ የአባትህንም ፡ እኅት ፡ የእናትህን ፡ እኅት ፡ የአባትህን ፡ የወንድም ፡ ሚስት ፡ የወንድምህን ፡ ሚስት ፡ የልጅዋንም ፡ ሚስት ፡ እንደዚሁም ፡ የወንድ ፡ ልጅዋን ፡ ሴት ልጅ ፡ የሴት ፡ ልጅዋንም ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ሴትንም ፡ ከልጅዋ ፡ ጋራ ፡ በሕይወት ፡ ሳለች ፡ ሴትንም ፡ በግዳጅዋ ፡ ጊዜ ፡ በጓደኛህም ፡ ሚስት ፡ አትርከስ ። ሴትን ፡ እንደመተኛትም ፡ ወንድ ፡ ከወንድ ፡ ጋራ ፡ አይተኛ ። ወንድ ፡ ወይም ፡ ሴት ፡ ከእንስሳ ፡ ወገን ፡ በማናቸውም ፡ አይርከሱ። (ዘሌ ፡ ፲፰ ፡ ፮ - ፳፫) ።

፩ሺ፰፻፹፪ የአዝመራችሁን ፡ እህል ፡ በምታጭዱበት ፡

አንቀጽ ፡ ፶፫ ።

ኢትጠናቀቁ ፡ ዐጺደ ፡ እንዘ ፡ ተዐጽዱ ፡ ወኢት
እረ ፡ ዘወድቀ ፡ እምኔሁ ፡ ወኢትግባእ ፡ እምድ
ኅረ ፡ ቀሲመ ፡ ዓጸደ ፡ ወይንከ ፡ ወኢትእረ ፡ ዘተ
ርፈ ፡ እላ ፡ ኅድጎ ፡ ለነዳይ ፡ ወለግዩር ።

፩ሺ.፰፻፹፫ ወአነ ፡ እግዚአብሔር ፡ እምላክክሙ ፡ እፈ
ድየክሙ ፡ ሠናየ ፡ ወኢታብእ ፡ ዓስበ ፡ ለዓሳብ፡
በኀቤከ ፡ እስከ ፡ ይጸብሕ ፡ ወኢትንብብ ፡ ሕሡ
መ ፡ ላዕለ ፡ ጽሙም ፡ ወኢትደይ ፡ ዕቅፍተ ፡
ቅድመ ፡ ዕዉር ፡ ወኢትጠየር ፡ በዖፍ ፡ ወኢት
ትፋለሱ ።

፩ሺ.፰፻፹፬ ወኢትግበሩ ፡ ቈናዝዓተ ፡ እምሥዕርተ ፡ ርእ
ስክሙ ፡ ወኢትላጺ ፡ መንፈቀ ፡ ሥዕርተ ፡ ርእ
ስከ ፡ ወኢትላጽዩ ፡ ስፍሐ ፡ ጽሕምክሙ ። ወእ
መበ ፡ ዘሞተ ፡ ኢተሐንፍጡ ፡ ገጸክሙ ፡ ወመ
ላጼ ፡ ኢታቅርቡ ፡ ዲበ ፡ ሥጋክሙ ፡ ወኢትኅ
ትሙ ፡ እባለክሙ ፡ በመርፍዕ ። ወኢታዘምዋ ፡
ለወለትከ ፡ ወኢትሖር ፡ ኀበ ፡ ሰብእ ፡ ሐረስ ፡
ውተአማርያን ፡ ወኢትትልውዎሙ ፡ ለሰብእ ፡
ሥራይ ፡ እስመ ፡ አነ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክ
ክሙ ፡ ዘአእምር ፡ ኅቡአ ።

፩ሺ.፰፻፹፭ ወአክብር ፡ ለዘይልህቅ ፡ እምኔከ ፡ ወኢታ
ሕሥሙ ፡ ላዕለ ፡ ግዩር ፡ ዘየኀድር ፡ ውስተ ፡
ምድርክሙ ፡ ወይኩን ፡ ማእከሌክሙ ፡ ከመ ፡
፩ዱ ፡ እምኔክሙ ። ወኢትግበሩ ፡ ዐመፃ ፡ በው
ስተ ፡ ፍትሕ ፡ ወኢ ፡ በውስተ ፡ ምግኔ ፡ ዘኑ
ልቍ ፡ ወኢ ፡ በመዳልው ፡ ወኢ ፡ በመስፈርት ፡
እላ ፡ መዳልውክኒ ፡ ዘበጽድቅ ፡ ይኩና ፡ ወእእ
ባኒ ፡ መዳልውክኒ ፡ ዘበጽድቅ ፡ ይኩና ፡ ወመስ
ፈርትክኒ ፡ ወኀሞርክኒ ፡ ዘበጽድቅ ፡ ይኩን
ክሙ ፡ እስመ ፡ ራትዕ ፡ አነ ፡ እግዚአብሔር ፡
እምላክክሙ ።

፩ሺ.፰፻፹፮ ወዘይከው ፡ ዘርእ ፡ ውስተ ፡ ብእሲት ፡ ንክ
ርት ፡ ዘኢማእምንት ፡ ይትወገር ፡ በእብን ፡ ወዘ
ተዐወረ ፡ ኪያሁ ፡ አነ ፡ እደመስሶ ።

፩ሺ.፰፻፹፯ ዘማዊ ፡ ወዘማዊት ፡ ይትቀተሉ ፡ ከማሁ
ዘይረክቦ ፡ በእንስሳ ፡ ብእሲሁ ፡ ይትቀተል ፡
ወእንስሳሁ ፡ ይትወገር ፡ መሠርይ ፡ ወተእ
ማኒ ይትቀተሉ ። ወኢታውስብ ፡ ብእሲተ ፡
ዘማዊተ ፡ ወኢ ፡ እንተ ፡ ደኀርዋ ። ወለተ ፡
ካህን ፡ ለእመ ፡ ዘመወት ፡ እስመ ፡ እስተኃፈ

ስለ ፡ ብሉይና ፡ ሐዲስ ።

ጊዜ ፡ ስታጭዱ ፡ ማጨጃችን ፡ አትጠናቀቁ ።
(አጥርታችሁ ፡ አትጨዱ) ፡ ከእርሱ ፡ የወደቀ
ውንም ፡ አትልቀም ። ወይንህንም ፡ ከለቀምህ ፡
በኋላ ፡ አትመልስ ። የተረፈውንም ፡ አትል
ቀም ። ለደኻና ፡ ለስደተኛ ፡ ተወው ፡ እንጂ ።
ዘሌ ፡ ፲፱ ፡ ፱ - ፲፱) ።

፩ሺ.፰፻፹፫ እኔ ፡ ፈጣሪያችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ መልካ
ሙን ፡ እከፍላችኋለሁ ። የምንደኛን ፡ ደመወዝ ፡
እስኪነጋ ፡ ድረስ ፡ በአንተ ፡ ዘንድ ፡ አታሳድር ።
በደንቆሮ ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አትናገር ።
በዕውር ፡ ፊት ፡ እንቅፋት ፡ አትጨምር ። በዖ
ፍም ፡ አታሟርት ። አትዘሩፉም ።

፩ሺ.፰፻፹፬ ከራሳችሁ ፡ ፀጕር ፡ ቁርንጎ ፡ አትሥሩ ።
የራስ ፡ ፀጕርህን ፡ እኩሌታ ፡ አትላጭ ። የ ጢ
ማችሁንም ፡ ስፋት ፡ አትላጩ ። የሞተም ፡
ቢኖር ፡ ፊታችሁን ፡ አትንጩ ። ወደ ፡ ሥጋችሁ
ም ፡ ምላጭ ፡ አታቅርቡ ። ሰውነታችሁንም ፡
በመርፌ ፡ አትነቀሱ ። ሴት ፡ ልጅህን ፡ አመን
ዝራ ፡ አታድርጋት ። ወደሟርቶኛ ፡ ሰዎችና ፡
ወደባለአምልኮቶች ፡ አትሂድ ። የሥራይ ፡ ሰዎ
ችን ፡ (ሥራይ ፡ የሚያደርጉ ፡ ሰዎችን) ፡ አትከተ
ላቸው ። የተሰወረውን ፡ የማውቅ ፡ እኔ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ፈጣሪያችሁ ፡ ነኝና ።

፩ሺ.፰፻፹፭ ከአንተ ፡ የሚሸመግለውንም ፡ አክብረው ።
በሀገራችሁ ፡ በሚኖር ፡ መጻተኛ ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡
ነገር ፡ አታድርጉ ። በመካከላችሁም ፡ ከእና
ንተ ፡ እንደ ፡ አንዱ ፡ ይሁን ። በፍርድ ፡ ወይም ፡
በቍጥር ፡ ልክ ፡ በሚዛን ፡ ወይም ፡ በመሥፈ
ሪያ ፡ ዓመፅን ፡ አታድርጉ ። ሚዛኖችህ ፡ በእው
ነት ፡ ይሁኑ ፡ እንጂ ። የሚዛንህ ፡ (የምትመዝን
ባቸው) ፡ ድንጋዮችም ፡ በእውነት ፡ ይሁኑ ።
መስፈሪያህና ፡ ጎሞርህም ፡ በእውነት ፡ ይሁን
ላችሁ ። እኔ ፡ ፈጣሪያችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡
ቅን ፡ ነኝና ። (ዘሌ ፡ ፲፱ ፡ ፱ - ፴፯) ።

፩ሺ.፰፻፹፮ በአላመነች ፡ በባዕድ ፡ ሴት ፡ ውስጥ ፡ ዘርዕ ፡
ያፈሰሰ ፡ በደንጋይ ፡ ይወገር ። እርሱንም ፡ ቸል ፡
ያለውን ፡ እኔ ፡ ለጠፋዋለሁ ። (ዘሌ ፡ ፳ ፡ ፱) ።

፩ሺ.፰፻፹፯ ዘማዊና ፡ ዘማዊት ፡ (አመንዝራና ፡ አመንዝራ
ዪት) ፡ ይገደሉ ። እንደዚሁም ፡ በከብት ፡ የረ
ከበ ፡ በውየው ፡ ይገደል ። እንስሳውም ፡ ይወ
ገር ። መሠርይ ፡ በእርሱም ፡ የሚያምን ይገ
ደሉ ። (ዘሌ ፡ ፳ ፡ ፲ ። ፳ ፡ ፳፯) ። አመንዝራዪ
ቱን ፡ ወይም ፡ የፈቷትን ፡ ሴት ፡ አታግባ ። የካ

አንቀጽ ፡ ፶፩ ።

ረቶ ፡ ለእቡሃ ፡ ያውዕይዋ ፡ በእሳት ።

፩ሺ፭፻፹፰ ወካህን ፡ ዘየዐቢ ፡ ኢይንጺ ፡ ሥዕርቶ ፡ ወኢ ይሥጥጥ ፡ አልባሲሁ ፡ ላዕለ ፡ ዘሞተ ፡ ወኢያ ውስብ ፡ ዘአንበለ ፡ ድንግል ፡ እንተ ፡ እምነገዱ ።

፩ሺ፭፻፹፱ ወመበለተስ ፡ አው ፡ እንተ ፡ ደኀርዋ ፡ አው ፡ እንተ ፡ ዘመወት ፡ ኢያውስብ ፡ አሐተ ፡ እምኔ ሆን ።

፩ሺ፭፻፺ ወዘሂ ፡ ቀርበ ፡ ኀበ ፡ ቅድሳት ፡ እንዘ ፡ ርኩስ ፡ ውእቱ ፡ ትሠረው ፡ ይእቲ ፡ ነፍስ ፡ እምኀቤየ ። መኑሂ ፡ ዘእምባዕድ ፡ ዘመድ ፡ ኢይብላዕ ፡ እም ቅድሳት ፡ እስከ ፡ ፈላሲሁ ፡ ለካህን ፡ ወዓሳቡ ።

፩ሺ፭፻፺፩ ወዘሰ ፡ አጥረየ ፡ ካህን ፡ በንዋዩ ፡ ወዘሂ ፡ ተወልደ ፡ በቤቱ ፡ ይብልዑ ፡ እመባልዕቲሁ ። ወወለቱ ፡ ብእሲ ፡ ካህን ፡ ለእመ ፡ አውሰበት ፡ ብእሴ ፡ እምካልእ ፡ ዘመድ ፡ ኢትብላዕ ፡ እምዓ ሥራት ፡ ዘቅድሳት ።

፩ሺ፭፻፺፪ ወዘበ ፡ ነውር ፡ ላዕሌሁ ፡ ኢታምጽኡ ፡ መባአ ፡ እስመ ፡ ኢይሠጠወክሙ ፡ ወኵሎ ፡ ዓሥራተ ፡ አልሕምት ፡ ወአባግዕ ፡ ይኩን ፡ ዓሥ ራየ ፡ ቅዱስ ፡ ለእግዚአብሔር ።

፩ሺ፭፻፺፫ ትዳ ፡ ወነበቦ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሙሴ ፡ ወይ ቤሎ ፡ በሎሙ ፡ ለካህናት ፡ ይባርክዎሙ ፡ ለሕ ዝብ ፡ እንዘ ፡ ይቤሉ ፡ "ለይባርከ ፡ እግዚአብ ሔር ፡ ወይዕቀብከ ፡ ወያብርህ ፡ ገጾ ፡ ላዕሌከ ፡ ወይምሐርከ ፡ ወይሚጥ ፡ ፊቶ ፡ ኀቤከ ፡ ወየሀብከ ፡ ሰላመ ።" ወይበሉ ፡ በስምየ ፡ ላዕለ ፡ ደቂቀ ፡ እስራኤል ፡ ወአነሂ ፡ እባርኮ ፡ ላዕሌ ሆሙ ።

፩ሺ፭፻፺፬ ትሔ ፡ ወኢታንቀልቅል ፡ እምነ ፡ ትእዛዝ ፡ ዘነገሩከ ፡ መኳንንት ፡ ኢ ፡ ለየማን ፡ ወኢ ፡ ለፀ ጋም ። ወኢታቅም ፡ ፩ደ ፡ ስማዕተ ፡ ላዕለ ፡ ብእሲ ፡ በምንትኒ ፡ ግብር ፡ እምአበሳ ፡ ወስሕ ተት ፡ አላ ፡ በስምዐ ፡ ፪ቱ ፡ ወ፫ቱ ፡ ይቁም ፡ ኵሉ ፡ ነገር ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ ስምዐ ፡ ፩ዱ ፡ በዐ መፃ ፡ ላዕለ ፡ ብእሲ ፡ ለይትኀሠሡ ፡ መኳንንት ፡ ፈድፋደ ፡ ወይግበሩ ፡ ቦቱ ፡ በከመ ፡ ፈተዶ ፡ ይ ደግበር ፡ ላዕለ ፡ ካልኡ ።

፩ሺ፭፻፺፭ ወአግብእ ፡ ዘኮነ ፡ እምኔከ ፡ እኩየ ፡ ወለ እመ ፡ ኢኮነ ፡ እምአዝማዲከ ፡ አው ፡ ዘኢተአ

ስለ ፡ ብሉይና ፡ ሐዲስ ።

ሀን ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ብትሰስን ፡ አባቷን ፡ እሳፍራ ዋለችና ፡ በእሳት ፡ ያቃጥሉዋት ።

፩ሺ፭፻፹፰ ታላቁ ፡ ካህን ፡ ለሞተ ፡ ሰው ፡ ጠጉሩን ፡ አይንጭ ። ልብሱንም ፡ አይቅደድ ። ከነገዱ ፡ ከሆነች ፡ ድንግል ፡ በቀር ፡ አያግባ ።

፩ሺ፭፻፹፱ ባል ፡ የሌላትን ፡ ወይም ፡ የፈቷትን ፡ ወይም ፡ የሰሰነችውን ፡ ከእነዚህ ፡ አንዲቱን ፡ አያግባ ። (ዘሌ ፡ ፳፪ ፡ ፪ - ፲፭) ።

፩ሺ፭፻፺ ርኩስ ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፡ ወደ ፡ ተቀደሰው ፡ የቀረ በው ፡ ሰው ፡ ነፍስ ፡ ከእኔ ፡ ዘንድ ፡ ትጥፋ ። እስከ ፡ ካህኑ ፡ መጻተኛ ፡ እስከ ፡ ምንደኛው ፡ ድረስ ፡ ከሌላ ፡ ወገን ፡ የሆነ ፡ ሁሉ ፡ ከመሥዋ ዕት ፡ አይብላ ።

፩ሺ፭፻፺፩ ካህን ፡ በገንዘቡ ፡ የገዛው ፡ በቤቱም ፡ የተወ ለደው ፡ ከሚባለው ፡ (ከመሥዋዕቱ) ፡ ይብሉ ። የካህኑ ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ከሌላ ፡ ወገን ፡ የሆነ ፡ ባል ፡ ብታገባ ፡ ለመሥዋዕት ፡ ከሚሆነው ፡ አሥራት ፡ አትብላ ። (ዘሌ ፡ ፳፪ ፡ ፫ - ፲፩ ።

፩ሺ፭፻፺፪ ነውር ፡ በላዩ ፡ ያለበትን ፡ መባዕ ፡ አድርጋ ችሁ ፡ አታምጡ ። አልቀበላችሁምና ። የላሞ ችና ፡ የበጎች ፡ አሥራት ፡ ሁሉ ፡ ለእግዚአብሔ ር ፡ የተለየ ፡ አሥራት ፡ ይሁን ። (ዘሌ ፡ ፳፪ ፡ ፲፰ - ፳፭) ።

፩ሺ፭፻፺፫ ትዳ ። እግዚአብሔርም ፡ ለሙሴ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ነገረው ። ሕዝቡን ፡ እንዲህ ፡ እያሉ ፡ ይመርቋቸው ፡ ዘንድ ፡ ለካህናት ፡ ንገራቸው ። እግዚአብሔር ፡ ይባርክህ ፡ ይጠብቅህም ። ፊቱ ንም ፡ ያብራልህ ። ይቅርም ፡ ይበልህ ። ፊቱ ንም ፡ በአንተ ፡ ያሳድር ። ሰላሙንም ፡ ይስጥህ ። በእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ ስሜን ፡ ይናገሩ ። እኔም ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡ እባርካለሁ ። (ዘኍ ፡ ፮ ፡ ፳፬ - ፳፯) ።

፩ሺ፭፻፺፬ ትሄ ። መኳንንት ፡ ከነገሩህ ፡ ትእዛዝ ፡ ወደ ቀኝ ፡ ወይም ፡ ወደግራ ፡ አትናወጥ ። ከበደልና ፡ ከስሕተት ፡ ወገን ፡ በማናቸውም ፡ ሥራ ፡ በሰው ላይ ፡ አንድ ፡ ምስክር ፡ አትጥራ ። ነገር ፡ ሁሉ ፡ በ፪ና ፡ በ፫ ፡ ምስክር ፡ ይጸና ፡ እንጂ ። አንድ ፡ ሰው ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ በዓመፅ ፡ (በሐሰት) ፡ ምስ ክር ፡ ቢሆን ፡ ዳኞች ፡ በጥብቅ ፡ መርምረው ፡ በሌላው ፡ ሊያደርግ ፡ እንደ ፡ ወደደ ፡ በእርሱ ፡ ያድርጉ ። (ዘዳ ፡ ፲፱ ፡ ፲፭ - ፳) ።

፩ሺ፭፻፺፭ ከወንድምህ ፡ የጠፋውን ፡ መልስለት ። ከዘ መዶችህም ፡ ወገን ፡ ባይሆን ፡ ወይም ፡ የማታ

አንቀጽ ፡ ፶፩ ።

ምሮ ፡ እንብሮ ፡ ኀበ ፡ ማኅደርከ ፡ ወየሀሉ ፡ ኀቤከ ፡ እስከ ፡ የኀሥሥ ፡ እኁከ ፡ ወታገብእ ፡ ኀቤሁ ፡ እንስሳሁ ፡ ወልብሶ ። ወለዙሉ ፡ ጕያዪ ፡ ኢይደልወከ ፡ ከመ ፡ ትትዐወር ፡ በእንቲአሁ ።

፩ሺ፭፻፺፮ ኢይልበሱ ፡ እደው ፡ አርእየ ፡ አንስት ፡ ወአንስትኒ ፡ ኢይልበሳ ፡ አርአየ ፡ እደው ፡ ወኢየሀሉ ፡ ሥርዓተ ፡ እደው ፡ ላዕለ ፡ አንስት ፡ ወኢሥርዓተ ፡ አንስት ፡ ላዕለ ፡ እደው ፡ እስመ ፡ ርኩስ ፡ ውእቱ ፡ ዝንቱ ።

፩ሺ፭፻፺፯ ግበር ፡ ተሥላሰ ፡ ሐፁር ፡ በቤትከ ፡ ወኢትኅድግ ፡ መካነ ፡ ዘየወድቀከ ፡ እምኔሁ ።

፩ሺ፭፻፺፰ ወለእመ ፡ ተረከበ ፡ ብእሲ ፡ ዘሰሀ ፡ ሰረቀ ፡ ነፍሰ ፡ እምአኀዊሁ ፡ ወቀነዮ ፡ እው ፡ ሤጣ ፡ ቅትሎ ፡ ለሰራቂ ።

፩ሺ፭፻፺፱ ወእምከመ ፡ ኮነ ፡ ተጻልአ ፡ ማእከለ ፡ ሰብእ ፡ ያምጽእዎሙ ፡ ኀበ ፡ መኳንንት ፡ ከመ ፡ ይፍትሑ ፡ ማእከሌሆሙ ፡ ወያጸድቅዎ ፡ ለጻድቅ ፡ ወየዐምፅዎ ፡ ለዐማፂ ።

፩ሺ፮፻ ወሰእመ ፡ ይደልዎ ፡ ለዓማፂ ፡ ቅሥፈት ፡ ያሰክብዎ ፡ በከብዱ ፡ ወይቅሥፎ ፡ በቅድሜሁ ፡ በአምጣነ ፡ ኀጢአቱ ፡ ይቅሥፎ ፡ በኁልቈ ፡ ፵ ፡ ወኢይወስኩ ፡ ላዕሌሁ ፡ ምንተኒ ።

፩ሺ፮፻፩ ወኢትፋፅም ፡ እፉሁ ፡ ለላህም ፡ ሶበ ፡ ያኀይድ ፡ እክለ ።

፩ሺ፮፻፪ ወዳግማዊሰ ፡ ሕግ ፡ ዐ ፡ እምኔሁ ፡ ዘያኤምር ፡ ኀበ ፡ ልዑላን ፡ ኀበ ፡ ኅርየተ ፡ ፈቃዱ ፡ ለዘያፈቅድ ፡ ይኩን ፡ ፍጹመ ፡ ዘከመ ፡ ዐቂበ ፡ ድንግልና ፡ በከመ ፡ ተነግረ ፡ በአንቀጽ ፡ ተዋስቦ ። ወዘከመ ፡ ኀዲፈ ፡ ንዋይ ፡ ወመንግሥት ፡ ፍጹመ ፡ ወኀዲፈ ፡ ዓለም ፡ ወተሊወ ፡ ክርስቶስ ፡ ወምግባራቲሁ ፡ በአምጣነ ፡ ኀይሉ ፡ ለሥጋዊ ፡ በከመ ፡ ተነግረ ፡ በአንቀጸ ፡ መነኮሳት ።

፩ሺ፮፻፫ ወእምኔሁ ፡ ዘተነግረ ፡ ትእዛዙ ፡ ፍጹመ ፡ ዘከመ ፡ ገሥጾተ ፡ ኀይለ ፡ መዓት ፡ ወኀይለ ፡ ፍትወት ፡ ወእሠንዮ ፡ ለዘእሠነየ ፡ ወለዘእሒሠሠየ ፡ ወኀዲገ ፡ አድልዎ ፡ ሙሰተ ፡ እምልከ ፡ በምጽዋት ፡ ወጸሎት ፡ ወጾም ፡ ውኀሚዝ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ሀየንተ ፡ ካልአኒሁ ፡ ወምሂሮተ ፡ ሰብእ ፡ ምግባረ ፡ ትሩፋት ፡ ወገቢሮሙ ፡

ስለ ፡ ብሉይና ፡ ሐዲስ ።

ውቀው ፡ ቢሆን ፡ በቤትህ ፡ አኑረው ። ወንድምህ ፡ እስኪፈልገው ፡ ድረስ ፡ በአንተ ፡ ዘንድ ፡ ይኑር ። እንስሳውንና ፡ ልብሱንም ፡ ትመልስለታለህ ። ስለ ፡ ኩብላይም ፡ ሁሉ ፡ ቸል ፡ ልትል ፡ አይገባህም ።

፩ሺ፭፻፺፮ ወንዶች ፡ እንደ ፡ ሴቶች ፡ አይልበሱ ። ሴቶችም ፡ እንደ ፡ ወንዶች ፡ አይልበሱ ። የወንዶች ፡ ሥርዓት ፡ በሴቶች ፡ ላይ ፡ የሴቶችም ፡ ሥርዓት ፡ በወንዶች ፡ ላይ ፡ አይኑር ። ይህ ፡ ርኩስ ፡ ነውና ። (ዘዳ ፡ ፳፪ ፡ ፩ - ፮) ።

፩ሺ፭፻፺፯ በቤትህ ፡ ፫ ፡ ደረጃ ፡ እብጅ ። (፫ ፡ ቅጥር ፡ እብጅ) ፡ ከእርሱም ፡ የሚጥልህን ፡ ቦታ ፡ አትተው ። (ዘዳ ፡ ፳፪ - ፰) ።

፩ሺ፭፻፺፰ ከወንድሞቹ ፡ ወገን ፡ እነሆ ፡ ነፍስ ፡ የሰረቀ ፡ የገዛትም ፡ ወይም ፡ የሸጣት ፡ ሰው ፡ ቢገኝ ፡ ሌባውን ፡ ግደለው ። (ዘዳ ፡ ፳፬ ፡ ፯) ።

፩ሺ፭፻፺፱ በሰዎች ፡ መካከል ፡ ጠብ ፡ ቢሆን ፡ በመካከላቸው ፡ ይፈርዱ ፡ ዘንድ ፡ ወደዳኞች ፡ ያምጡቸው ። እውነተኛውን ፡ እውነተኛ ፡ ነህ ፡ ይበሉት ። በደለኛውንም ፡ በደለኛ ፡ ነህ ፡ ይበሉት ።

፩ሺ፮፻ ለዓመፀኛም ፡ ግርፋት ፡ ቢገባው ፡ በሆዱ ፡ ያስተኙት ። በፊቱም ፡ ይግረፈው ። በኃጢአቱ ፡ ልክ ፡ አርባ ፡ ቍጥር ፡ ይግረፈው ። ከአርባ ፡ በላይ ፡ ምንም ፡ አይጨምሩ ።

፩ሺ፮፻፩ እህል ፡ በምታበራይ ፡ ጊዜ ፡ የበሬውን ፡ አፍ ፡ አታፍን ። (ዘዳ ፡ ፳፭ ፡ ፩ - ፭) ።

፩ሺ፮፻፪ ሁለተኛው ፡ ሕግ ፡ ግን ፡ ፍጹም ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ የሚወድ ፡ ሰው ፡ ወደሚሻው ፡ ምርጫ ፡ ወደ ፡ ከፍተኞች ፡ የሚያመለክት ፡ ከእርሱ ፡ ወገን ፡ አለ ። ይኸውም ፡ በጋብቻ ፡ አንቀጽ ፡ እንደተነገረ ፡ ድንግልናን ፡ እንደመጠበቅ ፡ ገንዘብንም ፡ እንደመተውና ፡ ፈጽሞ ፡ እንደመናቅ ዓለምንም ፡ ትቶ ፡ ክርስቶስንና ፡ ሥራዎቹን ፡ በሥጋዊ ፡ ተፈጥሮ ፡ ኃይል ፡ ልክ ፡ እንደመከተል ፡ ያለ ፡ ነው ። በአንቀጸ ፡ መነኮሳት ፡ እንደ ተነገረ ። (ፍ ፡ ነ ፡ ፫፻፵፬ ። ፰፻፴) ።

፩ሺ፮፻፫ ከእርሱም ፡ ፈጽሞ ፡ የተነገረ ፡ ትእዛዙ ፡ የቁጣን ፡ ኀይልና ፡ የፍትወትን ፡ ኀይል ፡ እንደ ፡ መግታት ፡ ነው ። መልካም ፡ ለአደረገና ፡ ክፉም ፡ ለአደረገ ፡ መልካም ፡ ማድረግ ፡ በእምልኮ ፡ በምጽዋትና ፡ በጸሎት ፡ በጾምም ፡ ጊዜ ፡ አድልዎን ፡ መተው ፡ ስለሌላዎቹም ፡ ፈንታ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያትን ፡ መሻት ፡ ለሰዎችም ፡

አንቀጽ ፡ ፺፭ ።

በቅድሜሁ ፡ ወትስማሥት ፡ ላዕለ ፡ ምንዳቤ ፡ በሐዊረ ፡ ፍኖት ፡ እንተ ፡ ታበጽሕ ፡ ውስተ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ። ወተንሥኦ ፡ ላዕለ ፡ ተቀትሎ ፡ በእንበለ ፡ ግዚእ ፡ እምሃይማኖተ ፡ ጽድቅ ፡ በከመ ፡ ተነግረ ፡ በአንቀጸ ፡ ሰማዕታት

፩ሺ፰፻፶፱ ቃለ ፡ ወንጌል ፡ ዘእማቴዎስ ፡ ወንጌላዊ ፡ በእንተ ፡ እግዚእነ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ሎቱ ፡ ስብሐት ፡ ዘይቤ ፡ ወሶበ ፡ ርእየ ፡ እግዚእ ፡ ኢየሱስ ፡ ብዙኃነ ፡ አሕዛበ ፡ ዐርገ ፡ ውስተ ፡ ደብር ፡ ወነበረ ፡ ወመጽኡ ፡ አርዳኢሁ ፡ ኀቤሁ ፡ ወከሠተ ፡ አፉሁ ፡ እግዚእ ፡ ኢየሱስ ፡ ወመሀሮሙ ፡ እንዘ ፡ ይብል ፡ ብፁዓን ፡ ነዳያን ፡ በመንፈስ ፡ እስመ ፡ሎሙ ፡ ይእቲ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ። ብፁዓን ፡ እለ ፡ ይላሕዉ ፡ ይእዜ ፡ እስመ ፡ እሙንቱ ፡ ይትፌሥሑ ። ብፁዓን ፡ ትሑታን ፡ እስመ እሙንቱ ፡ ይወርስዋ ፡ ለምድር ። ብፁዓን ፡ እለ ፡ ይርኅቡ ፡ ወይጸምኡ ፡ በእንተ ፡ ጽድቅ ፡ እስመ ፡ እሙንቱ ፡ ይጸግቡ ። ብፁዓን ፡ መሓርያን ፡ እስመ ፡ ሎሙኒ ፡ ይምሕርዎሙ ። ብፁዓን ፡ ንጹሓነ ፡ ልብ ፡ እስመ ፡ እሙንቱ ፡ ይሬእይዎ ፡ ለእግዚአብሔር ። ብፁዓን ፡ ገባርያነ ፡ ሰላም ፡ እስመ ፡ እሙንቱ ፡ ውሉደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይሰመዩ ። ብፁዓን ፡ እለ ፡ ይሰደዱ ፡ በእንተ ፡ ጽድቅ ፡ እስመ ፡ ሎሙ ፡ ይእቲ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ። ብፁዓን ፡ አንትሙ ፡ ሶበ ፡ ይሰድዱክሙ ፡ ወይጼእሉክሙ ፡ ወይዘነጕጉክሙ ፡ ወይነቡ ፡ ኵሎ ፡ እኩየ ፡ በላዕሌክሙ ፡ እንዘ ፡ ይሔስዉ ፡ ዲቤክሙ ፡ በእንቲአየ ፡ ተፈሥሑ ፡ ወተኀሠዩ ፡ እስመ ፡ ዐስብክሙ ፡ ዐቢይ ፡ በሰማያት ፡ እስመ ፡ከማሁ ፡ ሰደድዎሙ ፡ ለነቢያት ፡ እለ ፡ እምቅድሜክሙ ። ይብራህ ፡ ብርሃንክሙ፡ በቅድመ ፡ ሰብእ ፡ ከመ ፡ ይርአዩ ፡ ምግባራቲክሙ ፡ ሠናየ ፡ ወይሰብሕዎ ፡ ለአቡክሙ ፡ ዘበሰማያት ። ወዘሰ ፡ ይገብር ፡ ወይሜህር ፡ ዐቢየ ፡ ይሰመይ ፡ በመንግሥተ ፡ ሰማያት ። እብለክሙ ለእመ ፡ ኢያፈድፈድክሙ ፡ ጸዲቀ ፡ እምጸሐፍት ፡ ወፈሪሳውያን ፡ ኢትበውኡ ፡ ውስተ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ።"

፩ሺ፰፻፷፰ ዘሀቱ ፡ ሰማዕክሙ ፡ ዘተብህለ ፡ ለቀደምት ፡ ክሙ ፡ ኢትቅትል ፡ ነፍሰ ፡ ወለዘቀተለ ፡ ነፍሰ ፡ ይደሉ ፡ ላዕሌሁ ፡ ኵነኔ ። ወአንሰ ፡ እብለክሙ ፡

ስለ ፡ ብሉይና ፡ ሐዲስ ።

የትሩፋትን ፡ ሥራ ፡ ማስተማር ፡ በፊቱም ፡ እርሱዋን ፡ መሥራት ፡ ወደ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ የምታደርስ ፡ መንገድን ፡ በመሄድ ፡ ጊዜ ፡ በችግር ፡ ላይ ፡ መታገሥ ፡ በአንቀጸ ፡ ሰማዕት ፡ እንደተነገረ ፡ ከእውነተኛው ፡ ሃይማኖት ፡ ባለ መመለስ ፡ ለመሞት ፡ መጨከን ፡ ነው ። (ፍ ፡ ነ ፡ ፯፻፷፩) ።

፩ሺ፰፻፶፱ ምስጋና ፡ ይግባውና ፡ ስለጌታችን ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ወንጌላዊ ፡ ማቴዎስ ፡ ከጻፈው ፡ የወንጌል ፡ ቃል ፡ ፷ ። ጌታ ፡ ኢየሱስ ፡ ብዙ ፡ ሰዎችን ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ከተራራ ፡ ላይ ፡ ወጥቶ ፡ ተቀመጠ ። ደቀ ፡ መዛሙርቱም ፡ ወደእርሱ ፡ መጡ ። ጌታ ፡ ኢየሱስም ፡ ነገሩን ፡ ጀመረ ። እንዲህም ፡ እያለ ፡ አስተማራቸው ። በመንፈስ ፡ ድሆች ፡ የሆኑ ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ። መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ የእነርሱ ፡ ናትና ። ዛሬ ፡ የሚያለቅሱ ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ። ደስ ፡ ይላችዋልና ። ትሑታን ብፁዓን ፡ ናቸው ። እነርሱ ፡ ምድርን ፡ ይወርሱዋታልና ። ስለ ፡ ጽድቅ ፡ የሚራቡና ፡ የሚጠሙ ብፁዓን ፡ ናቸው ። እነርሱ ፡ ይጠግባሉና ። ይቅር ፡ የሚሉ ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ። እነርሱንም ፡ ይቅር ፡ ይሏቸዋልና ። ልበ ፡ ንጹሖች ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ። እነርሱ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ያዩታልና ። ሰላምን ፡ የሚያደርጉ ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ። እነርሱ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ልጆች ፡ ይባላሉና ። ስለ፡ ጽድቅ ፡ የሚሰደዱ ፡ ብፁዓን ፡ ናቸው ። መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ የእነርሱ ፡ ናትና ። ቢያሳድዱዋችሁ ፡ ቢሰድቡዋችሁ ፡ ቢነቅፉዋችሁ ፡ ስለእኔም ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ እየዋሹ ፡ በላያችሁ ፡ ክፉን ፡ ሁሉ ፡ ቢናገሩም ፡ ብፁዓን ፡ ናችሁ ። ዋጋችሁም ፡ በሰማያት ፡ ታላቅ ፡ ነውና ፡ ፈጽሞ ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ። ከእናንተ ፡ አስቀድሞ ፡ የነበሩ ፡ ነቢያትን ፡ እንደዚሁ ፡ አሳድደዋቸዋልና ። ብርሃናችሁ ፡ በሰዎች ፡ ፊት ፡ ይብራ ። ሥራችሁን ፡ አይተው ፡ በሰማይ ፡ ያለ ፡ አባታችሁን ፡ ያመሰግኑት ፡ ዘንድ ። የሚሠራ ፡ ግን ፡ የሚያስተምርም ፡ በመንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ታላቅ ፡ ይባላል ። ከጸሐፍትና ፡ ከፈሪሳውያን ፡ ጽድቅን ፡ካላበለጣችሁ ፡ ወደ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ አትገቡም ፡ እላችኋለሁ ።

፩ሺ፰፻፷፰ ሀ ። ለቀደሙት ፡ ነፍስ ፡ አትግደል ፡ የተባለውን ፡ ሰምታችኋል ። ነፍስ ፡ ለገደለም ፡ ቅጣት፡ ይገባዋል ። እኔ ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ። በወንድሙ

እስመ ፡ ኵሉ ፡ ዘይትመዐዕ ፡ ላዕለ ፡ እኁሁ ፡ በከንቱ ፡ ደለወ ፡ ላዕሌሁ ፡ ኵነኔ ፡ ወዘይቤሎ ፡ ለእኁሁ ፡ ርሑሕ ፡ ዘፀርቅ ፡ ደለዎ ፡ ነውረ ፡ ማኅበር ፡ ወዘሂ ፡ ይቤሎ ፡ ለእኁሁ ፡ ዓብድ ፡ ደለዎ ፡ እሳተ ፡ ገሃነም ፡ ለእመ ፡ እንተ ፡ እምጻእከ ፡ መባእከ ፡ ኀበ ፡ ምሥዋዕ ፡ ወተዘከርከ ፡ በህየ ፡ ከመ ፡ ቦ ፡ እኁከ ፡ ዘተኀየሰከ ፡ ኅድግ ፡ ህየ ፡ መባእከ ፡ ቅድመ ፡ ምሥዋዕ ፡ ወሑር ፡ ቅድመ ፡ ወተዐረቅ ፡ ምስለ ፡ እኁከ ፡ ወእምዝ ፡ ገቢእከ ፡ አብእ ፡ መባእከ ።

፩ሺ፰፻፺፭ ሰማዕክሙ ፡ ዘተብህለ ፡ ለቀደምት ፡ ኢትዘምዉ ፡ ወእንሰ ፡ እብለክሙ ፡ ኵሉ ፡ ዘርእያ ፡ ለብእሲት ፡ ወፈተዋ ፡ ዘመወ ፡ ባቲ ፡ በልቡ ። ተብህለ ፡ ዘይድኅራ ፡ ለብእሲቱ ፡ የሀብ ፡ ላቲ ፡ መጽሐፈ ፡ ኅዳጋቲሃ ፡ ወእንሰ ፡ እብለክሙ ፡ ዘይድኅራ ፡ ለብእሲቱ ፡ ዘእንበለ ፡ ነገረ ፡ ዝሙት ፡ ለሊሁ ፡ ረሰያ ፡ ዘማዊተ ፡ ወዘሂ ፡ አውሰበ ፡ ኅድግተ ፡ ናሁ ፡ ዘመወ ።

፩ሺ፰፻፺፮ ወካዕበ ፡ ሰማዕክሙ ፡ ዘተብህለ ፡ ለቀደምት ፡ ኢትምሐል ፡ በሐሰት ፡ ወአግብእ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መሐላከ ። ወእንሰ ፡ እብለክሙ ፡ ኢትምሐሉ ፡ ግሙራ ፡ ኢ ፡ በሰማይ ፡ እስመ ፡ መንበሩ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ውእቱ ፡ ወኢ ፡ በምድር ፡ እስመ ፡ መከየደ ፡ እገሪሁ ፡ ይእቲ ፡ ወኢ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ እስመ ፡ ይእቲ ፡ ሀገሩ ፡ ለንጉሥ ፡ ዐቢይ ። ወኢትምሐል ፡ በርእስከ ፡ እስመ ፡ ኢይትክህለከ ፡ ትግበር ፡ አሐተ ፡ እምሥዕርት ፡ ርእስከ ፡ ኢጸዓዳ ፡ ወኢጸሊመ ፡ አላ ፡ ይኩን ፡ ቃልክሙ ፡ እመኒ ፡ እወ ፡ እወ ፡ ወእመኒ ፡ አልቦ ፡ አልቦ ፡ ወዘፈድፋደ ፡ እምዝንቱ ፡ እምእኩይ ፡ ውእቱ ።

፩ሺ፰፻፺፯ ሰማዕክሙ ፡ ዘተብህለ ፡ ዓይን ፡ ቤዛ ፡ ዓይን ፡ ወሰን ፡ ቤዛ ፡ ስን ፡ ወእንሰ ፡ እብለክሙ ፡ ኢትትቃወምዎ ፡ ለእኩይ ፡ በእኩይ ፡ ግሙራ ። ወለዘሂ ፡ ጸፍዐከ ፡ መልታሕቴከ ፡ ዘየማን ፡ ሚጥ ፡ሎቱ ፡ ካልእታሂ ። ወለዘሂ ፡ ፈቀደ ፡ ይትዓገልከ ልብሰከ ፡ ኅድግ ፡ ሎቱ ፡ ክዳነከሂ ። ወለዘሂ ፡ ዐበጠከ ፡ ፩ደ ፡ ምዕራፈ ፡ ሑር ፡ ምስሌሁ ፡ ፪ተ ፡ ምዕራፈ ። ምዕራፍ ፡ ብሂል ፡ ብጽሐተ ፡ እንሥእ ንጻሬ ፡ ወለዘሰእለከ ፡ ሀቦ ፡ ወለዘፈቀደ ፡ ይትለቃሕ ፡ እምኔከ ፡ ኢትክልኦ ። ሰማዕክሙ ፡ ዘተብህለ ፡ አፍቅር ፡ ቢጸከ ፡ ወጽላእ ፡ ጸላኢከ ። ወእንሰ ፡ እብለክሙ ፡ አፍቅሩ ፡ ጸላእተክሙ ፡



ላይ ፡ በከንቱ ፡ የሚቆጣ ፡ ሁሉ ፡ ቅጣት ፡ ይገባዋል ። ወንድሙንም ፡ ጨርቃም ፡ ወራዳ ፡ የሚለው ፡ የሸንጎ ፡ ቅጣት ፡ (ፍርድ) ፡ ይገባዋል ። ወንድሙንም ፡ ደንቆሮ ፡ የሚለው ፡ የገሃነም ፡ እሳት ፡ ተገባው ። መባሕህን ፡ ወደምሥዋዕ ፡ ብታመጣ ፡ ከዚያም ፡ የተጣላህ ፡ ወንድምህ ፡ እንዳለ ፡ ብታስብ ፡ መባዕህን ፡ ከዚያው ፡ ከምሥዋዑ ፡ ፊት ፡ ትተህ ፡ ሂድና ፡ አስቀድመህ ፡ ከወንድምህ ፡ ጋር ፡ ታረቅ ። ከዚህ ፡ በኋላም ፡ ተመልሰህ ፡ መባዕህን ፡ አግባ ።

፩ሺ፰፻፺፭ ለቀደሙት ፡ አትስሰኑ ፡ የተባለውን ፡ ሰምታችኋል ። እኔ ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ። ሴትን ፡ አይቶ ፡ የወደዳት ፡ ሁሉ ፡ በልቡ ፡ አመንዝሮባት ። ሚስቱን ፡ የሚፈታ ፡ ሰው ፡ የፍችዋን ፡ ደብዳቤ ፡ ይስጣት ፡ ተባለ ። እኔ ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ። ያለዝሙት ፡ ነገር ፡ ሚስቱን ፡ የሚፈታ ፡ ሰው ፡ ራሱ ፡ አመንዝራ ፡ አደረጋት ። የተፈታችዋንም ፡ ያገባ ፡ እነሆ ፡ አመነዘረ ።

፩ሺ፰፻፺፮ ዳግመኛም ፡ ለቀደሙት ፡ የተባለውን ፡ ሰምታችኋል ። በሐሰት ፡ አትማል ። መሐላህንም ፡ ለእግዚአብሔር ፡ መልስ ። እኔ ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ። ከቶ ፡ አትማሉ ። በሰማይም ፡ ቢሆን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ዙፋን ፡ ነውና ። በምድርም ፡ ቢሆን ፡ የእግሩ ፡ መረገጫ ፡ ናትና ። በኢየሩሳሌምም ፡ ቢሆን ፡ የታላቁ ፡ ንጉሥ ፡ አገር ፡ ናትና ። በራስህም ፡ አትማል ። ከራስህ ፡ ጠጉር ፡ አንዲቱን ፡ ነጭ ፡ ወይም ፡ ጥቁር ፡ ልታደርግ ፡ አትችልምና ። ነገራችሁ ፡ አዎን ፡ አዎን ፡ ወይም ፡ አይደለም ፡ አይደለም ፡ ይሁን ፡ እንጂ ። ከዚህም ፡ የበዛው ፡ (የወጣ) ፡ ከክፉ ፡ ወገን ፡ ነው ።

፩ሺ፰፻፺፯ ለቀደሙት ፡ የተባለውን ፡ ሰምታችኋል ። ዓይን ፡ የዓይን ፡ ቤዛ ፡ ነው ። ጥርስም ፡ የጥርስ ፡ ቤዛ ፡ ነው ። እኔ ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ። ክፉውን ፡ በክፉ ፡ ከቶ ፡ አትቃወሙት ። ቀኝ ፡ ፊትህን ፡ በጥፊ ፡ ለመታህ ፡ ሁለተኛዋንም ፡ መልስለት ። እጀጠባብህን ፡ ሊቀማህ ፡ ለወደደም ፡ መጐናጸፊያህን ፡ ተውለት ። አንድ ፡ ምዕራፍ ፡ ቢመልስልህ ፡ (ቢወስድህ) ፡ ሁለት ፡ ምዕራፍ ፡ ከእርሱ ፡ ጋር ፡ ሂድ ። ምዕራፍ ፡ ማለት ፡ ማየትን ፡ ማንሣት ፡ የሚያደርስበት ፡ ነው ። (የዓይን ፡ አስተያየት ፡ የሚያደርስበት ፡ ነው) ፡ ለለመነህም ፡ ስጠው ። ከአንተ ፡ ሊበደር ፡ የሚሻውን ፡ አት

ወደኀርዎሙ ፡ ለእለ ፡ ይረግሙክሙ ፡ ወእሠንዩ ፡ ለእለ ፡ ይጸልኡክሙ ፡ ወጸልዩ ፡ ዲበ ፡ እለ ይትዔገሉክሙ ፡ ወይሰድዱክሙ ፡ ወያቴክዙክሙ ፡ ከመ ፡ ይኩኑ ፡ ውሉዶ ለአቡክሙ ፡ ዘበሰማያት ። እስመ ፡ ውእቱ ፡ ያሠርቅ ፡ ፀሐዮ ፡ ላዕለ ፡ ኄራን ፡ ወእኩያን ፡ ወያዘንም ፡ ዝናመ ፡ ላዕለ ፡ ጻድቃን ፡ ወዐማፅያን ፡ ኩኑ ፡ አንትሙኒ ፡ ፍጹማነ ፡ ከመ ፡ አቡክሙ ፡ ሰማያዊ ፡ ፍጹም ፡ ውእቱ ።

፩ሺ፮፻፱ ርእዩ ፡ ኢትግበሩ ፡ ጽድቀክሙ ፡ በቅድመ ፡ ሰብእ ፡ ከመ ፡ ይርአዩክሙ ፡ እመ ፡ አኮሰ ፡ ዓስበ ፡ አልብክሙ ፡ በኀበ ፡ አቡክሙ ፡ በሰማያት ። ወሶበሂ ፡ ትጼልዩ ፡ ኢትኩኑ ፡ ከመ ፡ መደልዋን ፡ እማን ፡ እብለክሙ ፡ ከመ ፡ እሙንቱ ፡ ነሥኡ ፡ ዕሴቶሙ ፡ ወሠለጡ ፡ ዓስቦሙ ። ወሶበሂ ፡ ትጸውሙ ፡ ኢትቍጽሩ ፡ ገጸክሙ ፡ ከመ ፡ መደልዋን ።

፩ሺ፮፻፲ ኢትዝግቡ ፡ ለክሙ ፡ መዝገበ ፡ በውስተ ፡ ምድር ፡ ዳእሙ ፡ በውስተ ፡ ሰማያት ፡ ውንበ ፡ ሀሎ ፡ መዝገብክሙ ፡ ሀየ ፡ ይሄሉ ፡ ልብክሙ ። ኢይክል ፡ ፩ዱ ፡ ገብር ፡ ተቀንዮ ፡ ለ፪ቱ ፡ አጋእዝት ፡ ኢትክሉሂ ፡ ተቀንዮ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ወለንዋይ ። ኅሥሡ ፡ ቅድመ ፡ መንግሥተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወጽድቆ ፡ ወዝንቱሰ ፡ ኵሉ ፡ ይትዌሰክክሙ ። ኢተሐልዩ ፡ ለጌሠም ፡ እስመ ፡ ጌሠምሰ ፡ ትሔሊ ፡ ለርእሳ ፡ ወየአክላ ፡ ለዕለት ፡ እኪያ ።

፩ሺ፮፻፲፩ ኢትኰንኑ ፡ ከመ ፡ ኢትትኰነኑ ፡ ቅድመ ፡ አውፅእ ፡ ሠርዌ ፡ እምዓይንከ ፡ ወይእተ ፡ ጊዜ ፡ ትሬኢ ፡ ከመ ፡ ታውፅእ ፡ ሐሠረ ፡ ዘውስተ ፡ ዓይኑ ፡ ለካልእከ ። ኢተሀቡ ፡ ቅድሳተ ፡ ለከለባት ፡ ስእሉ ፡ ወይትወሀበክሙ ፡ ኅሡ ፡ ወትረክቡ ፡ ጐድጒዱ ፡ ወይትረኀው ፡ ለክሙ ። በከመ ፡ ትፈቅዱ ፡ ይግበሩ ፡ ለክሙ ፡ ሰብእ ፡ ግበሩ ፡ ሎሙ ፡ አንትሙሂ ፡ እስመ ፡ ከመዝ ፡ ውእቱ ፡ ኦሪትሂ ፡ ወነቢያትሂ ። ባኡ ፡ እንተ ፡ ጸባብ ፡ አንቀጽ ፡ እንተ ፡ ትወስድ ፡ ውስተ ፡ ሕይወት ፡ እስመ ፡ ሰፋሕት ፡ ይእቲ ፡ ስሐዊር ፡ ወፋኖትሰ ፡ ርኅብት ፡ ይእቲ ፡ እንተ ፡ ትወስድ ፡ ውስተ ፡ ኀጒል ። ተዓቀቡ ፡ እንከ ፡ እምሐሳውያነ ፡ ነቢያት ፡ እለ ፡ ይመጽኡ ፡ ኀቤክሙ ፡ በአልባስ ፡



ከልክለው ። ጓደኛህን ፡ ውደድ ፡ ጠላትህንም ፡ ጥላ ፡ የተባለውን ፡ ሰምታችኋል ። እኔ ፡ ግን ፡ እላችኋለሁ ። ጠላታችሁን ፡ ውደዱ ። የሚረግሙአችሁንም ፡ መርቋቸው ። ለሚጠሉአችሁም መልካም ፡ አድርጉ ። ለሚቀሙአችሁና ፡ ለሚያባርሯችሁ ፡ ለሚያሳዝኑአችሁም ፡ ጸልዩ ። ለሰማያት ፡ አባታችሁ ፡ ልጆቹ ፡ ትሆኑ ፡ ዘንድ፡ እርሱ ፡ ለደጎችና ፡ ለክፉዎች ፡ ፀሐይን ፡ ያወጣልና ። ዝናምንም ፡ ለጻድቃንና ፡ ለዓመፀኞች ፡ ያዘንማልና ። ሰማያዊ ፡ አባታችሁ ፡ ፍጹም ፡ እንደሆነ እናንተም ፡ ፍጹማን ፡ ሁኑ ።

፩ሺ፮፻፱ ያዩላችሁ ፡ ዘንድ ፡ ጽድቃችሁን ፡ በሰዎች ፡ ፊት ፡ እንዳታደርጉ ፡ እዩ ። ያለዚያስ ፡ በሰማያት ፡ ዋጋ ፡ የላችሁም ፡ በምትጸልዩበትም ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ግብዞች ፡ አትሁኑ ። እነርሱ ፡ ዋጋቸውን እንደ ፡ ወሰዱ ፡ ዋጋቸውንም ፡ እንደጨረሱ ፡ እውነት ፡ እላችኋለሁ ። በምትጾሙም ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ግብዞች ፡ ፊታችሁን ፡ አትቋጥሩ ።

፩ሺ፮፻፲ በሰማያት ፡ እንጂ ፡ በምድር ፡ ለእናንተ ፡ ድልብን ፡ አታድልቡ ። ድልባችሁ ፡ ካለበት ፡ ዘንድ ከዚያ ፡ ልባችሁ ፡ ይኖራል ። አንድ ፡ ባሪያ ፡ ለሁለት ፡ ጌቶች ፡ መገዛት ፡ አይችልም ። ለእግዚአብሔርና ለገንዘብ ፡ መገዛት ፡ አትችሉም ። አስቀድማችሁ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥትና ፡ ጽድቁን ፡ ሹ ። (ፈልጉ) ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ ግን ፡ ይጨመርላችኋል ። ለነገ ፡ አታስቡ ። ነገ ፡ ለራሱዋ ፡ ታስባለችና ፡ ለዕለትም ፡ ክፋቷ ፡ ይበቃታል ።

፩ሺ፮፻፲፩ እንዳይፈረድባችሁ ፡ አትፍረዱ ። አስቀድመህ ፡ ከዓይንህ ፡ ጉድፍን ፡ አውጣ ። ያን ፡ ጊዜ ፡ በባልንጀራህ ፡ ዓይን ፡ ያለውን ፡ ጉድፍ ፡ ለማውጣት ፡ ታያለህ ። የተቀደሰውን ፡ ለውሾች ፡ አትስጡ ። ለምኑ ፡ ይሰጣችኋልም ። ሹ ፡ (ፈልጉ) ፡ ታገኙማላችሁ ። ደጅ ፡ ምቱ ፡ ይከፈትላችኋልም ። ሰዎች ፡ ሊያደርጉላችሁ ፡ እንደምትወዱ ፡ እናንተም ፡ አድርጉላቸው ። ኦሪትም ፡ ነቢያትም ፡ እንደዚሁ ፡ ነውና ። ወደ ፡ ሕይወት ፡ በምትወስደው ፡ በጠባብ ፡ በር ፡ ግቡ ። ለመሄድ ፡ ሰፊ ፡ ናትና ። ወደጥፋት ፡ የምትወስደው ፡ መንገድ ፡ ግን ፡ ሰፊ ፡ ናት ። የበግ ፡ ልብሰን ፡ ለብሰው ፡ ወደ ፡ እናንተ ፡ ከሚመጡ ፡ ከሐሰተኞች ፡ ነቢያት ፡ ተጠበቁ ። በውስጣቸው ፡

እባግዕ ፡ ወእንተ ፡ ውስጠሙሰ ፡ ተኵላት ፡ መሠጥ ፡ ወእምፍሬሆሙ ፡ ታአምርዎሙ ።

፩ሺ፯፻፲፪ እኮ ፡ ኵሉ ፡ ዘይብለኒ ፡ እግዚኦ ፡ እግዚኦ ፡ ዘይበውእ ፡ ውስተ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ አላ ፡ ዘይገብር ፡ ፈቃዶ ፡ ለአቡየ ፡ ዘበሰማያት ። እብለክሙ ፡ ከመ ፡ ኵሉ ፡ ቃል ፡ ዘይነብብ ፡ ቦቱ ፡ ሰብእ ፡ ዕሩዐ ፡ ያገብእዎ ፡ ቃለ ፡ ተሠጥዎ ፡ በእንቲአሁ ፡ በዕለተ ፡ ደይን ። መኵሉ ፡ ዘይገብር ፡ ሥምረቶ ፡ ለአቡየ ፡ ዘበሰማያት ፡ ውእቱ ፡ እኁየ ፡ ወእኅትየ ፡ ወእምየ ። ኢይብለክ ፡ እስከ ፡ ፯ቱ ፡ ጊዜያት ፡ ሥረይ ፡ ለእኁከ ፡ አላ ፡ ሰብዓ ፡ ጊዜያተ ፡ በበስብዕ ። ዘይፈቅድ ፡ ይኩን ፡ ዐቢየ ፡ በውስቴትክሙ ፡ ይኩን ፡ ላእከ ፡ ወዘይፈቅድ ፡ እምኔክሙ ፡ ይኩን ፡ ሊቀ ፡ ይኩንክሙ ፡ ገብረ ። አማን ፡ እብለክሙ ፡ እመ ፡ ኢተመየጥክሙ ፡ ወኢኮንክሙ ፡ ከመዝ ፡ ሕፃን ፡ ኢትበውእዋ ፡ ለመንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ ወዘሂ ፡ ተትሕተ ፡ ከመ ፡ ዝንቱ ፡ ሕፃን ፡ ዐቢይ ፡ ውእቱ ፡ በመንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ አማን ፡ እብለክሙ ፡ ለእመ ፡ ብክሙ ፡ ሃይማኖት ፡ ወኢናፈቅሙ ፡ ሶበ ፡ ትቤልዎ ፡ ለዝንቱ ፡ ደብር ፡ ፍልስ ፡ ውስተ ፡ ባሕር ፡ ይከውን ፡ በከመ ፡ ነበብክሙ ። ወለኵሉ ፡ ዘትስእልዎ ፡ በጸሎት ፡ ወበሃይማኖት ፡ ትረክብዎ ።"

፩ሺ፯፻፲፫ ማርቆስ ፡ ዘ፲ወ፪ቱ ፡ "ወእሉ ፡ እሙንቱ ፡ እለ ፡ ውስተ ፡ ሦክ ፡ ተዘርኡ ፡ እሙንቱ ፡ እለ ፡ ይሰምዑ ፡ ቃለ ፡ ወይመውዖሙ ፡ ጻሕቀ ፡ ዝንቱ ፡ ዓለም ፡ ወብዕል ፡ ሰፋቢት ፡ ወኵሉ ፡ ፍትወታት ፡ እንተ ፡ ባቲ ፡ የሐውሩ ፡ ወየሐንቅዎ ፡ ለቃል ፡ ወኢይፈሪ ፡ በላዕሌሆሙ ። አልቦ ፡ ኅቡእ ፡ ዘኢይትከሠት ፡ ወአልቦ ፡ ክቡት ፡ ዘኢያስተርኢ ።"

፩ሺ፯፻፲፬ ሉቃስ ፡ ዘ፲ወ፰ቱ ፡ "አሌ ፡ ለክሙ ፡ አብዕልት እስመ ፡ ሠለጥክሙ ፡ ዓስበክሙ ። አሌ ፡ ለክሙ እለ ፡ ትጸግቡ ፡ ይእዜ ፡ እስመ ፡ ተርኅቡ ። አሌ ፡ ለክሙ ፡ እለ ፡ ትስሕቁ ፡ ይእዜ ፡ እስመ ፡ እንትሙ ፡ ትበክዩ ፡ ወትኄዝኑ ። አሌ ፡ ለክሙ ፡ ሶበ ፡ ይብሉ ፡ ኵሉ ፡ ሰብእ ፡ ቃለ ፡ ሠናየ ፡ ላዕሌክሙ ፡ እስመ ፡ ከማሁ ፡ ረሰይዎሙ ለአበዊክሙ ፡ ነቢያት ፡ ሐሳውያን ።

፩ሺ፯፻፲፭ ዘ፴ወ፰ቱ ፡ ኢትትፌሥሑ ፡ በዝ ፡ እስመ ፡ አጋንንት ፡ ይገንዩ ፡ ለክሙ ፡ ተፈሥሑስ ፡ እስመ ፡



ማን ፡ ነጣቂዎች ፡ ተኵላዎች ፡ ናቸው ። ከፍሬያቸውም ፡ የተነሣ ፡ ስወቋቸው ።

፩ሺ፯፻፲፪ አቤቱ ፡ አቤቱ ፡ የሚለኝ ፡ ሁሉ ፡ ወደ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ የሚገባ ፡ አይደለም ። በሰማያት ፡ ያለ ፡ የአባቴን ፡ ፈቃድ ፡ የሚፈጽም ፡ ነው ፡ እንጂ ። (ማቴ ፡ ፯ - ፳) ። ሰው ፡ በዋዘኛነት ፡ በሚናገረው ፡ ቃል ፡ ሁሉ ፡ በፍርድ ፡ ቀን ፡ ስለእርሱ ፡ የመልስ ፡ ቃል ፡ እንዲመልስለት ፡ እነግራችኋለሁ ። በሰማያት ፡ ያለ ፡ የአባቴን ፡ ፈቃድ ፡ የሚያደርግ ፡ ሁሉ ፡ ወንድሜ ፡ እኅቴም ፡ እናቴም ፡ እርሱ ፡ ነው ። (ማቴ ፡ ፲፪ ፡ ፴፮ ። ፵፱ - ፶) ። ለወንድምህ ፡ እስከ ፯ ፡ ጊዜ ፡ ይቅር ፡ በል ፡ አልልህም ። በየሰባቱ ፡ ፸ ፡ ጊዜ ፡ ነው ፡ እንጂ ። (ማቴ ፡ ፲፰ ፡ ፳፩ - ፳፪) ። በእናንተ ፡ ውስጥ ፡ ታላቅ ፡ ሊሆን ፡ የሚወድ ፡ አገልጋይ ፡ ይሁን ። ከእናንተም ፡ አለቃ ፡ ሊሆን ፡ የሚወድ ፡ ባሪያ ፡ ይሁናችሁ ። እውነት ፡ እላችኋለሁ ፡ ተመልሳችሁ ፡ እንደዚህ ፡ ሕፃን ፡ካልሆናችሁ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያትን ፡ አትገቡእትም ። (ማር ፡ ፱ ፡ ፴፫ - ፴፯) ። እውነት ፡ እላችኋለሁ ። ሃይማኖት ፡ ካላችሁ ፡ ካልተጠራጠራችሁም ፡ ይህን ፡ ተራራ ፡ ወደ ባሕር ፡ ፍለስ ፡ ብትሉት ፡ እንደ ተናገራችሁ ፡ ይሆናል ። በጸሎትና ፡ በሃይማኖት ፡ የምትለምኑትን ፡ ሁሉ ፡ ታገኙታላችሁ ። (ማቴ ፡ ፳፩ ፡ ፳፩ - ፳፪) ።

፩ሺ፯፻፲፫ ማርቆስ ፡ ፲፪ ። በእሾህ ፡ ውስጥ ፡ የተዘሩ ፡ እሊህ ፡ ናቸው ። ትምህርትን ፡ ሰምተው ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡ አሳብ ፡ አታላዩት ፡ ብዕልም ፡ የሚኖሩባት ፡ ምኞትም ፡ (ፍትወትም) ፡ ሁሉ ፡ ድል ፡ የሚነሣቸው ፡ ናቸው ። ትምህርቱንም ፡ ያንቁታል ። በላያቸውም ፡ አያፈራም ። (ማር ፡ ፬ ፡ ፲፰ - ፳) ። የማይገለጽ ፡ ስውር ፡ የለም ። የማይታይም ፡ ሽሽግ ፡ የለም ። (ሉቃ ፡ ፲፪ ፡ ፪ )።

፩ሺ፯፻፲፬ ሉቃስ ፡ ፲፰ ። ባለጸጎች ፡ ወዮላችሁ ። ዋጋችሁን ፡ ጨርሳችኋልና ። ዛሬ ፡ የምትጠግቡ ፡ ወዮላችሁ ። እናንተ ፡ ትራባላችሁና ። ዛሬ ፡ የምትስቁ ፡ ወዮላችሁ ። እናንተ ፡ ታለቅሳላችሁና ። ታዝኑማላችሁ ። ሰዎች ፡ በእናንተ ፡ ላይ ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ ባወሩ ፡ ጊዜ ፡ ወዮላችሁ ። ሐሰተኞች ፡ ነቢያት ፡ አባቶቻችሁን ፡ እንደዚሁ አድርገዋቸዋልና ። (ሉቃ ፡ ፮ ፡ ፳፬ - ፳፮) ።

፩ሺ፯፻፲፭ ፴፰ ። በዚህ ፡ ደስ ፡ አይበላችሁ ። አጋንንት ፡ ይገዙላችኋልና ። ነገር ፡ ግን ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፡

አንቀጽ ፡ ፵፰ ።

ተጽሕፈ ፡ እስማተከሙ ፡ በሰማያት ።

፩ሺ፮፻፲፮ ዘ፶ወ፬ቱ ፡ ወሶበ ፡ ይጼውዑከ ፡ ውስተ ፡ ምሳሕ ፡ ሐር ፡ ወርፍቅ ፡ ውስተ ፡ ዘይቴሐት ፡ ምርፋቅ ፡ እስመ ፡ ዘቦሉ ፡ ዘአልዐለ ፡ ርእሶ ፡ የኀሥር ፡ ወዘአትሐተ ፡ ርእሶ ፡ ይከብር ። ወሶበ ፡ ትገብር ፡ በዓለ ፡ አው ፡ ምሳሐ ፡ ኢትጸውዕ ፡ አዕርክቲከ ፡ ወአኃዊከ ፡ ወማኅፈረከ ፡ ወአዝማዲከ ፡ ወአግዋረከ ፡ አብዕልተ ፡ ከመ ፡ ለእመ ፡ ቦ ፡ ሶበ ፡ ይጼውዑከ ፡ እሙንቱኒ ፡ ካዕበ ፡ ይከውነከ ፡ ፍዳ ፡ በኀቤሆሙ ። ወባሕቱ ፡ ሶበ ፡ ትገብር ፡ በዓለከ ፡ ጸውዕ ፡ ነዳያነ ፡ ወጽኑሳነ ፡ ወመፃጕዓነ ፡ ወዕዉራነ ፡ ወብፁዕ ፡ አንተ ፡ እስመ ፡ አልቦሙ ፡ ዘይፈድዩከ ፡ ወትትዐሠይ ፡ ባሕቱ ፡ አመ ፡ ትንሣኤ ፡ ጻድቃን ።”

፩ሺ፮፻፲፯ ዮሐንስ ፡ ዘ፫ቱ ፡ ዘኢተወልደ ፡ አማይ ፡ ወእመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ኢይክል ፡ በዊአ ፡ ውስተ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ። ወአንትሙሰ ፡ ትብሉኒ ፡ ሊቅነ ፡ ወእግዚእነ ፡ ወሠናየ ፡ ትቤሉ ፡ እስመ ፡ ከማሁ ፡ አነ ፡ ሊቅክሙ ፡ ወእግዚእክሙ ፡ ወእመሰ ፡ አነ ፡ ሊቅክሙ ፡ ወእግዚእክሙ ፡ ነዋ ፡ ሐፀብኩ ፡ እገሪክሙ ፡ ወከማሁ ፡ አንትሙኒ ፡ ይደልወክሙ ፡ ትሕፅቡ ፡ እግረ ፡ ቢጽክሙ ፡ እስመ ፡ አርአያየ ፡ ወሀብኩክሙ ።” ዘሮሜ ፡ ፲ ወ፫ቱ ፡ “ብፁዕ ፡ ብእሲ ፡ ዘኩነና ፡ ለነፍሱ ፡ በዘተውህቦ ፡ አእምሮ ።”

፩ሺ፮፻፲፰ ዘቆሮንቶስ ፡ ፩ቱ ፡ ወለእመቦ ፡ ዘይሰመይ ፡ እምኔክሙ ፡ እኁወ ፡ ወኮነ ፡ ዘማዌ ፡ አው ፡ ተዓጋሤ ፡ አው ፡ መምለኬ ፡ ጣዖት ፡ አው ፡ ጸአሌ ፡ አው ፡ ሰካሬ ፡ አው ፡ ሀያዴ ፡ ኢትትሐወልዎ ፡ በመብልዕ ።

፩ሺ፮፻፲፱ ዘ፮ቱ ፡ ወለምንትኑ ፡ ኢትትገፍዑ ፡ ወለምንትኑ ፡ ኢትትሀየዱ ፡ ወባሕቱ ፡ አንትሙ ፡ ትገፍዑ ፡ ወተሀይዱ ፡ ካዕበ ፡ አኃዊክሙ ፡ ኢተአምሩኑ ፡ ከመ ፡ ዐማፅያን ፡ ኢይወርስዋ ፡ ለመንግሥተ ፡ እግዚአብሔር ። ኢያስሕቱክሙ ፡ ኢዘማውያን ፡ ወኢ ፡ እለ ፡ ያመልኩ ፡ ጣዖተ ፡ ወኢ ፡ እለ ፡ የሐውሩምሙ ፡ ወኢ ፡ እለ ፡ የሐውሩ ፡ ተባዕተ ፡ ወኢ ፡ ተዓጋልያን ፡ ወኢ ፡ ሰረ

ስለ ፡ ብሉይና ፡ ሐዲስ ።

ስማችሁ ፡ በሰማይ ፡ ተጽፏልና ። (ሉቃ ፡ ፲ ፡ ፳) ።

፩ሺ፮፻፲፮ ፶፬ ። ወደምሳ ፡ በጠሩህም ፡ ጊዜ ፡ ሂደህ ፡ ከዝቅተኛ ፡ መቀመጫ ፡ ተቀመጥ ። ራሱን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያደረገ ፡ ሁሉ ፡ ይዋረዳልና ። ራሱንም ፡ ዝቅ ፡ ዝቅ ፡ ያደረገ ፡ ይከብራልና ። በዐል ፡ ወይም ፡ ግብዣ ፡ በአደረግህ ፡ ጊዜ ፡ ወዳጆችህንና ፡ ወንድሞችህን ፡ አማቾችህንም ፡ ዘመዶችህንና ፡ ጎረቤቶችህን ፡ ባለጸጎችንም ፡ አትጥራ ። ምናልባት ፡ እነርሱም ፡ በጠሩህ ፡ ጊዜ ፡ በእነርሱም ፡ ዘንድ ፡ ደግሞ ፡ ብድራት ፡ ይሆንሃል ። ነገር ፡ ግን ፡ በዓል ፡ በምታደርግበት ፡ ጊዜ ፡ ድኆችንና ፡ ችግረኞችን ፡ ጎባጦችን ፡ ዕውሮችንም ፡ ጥራ ። ብፁዕም ፡ ትሆናለህ ። የሚከፍሉት ፡ የላቸውምና ። በጻድቃን ፡ ትንሣኤ ፡ ጊዜ ፡ ዋጋህን ፡ ታገኛለህ ፡ እንጂ ። (ሉቃ ፲፬ ፡ ፲፪ - ፲፭) ።

፩ሺ፮፻፲፯ ዮሐንስ ፡ ፫ ። ከውሀና ፡ ከመንፈስ ፡ ያልተወለደ ፡ ወደ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ መግባት ፡ አይችልም ። (ዮሐ ፡ ፫ ፡ ፭)። እናንተስ ፡ አለቃችንና ፡ ጌታችን ፡ ትሉኛላችሁ ። መልካምም ፡ ትላላችሁ ። እንደዚሁ ፡ እኔ ፡ አለቃችሁና ፡ ጌታችሁ ፡ ነኝና ። እነሆ ፡ እግራችሁን ፡ አጠብሁ ። እንደዚሁም ፡ እናንተ ፡ የባልንጀራችሁን ፡ እግር ፡ ልታጥቡ ፡ ይገባችኋል ። ምሳሌዬን ፡ ሰጥቻችኋለሁና ። (ዮሐ ፡ ፲፫ ፡ ፲፫ - ፲፮) ። ሮሜ ፡ ፲፫ ። በተሰጠው ፡ አእምሮ ፡ ሰውነቱን ፡ የቀጣት ፡ ሰው ፡ ብፁዕ ፡ ነው ። (ሮሜ ፡ ፲፬ ፡ ፳፪) ።

፩ሺ፮፻፲፰ ቆሮንቶስ ፡ ፩ ። ከእናንተ ፡ ወገን ፡ ወንድም ፡ የሚባል ፡ ቢኖር ፡ ዘማዊ ፡ ወይም ፡ ቀማኛ ፡ ወይም ፡ ጣዖት ፡ የሚያመልክ ፡ ወይም ፡ ተሳዳቢ ፡ ወይም ፡ ሰካራም ፡ ወይም ፡ ነጣቂ ፡ ቢሆን ፡ በመብል ፡ ጊዜ ፡ አትቀላቀሉት ። (፩ ቆሮ ፡ ፭ ፡ ፲፩ - ፲፪) ።

፩ሺ፮፻፲፱ ፮ ። ለምን ፡ አትገፉም ? ለምንስ ፡ አትቀሙም ? ነገር ፡ ግን ፡ እናንተ ፡ ትገፉላችሁ ። (ትበድላላችሁ) ፡ ዳግመኛም ፡ ወንድሞቻችሁን ፡ ትቀማላችሁ ። ዓመፀኞች ፡ መንግሥተ ፡ ማያትን ፡ እንደማይወርሱአት ፡ አታውቁምን ? ዘማውያን ፡ ቢሆኑ ፡ ጣዖት ፡ የሚያመልኩም ፡ የሚሄዱባቸውም ፡ ወይም ፡ ወደ ፡ ወንድ የሚሄዱ ፡ ወይም ፡ ቀማኞች ፡ ወይም ፡ ሌቦች ፡

ቅት ፡ ወኢ ፡ ሰካርያን ፡ ወኢ ፡ ጸአልያን ፡ ወኢ ሀያድያን ፡ እሉ ፡ ኵሎሙ ፡ ኢይወርስዋ ፡ ለመን ግሥት ፡ እግዚአብሔር ።

፩ሺ፩፻፳ ዘ፲ወ፪ቱ ፡ ቅንኡ ፡ ለእንተ ፡ ተዐቢ ፡ ጸጋ ፡ አንሰ ፡ አርእየክሙ ፡ ካዕበ ፡ ፍኖተ ፡ ካልአ ፡ ዘይኄይስ ፡ ፈድፋደ ። ወእመኒ ፡ ነበብኩ ፡ በልሳነ ፡ ኵሉ ፡ ሰብእ ፡ ወነገረ ፡ መላእክት ፡ ወእመኒ ፡ ተነበይኩ ፡ ወአእመርኩ ፡ ኵሎ ፡ ዘኅቡእ ፡ ወነተሎ ፡ ዘተበብ ፡ ወእመኒ ፡ ብየ ፡ ሃይ ማኖት ፡ እስከ ፡ አፈልስ ፡ አድባረ ፡ ወእመኒ ፡ አብላዕኩ ፡ ለነዳያን ፡ ኵሎ ፡ ዘብየ ፡ ወዓዲ ፡ ሥጋየኒ ፡ ለውዕየተ ፡ እሳት ፡ ወተፋቅሮ ፡ አል ብየ ፡ አልቦ ፡ ዘረባኅኩ ። እስመ ፡ ዘቦቱ ፡ ተፋ ቅሮ ፡ ርኁፉ ፡ መንፈሱ ፡ ውእቱ ፡ ውናየ ፡ ተላጽቆ ፡ ኢይቀንእ ፡ ወኢይትሀወክ ፡ ኢይትዔ በይ ፡ ወኢያመጽእ ፡ ዘያስተኃፍር ፡ ወኢየኀ ሥሥ ፡ ተድላ ፡ ለባሕቲቱ ፡ ኢይትመዐዕ ፡ ወኢያሔሊ ፡ እኩየ ፡ ኢይትፌሣሕ ፡ በግፍዕ ፡ ወይትፌሣሕ ፡ በጽድቅ ፡ ይትዔገሥ ፡ በኵሉ ፡ ወበኵሉ ፡ ወየአምን ። ወይትዌከል ፡ በኵሉ ፡ ወይፀመድ ፡ በኵሉ ፡ ወእሉ ፡ እሙንቱ ፡ ፫ቱ ፡ እለ ፡ ይነብሩ ፡ ሃይማኖት ፡ ወተስፋ ፡ ወተፋ ቅሮ ፡ ወእምነ ፡ ኵሎሙ ፡ የዐቢ ፡ ተፋቅሮ ።

፩ሺ፩፻፳፩ ዘ፲ወ፫ቱ ፡ ወባሕቱ ፡ ኩኑ ፡ ከመ ፡ ሕፃናት ፡ ለገቢረ ፡ እከይ ፡ ወፍጹማነ ፡ በምክርክሙ ።

፩ሺ፩፻፳፪ ዘቆሮንቶስ ፡ ፫ቱ ፡ እስመ ፡ ዘለወነ ፡ ለኵልነ ፡ ከመ ፡ ንቁም ፡ ቅድመ ፡ መንበሩ ፡ ለክርስቶስ ፡ ወይፈድዮ ፡ ለለ፩ዱ ፡ እምኔነ ፡ በከመ ፡ ምግ ባሩ ፡ ዘገብረ ፡ በሥጋሁ ፡ እመኒ ፡ ሠናየ ፡ ወእ መኒ ፡ እኩየ ።

፩ሺ፩፻፳፫ ዘ፬ቱ ፡ ዑቁ ፡ ኢትረስዩ ፡ ምክንያተ ፡ ዕቅፍት ፡ ለመኑሂ ፡ ከመ ፡ ኢይባእ ፡ ነውር ፡ ውስተ ፡ መልእክትነ ። ወባሕቱ ፡ ናግዕድ ፡ ለሊነ ፡ በኵሉ ፡ ግብር ፡ ከመ ፡ ላእካነ ፡ እግዚአብሔር ፡ ንሕነ ፡ በዐቢይ ፡ ትዕግሥት ፡ ውስተ ፡ ፃዕር ፡ ወምንዳቤያት ፡ በሕማም ፡ ወበተቀሥፎ ፡ በተ ሞቅሖ ፡ ወበስደት ፡ በጻማ ፡ ወበትጋሀ ፡ በጾም ፡ ወበንጽሕና ፡ በአእምሮ ፡ ወበአንብሮ ፡ መንፈስ ፡ በተፋቅሮ ፡ ወበተራኅርኆ ፡ በእንግዳ ፡ መን ፈስ ፡ ወበተፋቅሮ ፡ ዘእንበለ ፡ አድልዎ ፡ በነገረ ጽድቅ ፡ ወበኀይለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወበንዋየ ፡

ወይም ፡ ሰካራሞች ፡ ወይም ፡ ተሳዳቢዎች ፡ ወይም ፡ ነጣቂዎች ፡ አያስቷችሁ ። እሊህ ፡ ሁሉ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ መንግሥት ፡ አይወር ሱአትም ። (፩ ቆሮ ፡ ፮ ፡ ፯ - ፲፯) ።

፩ሺ፩፻፳ ፲፪ ። ስምትበልጠው ፡ ጸጋ ፡ ቅኑ ። እኔም ፡ ዳግ መኛ ፡ እጅግ ፡ የበለጠ ፡ ሌላ ፡ ጎዳና ፡ አሳያችኋ ለሁ ፡ በሰዎች ፡ ሁሉ ፡ ቋንቋና ፡ በመላእክት ፡ ቋንቋ ፡ ብናገር ፡ ትንቢትም ፡ ብናገር ፡ የተሰወረ ውን ፡ ሁሉና ፡ የጥበብን ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ባውቅ ፡ ተራራም ፡ እስከእፈልስ ፡ ድረስ ፡ ሃይማኖት ፡ ቢኖረኝ ፡ ያለኝንም ፡ ሁሉ ፡ ለድሆች ፡ ባበላ ፡ ዳግመኛም ፡ ሥጋዬን ፡ ለእሳት ፡ ቃጠሎ ፡ ብሰጥ ፡ ፍቅር ፡ ከሌለኝ ፡ የተጠቀምሁት ፡ የለም ። ፍቅር ፡ ያለው ፡ ሰው ፡ ርኁሩኅ ፡ ትዕግ ሥተኛም ፡ ነውና ። በፍቅር ፡ መልካም ፡ የሆነ ፡ (ፍጹም ፡ የሆነ) ፡ አይቀናም ። ቸልም ፡ አይልም አይታበይምም ። የሚያሳፍርም ፡ ነገር ፡ አያመ ጣም ። ለብቻውም ፡ ተድላን ፡ አይሻም ። አይበ ሳጭም ። ክፉም ፡ አያስብም ። በግፍዕ ፡ ደስ ፡ አይለውም ። በእውነት ፡ ግን ፡ ደስ ፡ ይለዋል ። በሁሉ ፡ ይታገሣል ። በሁሉም ፡ ይታመናል ። ጸንተውም ፡ የሚኖሩ ፡ ሃይማኖት ፡ ተስፋ ፡ ፍቅር ፡ ናቸው ። ከሁሉም ፡ ፍቅር ፡ ይበልጣል። (፩ ቆሮ ፡ ፲፪ ፡ ፴፩ ። ፲፫ ፡ ፩ - ፲፫) ።

፩ሺ፩፻፳፩ ፲፫ ። ነገር ፡ ግን ፡ ክፉ ፡ ለመሥራት ፡ እንደ ፡ ሕፃናት ፡ ሁኑ ። በምክራችሁ ፡ ግን ፡ ፍጹማን ፡ ሁኑ ። (፩ ፡ ቆሮ ፡ ፲፬ ፡ ፳) ።

፩ሺ፩፻፳፪ ቆሮንቶስ ፡ ፫ ። ሁላችንም ፡ በክርስቶስ ፡ ዙፋን ፡ ፊት ፡ እንቆም ፡ ዘንድ ፡ አለብን ። ከእ ኛም ፡ ለእያንዳንዱ ፡ መልካምም ፡ ቢሆን ፡ ክፉም ፡ ቢሆን ፡ በሥጋው ፡ እንደ ፡ ሠራው ፡ ሥራ ፡ ይከ ፍለዋል ። (፪ ቆሮ ፡ ፭ ፡ ፲) ።

፩ሺ፩፻፳፫ ፬ ። ለማንም ፡ የዕንቅፋት ፡ ምክንያት ፡ እንዳ ታደርጉ ፡ ዕወቁ ። በመልእክታችን ፡ ነውር ፡ እንዳይገባ ። ነገር ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔር ፡ አገ ልጋዮች ፡ እንደመሆናችን ፡ ሥራን ፡ ሁሉ ፡ ራሳ ችን ፡ እንግለጥ ፡ እንጂ ። በጭንቅና ፡ በችግር ፡ ውስጥ ፡ በታላቅ ፡ ትዕግሥት ፡ በመታመም ፡ በመገረፍ ፡ በመታሰር ፡ በመሰደድ ፡ በድካም ፡ በትጋት ፡ በጾም ፡ በንጽሕና ፡ በዕውቀት ፡ መን ፈስን ፡ በማሰረዘም ፡ በፍቅር ፡ በመራራት ፡ ልበናን ፡ ንጹሕ ፡ በማድረግ ፡ ያለማድላት ፡ በመፋቀር ፡ በእውነተኛ ፡ ነገር ፡ በእግዚአብ

ሐቅል ፡ ዘጽድቅ ፡ ዘእምየማን ፡ ወእምጺጋም ፡ በክብር ፡ ወበኀሣር ፡ በበረከት ፡ ወበመርገም ።”

፩ሺ፯፻፳፬ ዘገላትያ ፡ ወዑሩ ፡ በበይናቲክሙ ፡ ክበደ ፡ ቢጽክሙ ፡ ወነሥሉ ፡ ብእሲ ፡ እምኔክሙ ፡ ያመክር ፡ ምግባሮ ፡ ወኢትስሐቱ ፡ እልቦ ፡ ዘያስተዓብዮ ፡ ለእግዚአብሔር ። ወዘዘርአ ፡ ሰብእ ፡ የአርር ፡ ወዘዘርአ ፡ ምግባራተ ፡ ሥጋ ፡ የዐርር ፡ እምውስቴቱ ፡ ሙስና ። ወዘይዘርእ ፡ ምግባራተ ፡ መንፈስ ፡ በመንፈስ ፡ የአርር ፡ ሕይወተ ፡ ዘለዓለም ። ወእምከመ ፡ ገበርነ ፡ ሠናያተ ፡ ኢንትሀከይ ፡ እስመ ፡ በለወነ ፡ በጊዜሁ ፡ ንአርር ፡ እምግባነ ፡ ብነ ፡ ዕለት ፡ ንግበር ፡ ሠናየ ፡ ለኵሉ ፡ ወኢንትሀከይ ፡ እንከ ።

፩ሺ፯፻፳፭ ዘኤፌሶን ፡ ፫፡ ፡ አስተበቍዐክሙ ፡ ከመ ፡ ትሑሩ ፡ በበይደሉ ፡ ለጸዋዔክሙ ፡ እንተ ፡ ተጸዋዕክሙ ፡ እንዘ ፡ ታቴሕቱ ፡ ርእሰክሙ ፡ በኵሉ ፡ ጸሕቅ ፡ ወትዕግሥት ፡ ወየውሃት ። ወኩኑ ፡ እንዘ ፡ ትትዔገሡ ፡ በበይናቲክሙ ፡ በፍቅር ፡ ወትጽሕቁ ፡ ለዐቂበ ፡ ተስናእዎ ፡ በመንፈስ ፡ ወበማእሰረ ፡ ሰላም ፡ ከመ ፡ ትኩኑ ፡ ፩ደ ፡ ሥጋ ፡ ወ፩ደ ፡ መንፈስ ።

፩ሺ፯፻፳፯ ዘ፬ቱ ፡ ወዘእንበለ ፡ ይዕርብ ፡ ፀሐይ ፡ አቍርሩ ፡ መዓተክሙ ፡ ወኢተሀብዎ ፡ ፍኖተ ፡ ለሰይጣን ፡ ለአስሕቶትክሙ ። ዘይሰርቅኒ ፡ ኢይሰርቅ ፡ እንከ ፡ አላ ፡ ለይትገበር ፡ ወይጻሙ ፡ በእደዊሁ ፡ ለገቢረ ፡ ሠናይ ፡ በዘይረድኦ ፡ ለጽኑስ ። ወነሥሉ ፡ ነገር ፡ ሕሡም ፡ ኢይፃእ ፡ እምአፉክሙ ፡ ዘእንበለ ፡ ሠናይ ፡ በዘይትሐነጽ ፡ ትትካዘክሙ ፡ ወኵሎ ፡ መሪረ ፡ ወቁመ ፡ ወቍጥዓ ፡ ወከላሐ ፡ ወፅርፈተ ፡ አእትቱ ፡ እምላዕሌክሙ ፡ ምስለ ፡ ኵሉ ፡ እከይ ። ወኩኑ ፡ መሐርያነ ፡ ቢጽክሙ ፡ ወመሐሩ ፡ በከመ ፡ መሐረክሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ ክርስቶስ ፡ ወተመሰሉ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ከመ ፡ ውሉድ ፡ ፍቁራን ። ወዝሙትሰ ፡ ወኵሉ ፡ ርኵስ ፡ ወሀመዛ ፡ ኢይሰማዕ ፡ በላዕሌክሙ ፡ በከመ ፡ ኢይደልዎሙ ፡ ለቅዱሳን ፡ ነገረ ፡ ኀፍረት ፡ ወነገረ ፡ ዕበድ ፡ ወነገረ ፡ ስላቅ ፡ ወተላህዮ ፡ ለሣቂ ፡ ክብር ፡ እንተ ፡ ኢትደሉ ፡ ኢትቅረብዋ ።

ዘፊልጵስዩስ ፡ ወፈጽሙ ፡ ከዊነ ፡ ፍሥሓየ ፡ ከመ ፡ ተሀልዉ ፡ በ፩ዱ ፡ ምክር ፡ ወበ፩ዱ ፡ ፍቅር ፡ ወአሐቲ ፡ ነፍስ ፡ ወኢትግበሩ ፡ በምንትኒ ፡ ተኃ



ሐር ፡ ኃይል ፡ ከተቀኘና ፡ ከግራ ፡ በሚሆን ፡ በእውነት ፡ የጦር ፡ ዕቃ ፡ በክብር ፡ በመዋረድ ፡ በምርቃት ፡ በርግማንም ። (፪ ፡ ቆሮ ፡ ፮ ፡ ፫ - ፲)።

፩ሺ፯፻፳፬ ገላትያ ። እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ የባልንጀራችሁን ፡ ሸክም ፡ ተሸከሙ ። ከእናንተ ፡ ወገን ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ሥራውን ፡ ይመርምር ። አትሳቱም ። እግዚአብሔርንም ፡ የሚያለንፈው ፡ እዮኑር ። ሰው ፡ የዘራውን ፡ ይለቅማል ። የሥጋ ፡ ሥራዎችን ፡ የሚዘራም ፡ ከውስጡ ፡ ጥፋትን ፡ ይለቅማል ። የመንፈስ ፡ ሥራዎችንም ፡ የሚዘራ ፡ በመንፈስ ፡ የዘለዓለም ፡ ሕይወትን ፡ ይለቅማል ። መልካም ፡ ብንሠራም ፡ አንሰንፍ ። በጊዜው ፡ እንለቅመዋለንና ። ቀን ፡ ሳለልን ፡ ለሁሉ ፡ መልካም ፡ እንሥራ ። እንግዲህ ፡ አንሰንፍ ። (ገላ ፡ ፮ ፡ ፩ - ፲) ።

፩ሺ፯፻፳፭ ኤፌሶን ፡ ፫ ። ለተጠራችሁባት ፡ አጠራር ፡ በሚገባ ፡ በፍጹም ፡ ትኅትና ፡ በትዕግሥት ፡ በገርነትም ፡ ራሳችሁን ፡ ዝቅ ፡ ዝቅ ፡ አድርጋችሁ ፡ ትኖሩ ፡ ዘንድ ፡ እማልዳችኋለሁ ። እርስ ፡ በርሳችሁ ፡ በፍቅር ፡ እየታገሣችሁ ፡ በመንፈስም ፡ ስምምነት ፡ ለመጠበቅ ፡ እየተጋችሁ ፡ በስላምም ፡ ማሰሪያ ፡ ኑሩ ፡ አንድ ፡ ሥጋና ፡ አንድ ፡ ነፍስ ፡ ትሆኑ ፡ ዘንድ ። (ኤፌ ፡ ፬ ፡ ፩ - ፫) ።

፩ሺ፯፻፳፮ ፬ ። ፀሐይም ፡ ሳይገባ ፡ ቁጣችሁን ፡ አብርዱ ። ለሰይጣንም ፡ እናንተን ፡ ለማሳት ፡ መንገድ ፡ አትስጡት ። የሚሰርቅም ፡ እንግዲህ ፡ አይስረቅ ። ችግረኛውን ፡ በሚረዳው ፡ ገንዘብ ፡ መልካም ፡ ለመሥራት ፡ በእጆቹ ፡ ይሥራ ፡ ይድከምም ፡ እንጂ ። ግዳጃችሁ ፡ በሚፈጸም ፡ ገንዘብ ፡ ከመልካም ፡ በቀር ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ከአፋችሁ ፡ አይውጣ ። መራራውን ፡ ሁሉ ፡ ቂምን ፡ ቁጣን ፡ ጩኸትን ፡ ስድብንም ፡ ከክፉ ፡ ሁሉ ፡ ጋር ፡ ከእናንተ ፡ አርቁ ። ባልንጀሮቻችሁንም ፡ ይቅር ፡ የምትሉ ፡ ሁኑ ። እግዚአብሔር ፡ ክርስቶስ ፡ ይቅር ፡ እንዳላችሁ ፡ ይቅር ፡ በሉ ። የተወደዳችሁ ፡ ልጆችም ፡ እንደመሆናችሁ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ምሰሉ ። ዝሙት ፡ ግን ፡ ርኩስ ፡ ሁሉ ፡ ዓመፃም ፡ በእናንተ ፡ አይሰማ ። የኀፍረት ፡ ነገርና ፡ የስንፍና ፡ ነገር ፡ የዘብዘብትም ፡ ነገር ፡ ፈሊዋታም ፡ ለቅዱሳን ፡ እንደማይገባቸው ። ይችን ፡ የማትገባ ፡ ሥራ ፡ አትቅረቡአት ። (ኤፌ ፡ ፬ ፡ ፳፮ - ፴፪ ። ፭ ፡ ፩ - ፬) ።

፩ሺ፯፻፳፯ ፊልጵስዩስ ። የደስታዬን ፡ አኳኋን ፡ ፈጽሙ። በ፩ ፡ ምክርና ፡ በ፩ ፡ ፍቅር ፡ በአንዲትም ፡ ነፍስ ፡ ትኖሩ ፡ ዘንድ ። በማናቸውም ፡ ጠብ ፡

እዙ ፡ ወተወድሶ ፡ በከንቱ ፡ እላ ፡ በትሑት ፡ ልብ ፡ ወስደረሲ ፡ ለለ፩ዱ ፡ እምኔክሙ ፡ ቢጸ ፡ ዚእሁ ፡ ዘይኄይስ ፡ እምኔሁ ።"

፩ሺ፮፻፳፰ መልእከተ ፡ ሐዋርያት ፡ ወዘሰ ፡ የእምር ፡ ገቢ ርታ ፡ ሰሠናይት ፡ ወኢይገብራ ፡ ኃጢአተ ፡ ትከውኖ ። ወእትሕቱ ፡ ርእሰክሙ ፡ ሰኵሉ ፡ ፍጥረተ ፡ እንስ ፡ እመሕያው ፡ በእንተ ፡ እግዚ እነ ።



ክርክርንና ፡ በከንቱ ፡ መወደስን ፡ አታድርጉ ። በትሑት ፡ ልብ ፡ እንጂ ። ከእናንተ ፡ እያንዳንዱ ባልንጀራውን ፡ ከእርሱ ፡ የሚሻል ፡ ያድርግ ። (ፊል ፡ ፪ ፡ ፩ - ፫) ።

፩ሺ፮፻፳፰ የሐዋርያት ፡ መልእክት ። መልካም ፡ መሥ ራትን ፡ የሚያውቅ ፡ የማይሠራትም ፡ ኃጢአት፡ ትሆንበታለች ። (ያዕ ፡ ፬ ፡ ፲፯) ። ስለ ፡ ጌታችን ፡ ብላችሁ ፡ ለሰው ፡ ፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ ራሳችሁን ፡ ዝቅ ፡ አድርጉ ፡ (፩ ፡ ጴጥ ፡ ፪ ፡ ፲፫) ።

## እንቀጽ ፡ ፵ወ፰ቱ ፡

በእንተ ፡ ዘኮነሂሆሙ ፡ ለክሐድያን ፡ እምላክ ፡ ልዑል ፡ ወፀረፍ ፡ ላዕሌሁ ። ወእምልኮተ ፡ ባዕድ ፡ ወዘይወስድ ፡ ኀቤሃ ፡ እምከዊነ ፡ ረቃዪ፡ ወመሠርይ ፡ ወስእለ ፡ ያስግሉ ፡ በፍሬ ፡ ዕፀው ፡ ወኀጠታት ፡ ወፋላት ።

፩ሺ፮፻፳፱ ምስራፍ ፡ ቀዳማዊ ። በእንተ ፡ በእተ ፡ ክሕ ደት ፡ እምኔሁ ። ይቤ ፡ እግዚእነ ፡ በወንጌል ፡ ጽሑፍ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እምላክከ ፡ ኪያሁ ፡ ታምልክ ፡ ወሎቱ ፡ ለባሕቲቱ ፡ ትስግድ ፡ "ወእዘዞሙ ፡ ለአርዳኢሁ ፡ እንዘ ፡ ይብል ፡ ሑሩ ፡ ወመሀሩ ፡ ኵሎ ፡ አሕዛበ ፡ ወእንዘ ፡ ታጠምቅዎሙ ፡ በስ ፡ በስመ ፡ አብ ፡ ወወልድ ፡ ወመንፈስ ፡ ቅዱስ ።" ወይቤ ፡ እስመ ፡ እግዚአ ብሔር ፡ መንፈስ ፡ ውእቱ ፡ ወይቤ ፡ አነ ፡ ወአብ ፩ዱ ፡ ንሕነ ፡ ወኵሉ ፡ ዘእቡየ ፡ ዚአየ ፡ ውእቱ ። ወዛቲ ፡ ቃል ፡ ታኤምር ፡ ከመ ፡ ይደሉ ፡ እሚነ ፡ ተዋሕዶቱ ፡ እምላካዊት ፡ ወትሥልስተ ፡ አካላ ቲሁ ፡ ወዕሪና ፡ አካላት ፡ በ፩ዱ ፡ ባሕርይ ፡ እም ላካዊ ፡ ወሥልጣነ ፡ ዚአሁ ፡ ወሰበየ ፡ ስብሐ ቲሁ ።

## እንቀጽ ፡ ፵፰ ።

ልዑል ፡ እምላክን ፡ ስለሚክዱ ፡ ሰዎችና ፡ እር ሱንም ፡ ስለመሳደብ ፡ ጣዖትን ፡ ስለማምለክ ፡ የሚረጩና ፡ መድኀኒት ፡ አድራጊ ፡ ከመሆን ፡ የተነሣ ፡ ወደእርስዋ ፡ ስለሚወስድ ፡ በስንፍት ፡ ፍሬና ፡ በቅንጣት ፡ በሚርትም ፡ ስለሚጠነቁሉ ፡ ሰዎች ፡ ቅጣት ፡ ይናገራል ።

፩ሺ፮፻፳፱ መጀመሪያ ፡ ምስሪፍ ። ከዚህ ፡ የተነሣ ፡ ከክ ሀደት ፡ ስለመውጣት ፡ ይናገራል ። ጌታችን ፡ በወንጌል ፡ እንዲህ ፡ አለ ። እርስን ፡ ፈጣሪህን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ታመልክ ፡ ዘንድ ፡ ለእርሱም ፡ ብቻ ፡ ትስግድ ፡ ዘንድ ፡ ተጽፏል ። (ማቴ ፡ ፬ ፡ ፲) ። ደቀመዛሙርቱንም ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ አዘ ዛቸው ። ሂዱና ፡ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡ አስተምሩ ። ስታጠምቁአቸውም ፡ በአብ ፡ በወልድ ፡ በመን ፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ስም ፡ በሉ ። (ማቴ ፡ ፳፰ ፡ ፲፱)። እግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ ነውናም ፡ አለ ። (ዮሐ ፡ ፬ ፡ ፳፬) ። እብና ፡ እኔ ፡ አንድ ፡ ነን ። የአባ ቴም ፡ ገንዘብ ፡ የእኔ ፡ ነው ፡ አለ ። (ዮሐ ፡ ፲ ፡ ፴) ። ይህችም ፡ ቃል ፡ አምላካዊት ፡ ተዋሕዶው ንና ፡ የአካላቱን ፡ ሦስትነት ፡ በአንድ ፡ አምላ ካዊ ፡ ባሕርይም ፡ የአካላቱን ፡ ዕሪና ፡ (እኩል ነት) ፡ የእርሱን ፡ ሥልጣን ፡ የጌትነቱንም ፡ ገና ናንት ፡ ማመን ፡ እንዲገባ ፡ ታመለክታለች ።

፩ሺ፮፻፴ ወይደሉ ፡ እምልኮ ፡ ወስጊድ ፡ ለአምላክ ፡ ባሕ ቲቱ ፡ እምቃለ ፡ ወንጌል ፡ ካዕበ ፡ ወእግዚአብ ሔር ፡ ውእቱ ፡ ቃል ፡ ወውእቱ ፡ ቃል ፡ ሥጋ ፡ ኮነ ፡ ወኀደረ ፡ ላዕሌነ ፡ ወርኢነ ፡ ስብሐቲሁ ፡ ከመ ፡ ስብሐተ ፡ ወልድ ፡ ዋሕድ ፡ ለአቡሁ ። ወዛቲ ፡ እማሬ ፡ በእንተ ፡ ተሠማዮቱ ፡ ለእም ላክ ፡ ወዝንቱ ፡ ውእቱ ፡ ክርስቶስ ፡ ለሥልጣኑ ፡ ይደሉ ፡ ስብሐት ፡ ወስሠናይቱ ፡ ይደሉ ፡ አኰ

፩ሺ፮፻፴ አምልኮና ፡ ስጊድ ፡ ለአምላክ ፡ ብቻ ፡ ይገባል። ዳግመኛም ፡ ከወንጌል ፡ ቃል ። ቃልም ፡ እግዚ አብሔር ፡ ነበረ ። ያም ፡ ቃል ፡ ሥጋ ፡ ሆነ ። በእ ኛም ፡ አደረ ። ጌትነቱንም ፡ ለአባቱ ፡ እንደ ፡ አንድ ልጅ ፡ ጌትነት ፡ አየን ። (ዮሐ ፡ ፩ ፡ ፩ ፡ ፲፬) ። ይህችም ፡ ስለአምላክ ፡ ሰው ፡ መሆን ፡ ምል ክት ፡ ናት ። ይኸውም ፡ ክርስቶስ ፡ ነው ። ለሥ ልጣኑ ፡ ክብር ፡ ይገባል ። ለቸርነቱም ፡ ምስ

አንቀጽ ፡ ፺፩ ።

እዘ ፡ ወተወድሶ ፡ በከንቱ ፡ እላ ፡ በትሑት ፡ ልብ ፡ ወለያሬሲ ፡ ለለፈዱ ፡ እምኔክሙ ፡ ቢጾ ፡ ዘእሁ ፡ ዘይኄይስ ፡ እምኔሁ ።

፩ሺ፯፻፹፰ መልእክተ ፡ ሐዋርያት ፡ ወዘሰ ፡ የእምር ፡ ገቢሮታ ፡ ለሠናይት ፡ ወኢይገብራ ፡ ኃጢአተ ፡ ትከውኖ ። ወአትሕቱ ፡ ርእሰክሙ ፡ ለኵሉ ፡ ፍጥረተ ፡ እጓለ ፡ እመሕያው ፡ በእንተ ፡ እግዚእነ ።

ስለ ፡ ክሐድያን ፡ ቅጣት ።

ክርክርንና ፡ በከንቱ ፡ መወደስን ፡ አታድርጉ ። በትሑት ፡ ልብ ፡ እንጂ ። ከእናንተ ፡ እያንዳንዱ ባልንጀራውን ፡ ከእርሱ ፡ የሚሻል ፡ ያድርግ ። (ፊል ፡ ፪ ፡ ፩ - ፫) ።

፩ሺ፯፻፹፰ የሐዋርያት ፡ መልእክት ። መልካም ፡ መሥራትን ፡ የሚያውቅ ፡ የማይሠራትም ፡ ኃጢአት፡ ትሆንበታለች ። (ያዕ ፡ ፬ ፡ ፲፯) ። ስለ ፡ ጌታችን ፡ ብላችሁ ፡ ለሰው ፡ ፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ ራሳችሁን ፡ ዝቅ ፡ አድርጉ ፡ (፩ ፡ ጴጥ ፡ ፪ ፡ ፲፫) ።

## አንቀጽ ፡ ፺ወ፪ቱ ፡

በእንተ ፡ ዘኮነኒሆሙ ፡ ለክሓድያን ፡ አምላክ ፡ ልዑል ፡ ወበረፍ ፡ ላዕሌሁ ። ወአምልኮተ ፡ ባዕድ ፡ ወዘይወስድ ፡ ኀቤሃ ፡ እምከዊን ፡ ረቃዒ ፡ ወመሠርይ ፡ ወለእለ ፡ ያሰግሉ ፡ በፍሬ ፡ ዕፀው ፡ ወኀጠታት ፡ ወፉላት ።

፩ሺ፯፻፹፱ ምዕራፍ ፡ ቀዳማዊ ። በእንተ ፡ ዘእተ ፡ ክሕደት ፡ እምኔሁ ። ይቤ ፡ እግዚእነ ፡ በወንጌል ፡ ጽሑፍ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አምላክከ ፡ ኪያሁ ፡ ታምልክ ፡ ወሎቱ ፡ ለባሕቲቱ ፡ ትሰግድ ፡ "ወአዘዘሙ ፡ ለአርዳኢሁ ፡ እንዘ ፡ ይብል ፡ ሑሩ ፡ ወመሀሩ ፡ ኵሎ ፡ አሕዛበ ፡ ወእንዘ ፡ ታጠምቅዎሙ ፡ በሉ ፡ በስመ ፡ አብ ፡ ወወልድ ፡ ወመንፈስ ፡ ቅዱስ ።" ወይቤ ፡ እስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ ውእቱ ፡ ወይቤ ፡ አነ ፡ ወአብ ፩ዱ ፡ ንሕነ ፡ ወኵሉ ፡ ዘአቡየ ፡ ዚአየ ፡ ውእቱ ። ወዛቲ ፡ ቃል ፡ ታኤምር ፡ ከመ ፡ ይደሉ ፡ እሚን ፡ ተዋሕዶቱ ፡ አምላካዊት ፡ ወትሥልስተ ፡ አካላቲሁ ፡ ወዕሪና ፡ አካላት ፡ በ፩ዱ ፡ ባሕርይ ፡ አምላካዊ ፡ ወሥልጣን ፡ ዚአሁ ፡ ወዕበየ ፡ ስብሐቲሁ ።

## አንቀጽ ፡ ፺፪ ።

ልዑል ፡ አምላክን ፡ ስለሚክዱ ፡ ሰዎችና ፡ እርሱንም ፡ ስለመሳደብ ፡ ጣዖትን ፡ ስለማምለክ ፡ የሚረዳንና ፡ መደገኛት ፡ አድራጊ ፡ ከመሆን ፡ የተነሣ ፡ ወደእርስዋ ፡ ስለሚወስድ ፡ በዕንጨት ፡ ፍሬና ፡ በቅንጣት ፡ በሚርትም ፡ ስለሚጠንቁሉ፡ ሰዎች ፡ ቅጣት ፡ ይናገራል ።

፩ሺ፯፻፹፱ መጀመሪያ ፡ ምዕራፍ ። ከዚህ ፡ የተነሣ ፡ ከክህደት ፡ ስለመውጣት ፡ ይናገራል ። ጌታችን ፡ በወንጌል ፡ እንዲህ ፡ አለ ። እርሱን ፡ ፈጣሪህን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ታመልክ ፡ ዘንድ ፡ ለእርሱም ፡ ብቻ ፡ ትሰግድ ፡ ዘንድ ፡ ተጽፏል ። (ማቴ ፡ ፬ ፡ ፲) ። ደቀመዛሙርቱንም ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ አዘዛቸው ። ሂዱና ፡ አሕዛብን ፡ ሁሉ ፡ አስተምሩ ። ስታጠምቁአቸውም ፡ በአብ ፡ በወልድ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ ስም ፡ በሉ ። (ማቴ ፡ ፳፰ ፡ ፲፱)። እግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ ነውና ፡ አለ ። (ዮሐ ፡ ፬ ፡ ፳፬) ። አብና ፡ እኔ ፡ አንድ ፡ ነን ። የአባቴም ፡ ገንዘብ ፡ የእኔ ፡ ነው ፡ አለ ። (ዮሐ ፡ ፲ ፡ ፴) ። ይህችም ፡ ቃል ፡ አምላካዊት ፡ ተዋሕዶውንና ፡ የአካላቱን ፡ ሦስትነት ፡ በአንድ ፡ አምላካዊ ፡ ባሕርይም ፡ የአካላቱን ፡ ዕሪና ፡ (እኩልነት) ፡ የእርሱን ፡ ሥልጣን ፡ የጌትነቱንም ፡ ገናናነት ፡ ማመን ፡ እንዲገባ ፡ ታመለክታለች ።

፩ሺ፯፻፺ ወይደሉ ፡ አምልኮ ፡ ወሰጊድ ፡ ለአምላክ ፡ ባሕቲቱ ፡ እምቃለ ፡ ወንጌል ፡ ካዕበ ፡ ወእግዚአብሔር ፡ ውእቱ ፡ ቃል ፡ ወውእቱ ፡ ቃል ፡ ሥጋ ፡ ኮነ ፡ ወኀደረ ፡ ላዕሌነ ፡ ወርኢነ ፡ ስብሐቲሁ ፡ ከመ ፡ ስብሐተ ፡ ወልድ ፡ ዋሕድ ፡ ለአቡሁ ። ወዛቲ ፡ እማሬ ፡ በእንተ ፡ ተሠማምዐ ፡ ለአምላክ ፡ ወዝንቱ ፡ ውእቱ ፡ ክርስቶስ ፡ ለሥልጣኑ ፡ ይደሉ ፡ ስብሐት ፡ ወሰጊድ ፡ ይደሉ ፡ አኰ

፩ሺ፯፻፺ አምልኮና ፡ ስጊድ ፡ ለአምላክ ፡ ብቻ ፡ ይገባል። ዳግመኛም ፡ ከወንጌል ፡ ቃል ። ቃልም ፡ እግዚአብሔር ፡ ነበረ ። ያም ፡ ቃል ፡ ሥጋ ፡ ሆነ ። በእኛም ፡ አደረ ። ጌትነቱንም ፡ ለአባቱ ፡ አንድ ፡ አንድ ልጅ ፡ ጌትነት ፡ አየን ። (ዮሐ ፡ ፩ ፡ ፩ ፡ ፲፬) ። ይህችም ፡ ስለአምላክ ፡ ሰው ፡ መሆን ፡ ምልክት ፡ ናት ። ይኸውም ፡ ክርስቶስ ፡ ነው ። ለሥልጣኑ ፡ ክብር ፡ ይገባል ። ለቸርነቱም ፡ ምስ

ቱት ። ወይቤ ፡ ልዑል ፡ ሎቱ ፡ ስብሐት ፡ በውስተ ፡ አሪት ፡ እነ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክከ ፡ ኢታምልክ ፡ ባዕደ ፡ አምላከ ፡ ዘእንበሌየ ፡ ወተፍጻሜቱ ፡ ዝንቱ ፡ ቃል ።

፩ሺ፯፻፴፩ ምዕራፍ ፡ ዳግም ። በእንተ ፡ ሁኔኢየሙ ፡ ለለ ፩ዱ ፡ ዘዘዚአሁ ፡ ክሕደቶሙ ፡ ወውእቱ ፡ ፪ቱ ፡ ክፍል ። ቀዳሚሁ ፡ ሥርዓተ ፡ ሁኔኢ ፡ ሥጋዊ ። ትሕ ፡ ወለእመ ፡ ተንሥአ ፡ እምኔክሙ ፡ ነቢይ ፡ አው ፡ ሐላሚ ፡ ሕልም ፡ ወወሀበክሙ ፡ ትእምርተ ፡ ቃለ ፡ ጥያቄ ፡ ወለእመ ፡ ይቤለከ ፡ ንዓ ፡ ንሑር ፡ ወናምልክ ፡ አማልክተ ፡ ካልአነ ፡ ዘኢተአምርዎሙ ፡ ኢትስምዖ ፡ ለው ፡ ለውእቱ ፡ ነቢይ ፡ እው ፡ ለውእቱ ፡ ሐላሚ ፡ ሕልም ፡ እስመ ፡ ያሜክረክሙ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክክሙ ፡ ከመ ፡ ይርአይ ፡ ለእመ ፡ ታፈቅርዎ ፡ በኵሉ ፡ ልብክሙ ፡ ወነፍስክሙ ፡ አው ፡ አልቦ። ወለውእቱስ ፡ ነቢይ ፡ ወሐላሚ ፡ ሕልም ፡ ቅትልዎ ፡ እስመ ፡ ነበበ ፡ ሐሰተ ፡ ላዕለ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላክክሙ ።

፩ሺ፯፻፴፪ ወለእመኒ እኁከ ፡ እስሐተከ ፡ አው ፡ ወልድከ ፡ አው ፡ ብእሲትከ፡ አው ፡ ዓርክከ ፡ ወይቤለከ ፡ በኅቡእ ፡ ንዓ ፡ ናምልክ ፡ አማልክተ ፡ ካልአነ ፡ ዘኢተአምር ፡ አንተ ፡ ወኢ ፡ አበዊከ ፡ እምአማልክተ ፡ አሕዛብ ፡ ኢትፍቅድ ፡ ዘንተ ፡ ወኢትትመከሮ ፡ እምኔሁ ወኢትኅዝን ፡ ሎቱ ፡ ወኢትሠውሮ ፡ አላ ፡ ቅትሎ ፡ በውግረተ ፡ እብን ፡ ወእደዊከ ፡ ይቅድማ ፡ ወጊሮቶ ፡ ወእደዊሆሙ ፡ ለኵሎሙ ፡ ሕዝብ ፡ ድኅረ ።

፩ሺ፯፻፴፫ ወለእመ ፡ ሰማዕከ ፡ በአሐዱ ፡ እምአህጉሪከ ፡ ከመ ፡ ወፅኡ ፡ እምኔሃ ፡ ሰብእ ፡ ከሓድያን ፡ ወአስሐትዎሙ ፡ ለሰብአ ፡ ሀገሮሙ ፡ እንዘ ፡ ይብሉኑ ፡ ናምልክ ፡ አማልክተ ፡ ባዕዳነ ፡ ዘኢተአምርዎሙ ፡ አንትሙ ፡ ኅሥሥ ፡ ጥያቄ ፡ ዝንቱ ፡ ወተስአል ፡ በእንቲአሁ ፡ እንዘ ፡ ተሐትት ። ወለእመ ፡ ኮነ ፡ እሙነ ፡ ወጥዩቀ ፡ ቅትሎሙ ፡ ለሰብአ ፡ ይእቲ ፡ ሀገር ፡ በብልሐ ፡ ሰይፍ ፡ ወአጥፍኦ ፡ ኪያሃ ፡ ወለኵሎሙ ፡ እለ ፡ ሀለዉ ፡ ውስቴታ ፡ ወአውዕያ ፡ በእሳት ።

፩ሺ፯፻፴፬ ትሕ ፡ ወዘሂ ፡ ይሠውዕ ፡ ለአማልክት ፡ ዘእንበለ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ለይሙት ።

፩ሺ፯፻፴፭ ትሕ ፡ ወዘይሁብ ፡ እምዘርኡ ፡ ለሞሎክ ፡ ይት



ጋና ፡ ይባባል ። ልዑልም ፡ ምስጋና ፡ ይግባውና፡ በኦሪት ፡ እንዲህ ፡ አለ ። እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ፈጣሪህ ፡ ነኝ ። ከእኔ ፡ ሌላ ፡ ባዕድ ፡ አምላክ ፡ አታምልክ ። የዚህንም ፡ ቃል ፡ መጨረሻ ፡ ተናገረ ። (ዘፀ ፡ ፳ ፡ ፫) ።

፩ሺ፯፻፴፩ ፪ኛ ፡ ምዕራፍ ፡ ከሀደታቸው ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ስለሆነ ፡ ስለእያንዳንዱ ፡ ቅጣት ፡ ይናገራል ። ይኸውም ፡ ሁለት ፡ ክፍል ፡ ነው ። መጀመሪያው ፡ የሥጋዊን ፡ ቅጣት ፡ ሥርዓት ፡ ይናገራል ። ትሕ ፡ ከእናንተ ፡ ወገን ፡ ነቢይ ፡ ወይም ፡ ሕልም ፡ የሚያልም ፡ ቢነሣ ፡ አስረጅ ፡ የሚሆን ፡ የቃል ፡ ምልክትም ፡ ቢሰጣችሁ ፡ የማታውቋቸውን ፡ ሌሎችን ፡ አማልክት ፡ ና ፡ ሂደን እናምልክ ፡ ቢልህም ፡ ያንን ፡ ነቢይ ፡ ወይም ፡ ያንን ፡ ሕልም ፡ አላሚ ፡ አትስሙት ። ፈጣሪያችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ በፍጹም ፡ ልቦናችሁና ፡ ሰውነታችሁ ፡ ትወዱት ፡ እንደሆነ ፡ ያይ ፡ ዘንድ ፡ ይፈትናችኋልና ። ያንን ፡ ነቢይ ፡ ማን ፡ ሕልም፡አላሚውንም፡ግደሉት። በፈጣሪያችሁ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ ሐሰት ፡ ተናግሯልና ።

፩ሺ፯፻፴፪ ወንድምህ ፡ ወይም ፡ ልጅህ ፡ ወይም ፡ ሚስትህ ፡ ወይም ፡ ወዳጅህ ፡ ቢያስትህ ፡ ከአሕዛብ ፡ አማልክት ፡ ወገን ፡ አንተ ፡ ወይም ፡ አባቶችህ ፡ የማታውቋቸውን ፡ አማልክት ፡ በስውር ፡ ና ፡ እናምልክ ፡ ቢልህ ፡ ይህን ፡ አትሻ ። ከእርሱም ፡ አትቀበል ። አትዘንለትም ። አትሰውረውም ። በደንጋይ ፡ ወግረህ ፡ግደለው ፡ እንጂ ። የአንተ፡ እጆች ፡ አስቀድመው ፡ ይውገሩት ። ኋላም ፡ የሕዝቡ ፡ ሁሉ ፡ እጅ ።

፩ሺ፯፻፴፫ ከሀገሮችህ ፡ በአንዲቱ ፡ ከሐድያን ፡ ሰዎች ፡ ከእርስዋ ፡ ወጥተው ፡ የሀገራቸውን ፡ ሰዎች ፡ እናንተ ፡ የማታውቋቸውን ፡ ሌሎችን ፡ አማልክት ፡ ኑ ፡ እናምልክ ፡ ብለው ፡ እንዳሳቷቸው ፡ ብትሰማ ፡ የዚህን ፡ ርግጥ ፡ መርምር ። ስለእርሱ እየመረመርህ ፡ ጠይቅ ። የታመነና ፡ የተረጋገጠ ቢሆንም ፡ የዚያችን ፡ ሀገር ፡ ሰዎች ፡ በሰይፍ ፡ ስለት ፡ ግደላቸው ። ሀገሪቱንም ፡ አጥፋ ። በውስጧ ፡ ያሉትንም ፡ ሁሉ ። በእሳትም ፡ አቃጥላት ። (ዘዳ ፡ ፲፫ ፡ ፩ - ፲፯) ።

፩ሺ፯፻፴፬ ትሕ ። ለእግዚአብሔር ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ ለጣዖታት ፡ መሥዋዕት ፡ የሚሠዋ ፡ ይሙት ። (ዘፀ ፡ ፳፪ ፡ ፳) ።

፩ሺ፯፻፴፭ ትሕ ። ከልጆቹ ፡ ለሞሎክ ፡ የሚሰጥ ፡ በደን

